THE

# NEW TESTAMENT

OF OUR

LORD AND SAVIOUR

# JESUS CHRIST,

IN AMHARIC.



PRINTED AT THE EXPENSE AND BY THE REQUEST
OF THE BRITISH AND FOREIGN BIBLE SOCIETY IN LONDON.
AT THE MISSION PRESS OF ST. CHRISCHONA NEAR BASLE. SWITZERLAND.
1886.

# አዲስ፡ኪዳን፡

እርሱም፡

የጌታችንና ፡ የመድኃኒታችን፡

# የ የ ሱ ስ ፡ ክ ር ስ ቶ ስ፡

ወንጌል ፡ ቅዱስ፡

የሐዋርያቱም ፡ መጻሕፍት።

ባማርኛ ፡ ቋንቋ።



በእንግሊዝ ፡ በሎንደን ፡ ከተማ ፡ ያለች ፡ የክርስቲያን ፡ ጉባኤ ፡ በክርሾና ፡ በሕልዌትያ፡
መንግሥት ፡ ባለች ፡ ማኅተምያ ፡ አሳተመችው።
በ፲፰፻፸፯፤ አመት፡
ከጌታችን፡ ከየሱስ፡ ክርስተስ፡ ከልደቱ፡ በኋላ።

ያዲስ ፡ ኪዳን ፡ መጻሕፍት።

---



---

ብሉይን፡ ከሐዲስ፡ ጋራ፡ ለመጋጠም፡ ሐዲስንም፡ እርሱ፡ በርሱ፡ ለመመርመር፡ በምዕራፉ፡ ሁሉ፡ ክፍል፡ ያለውን፡ ምልክት፡ አስተውል። መጽሐፍ፡ ቅዱስን፡ ለመማርና፡ ለማስተዋል፡ ተጻፈ። እግዚአ ብሔር፡ብርሃኑን፡ይግለጽልሀ፡ የሕይወትን፡ መንገድ፡ ይምራሁ።

ስፍራ፡ ስለ፡ ጠበበ፡ የመጽሐፍ፡ ቅዱስን፡ መጻሕፍት፡ እንደህ፡ ብሎ፡ ተጻፈ።

ዘፍጥ፡ . . . ማለት፡ ኦሪት፡ ዘፍጥረት።
ዘፀአ፡ . . . ማለት፡ ኦሪት፡ ዘፀአት።
ዘሌዋ፡ . . . ማለት፡ ኦሪት፡ ዘሌዋውያን።
ዘኍል፡ . . . ማለት፡ ኦሪት፡ ዘኍልቍ።
ዘዳግ፡ . . . ማለት፡ ኦሪት፡ ዘዳግም።
ኢያ፡ . . . ማለት፡ መጽሐፈ፡ ኢያሱ፡ ወልደ፡ ነዌ።
መሳ፡ . . . ማለት፡ መጽሐፈ፡ መሳፍንት።
ሩት፡ . . . ማለት፡ መጽሐፈ፡ ሩት።
፩፡ ሳሙኤ፡ . . . ማለት፡ መጽሐፈ፡ ሳሙኤል፡ ቀደማዊ።
፪፡ ሳሙኤ፡ . . . ማለት፡ መጽሐፈ፡ ሳሙኤል፡ ካልእ።
፩፡ ነገሥ፡ . . . ማለት፡ መጽሐፈ፡ ነገሥት፡ ቀደማዊ።
፪፡ ነገሥ፡ . . . ማለት፡ መጽሐፈ፡ ነገሥት፡ ካልእ።
፩፡ ዜና፡ . . . ማለት፡ መጽሐፈ፡ ዜና፡ መዋዕል፡ ቀደማዊ።
፪፡ ዜና፡ . . . ማለት፡ መጽሐፈ፡ ዜና፡ መዋዕል፡ ካልእ።
ዕዝ፡ . . . ማለት፡ መጽሐፈ፡ ዕዝራ።
ነህ፡ . . . ማለት፡ መጽሐፈ፡ ነህምያ።
አስቴ፡ . . . ማለት፡ መጽሐፈ፡ አስቴር።
ኢዮብ፡ . . . ማለት፡ መጽሐፈ፡ ኢዮብ።
መዝ፡ . . . ማለት፡ መጽሐፈ፡ መዝሙራት፡ ዘዳዊት።
ምሳ፡ . . . ማለት፡ መጽሐፈ፡ ምሳሌ።
መክ፡ . . . ማለት፡ መጽሐፈ፡ መክብብ።
መኃ፡ . . . ማለት፡ መጽሐፈ፡ መኃልየ፡ መኃልይ።
ኢሳ፡ . . . ማለት፡ ትንቢተ፡ ኢሳይያስ።
ኤር፡ . . . ማለት፡ ትንቢተ፡ ኤርምያስ።
ሕዝ፡ . . . ማለት፡ ትንቢተ፡ ሕዝቅኤል።
ዳን፡ . . . ማለት፡ ትንቢተ፡ ዳንኤል።
ሆሴ፡ . . . ማለት፡ ትንቢተ፡ ሆሴዕ።
ኢዮ፡ . . . ማለት፡ ትንቢተ፡ ኢዮኤል።
ዓሞ፡ . . . ማለት፡ ትንቢተ፡ ዓሞጽ።
ኦብድ፡ . . . ማለት፡ ትንቢተ፡ ኦብድዩ።
ዮና፡ . . . ማለት፡ ትንቢተ፡ ዮናስ።
ሚክ፡ . . . ማለት፡ ትንቢተ፡ ሚክያስ።
ናሆ፡ . . . ማለት፡ ትንቢተ፡ ናሆም።
እንባ፡ . . . ማለት፡ ትንቢተ፡ እንባቆም።
ሶፎን፡ . . . ማለት፡ ትንቢተ፡ ሶፎንያስ።
ሐጌ፡ . . . ማለት፡ ትንቢተ፡ ሐጌ።
ዘካ፡ . . . ማለት፡ ትንቢተ፡ ዘካርያስ።
መልክ፡ . . . ማለት፡ ትንቢተ፡ መልክያስ።

ማቴ፡ . . ማለት፡ የማቴዎስ፡ ወንጌል።

ማር፡ . . ማለት፡ የማርቆስ፡ ወንጌል።

ሉቃ፡ . . . ማለት፡ የሉቃስ፡ ወንጌል።

ዮሐ፡ . . ማለት፡ የዮሐንስ፡ ወንጌል።

የሐዋ፡ . . ማለት፡ የሐዋርያት፡ ስራ።

ሮሜ፡ . . ማለት፡ የጳውሎስ፡ መልእክት፡ ወደ፡ ሮሜ፡ ሰዎች።

፩፡ ቆሮን፡ . ማለት፡ የጳውሎስ፡ መልእክት፡ መጀመርያዪቱ፡ ወደ፡ ቆሮንቶስ፡ ሰዎች።

፪፡ ቆሮን፡ . ማለት፡ የጳውሎስ፡ መልእክት፡ ሁለተኛዪቱ፡ ወደ፡ ቆሮንቶስ፡ ሰዎች።

ገላት፡ . . ማለት፡ የጳውሎስ፡ መልእክት፡ ወደ፡ ገላትያ፡ ሰዎች።

ኤፌ፡ . . ማለት፡ የጳውሎስ፡ መልእክት፡ ወደ፡ ኤፌሶን፡ ሰዎች።

ፊል፡ . . . ማለት፡ የጳውሎስ፡ መልእክት፡ ወደ፡ ፊልጵስዩስ፡ ሰዎች።

ቆለ፡ . . . ማለት፡ የጳውሎስ፡ መልእክት፡ ወደ፡ ቆለሳይስ፡ ሰዎች።

፩፡ ተሰ፡ . . ማለት፡ የጳውሎስ፡ መልእክት፡ መጀመርያዪቱ፡ ወደ፡ ተሰሎንቄ፡ ሰዎች።

፪፡ ተሰ፡ . . ማለት፡ የጳውሎስ፡ መልእክት፡ ሁለተኛዪቱ፡ ወደ፡ ተሰሎንቄ፡ ሰዎች።

፩፡ ጢሞ፡ . ማለት፡ የጳውሎስ፡ መልእክት፡ መጀመርያዪቱ፡ ወደ፡ ጢሞቴዎስ።

፪፡ ጢሞ፡ . ማለት፡ የጳውሎስ፡ መልእክት፡ ሁለተኛዪቱ፡ ወደ፡ ጢሞቴዎስ።

ቲጦ፡ . . . ማለት፡ የጳውሎስ፡ መልእክት፡ ወደ፡ ቲጦስ።

ፊልሞ፡ . . ማለት፡ የጳውሎስ፡ መልእክት፡ ወደ፡ ፊልሞን።

ዕብ፡ . . . ማለት፡ የጳውሎስ፡ መልእክት፡ ወደ፡ ዕብራውያን።

ያዕ፡ . . . ማለት፡ የያዕቆብ፡ መልእክት፡ ከተሊካዊት።

፩፡ ጴጥ፡ . ማለት፡ የጴጥሮስ፡ መልእክት፡ ክተሊካዊት፡ መጀመርያዪቱ።

፪፡ ጴጥ፡ . ማለት፡ የጴጥሮስ፡ መልእክት፡ ከተሊካዊት፡ ሁለተኛዪቱ።

፩፡ ዮሐ፡ . ማለት፡ የዮሐንስ፡ መልእክት፡ ከተሊካዊት፡ መጀመርያዪቱ።

፪፡ ዮሐ፡ . ማለት፡ የዮሐንስ፡ መልእክት፡ ሁለተኛዪቱ።

፫፡ ዮሐ፡ . ማለት፡ የዮሐንስ፡ መልእክት፡ ሶስተኛዪቱ።

ይሁዳ፡ . . ማለት፡ የይሁዳ፡ መልእክት፡ ከተሊካዊት።

ራእ፡ . . . ማለት፡ የዮሐንስ፡ ራእይ።

ም፡ . . . ማለት፡ ምዕራፍ።

ቍ፡ . . . ማለት፡ ቍጥር።

—፡ . . . ማለት፡ እስከ።

ማርቲን፡ ፍላድ፡ የወንጌል፡ መልክተኛ።

---

# የማቴዎስ ፡ ወንጌል።

| | | |
|---|---|---|
| ፵፡ | በእንተ፡ እለ፡ ተስአሉ፡ እመ፡ ይከውን፡ ኅድገ፡ ብእሲት። | ምዕራፍ፡ ፲፱፡ ፩፡ |
| ፵፩፡ | በእንተ፡ ባዕል፡ ዘተስእሎ፡ ለእግዚእ። | » ፲፱፡ ፲፮፡ |
| ፵፪፡ | በእንተ፡ ዘተዓሰበ፡ ገባእተ። | » ፳፡ ፩፡ |
| ፵፫፡ | በእንተ፡ ደቂቀ፡ ዘብደዎስ። | » ፳፡ ፳፡ |
| ፵፬፡ | በእንተ፡ ክልኤ፡ ዕውራን። | » ፳፡ ፳፱፡ |
| ፵፭፡ | በእንተ፡ ዕዋል። | » ፳፩፡ ፩፡ |
| ፵፮፡ | በእንተ፡ ዕውራን፡ ወስቡራን። | » ፳፩፡ ፲፬፡ |
| ፵፯፡ | በእንተ፡ በለስ፡ እንተ፡ የብሰት። | » ፳፩፡ ፲፰፡ |
| ፵፰፡ | በእንተ፡ እለ፡ ተስአልዎ፡ ካህናት፡ ወረበናት፡ ለኢየሱስ፡ በመገሕተ፡ መኑ፡ ትገብር፡ ዘንተ። | » ፳፩፡ ፳፫፡ |
| ፵፱፡ | በእንተ፡ ክልኤ፡ አኀው፡ ምሳሌ። | » ፳፩፡ ፳፰፡ |
| ፶፡ | በእንተ፡ ዐጸደ፡ ወይን፡ ምሳሌ። | » ፳፩፡ ፴፫፡ |
| ፶፩፡ | በእንተ፡ እለ፡ ተጸውዑ፡ ውስተ፡ ከብካብ። | » ፳፪፡ ፩፡ |
| ፶፪፡ | በእንተ፡ እለ፡ ተሰአልዎ፡ በእንተ፡ ዲናር። | » ፳፪፡ ፲፭፡ |
| ፶፫፡ | በእንተ፡ ሰዱቃውያን፡ እለ፡ ይብሉ፡ አልቦ፡ ትንሣኤ፡ ምውታን። | » ፳፪፡ ፳፫፡ |
| ፶፬፡ | በእንተ፡ ጸሐፊ፡ ዘተስአሎ፡ አይ፡ ትእዛዝ፡ የዐቢ። | » ፳፪፡ ፴፬፡ |
| ፶፭፡ | በእንተ፡ ፈሪሳውያን፡ ዘከመ፡ ተስአሎሙ፡ ክርስቶስ፡ ወልደ፡ መኑ፡ ውእቱ፡ ክርስቶስ። | » ፳፪፡ ፵፩፡ |
| ፶፮፡ | በእንተ፡ አሌ፡ ሎሙ፡ ለጸሐፍት፡ ወፈሪሳውያን። | » ፳፫፡ ፲፫፡ |
| ፶፯፡ | በእንተ፡ ኅልቀተ፡ ዓለም። | » ፳፬፡ ፩፡ |
| ፶፰፡ | በእንተ፡ ሰዓት፡ ወዕለት። | » ፳፬፡ ፴፮፡ |
| ፶፱፡ | በእንተ፡ ዐሠሩ፡ ደናግል | » ፳፭፡ ፩፡ |
| ፷፡ | በእንተ፡ እለ፡ ነሥኡ፡ መካልየ፡ ብሩር። | » ፳፭፡ ፲፬፡ |
| ፷፩፡ | በእንተ፡ ምጽአቱ፡ ለክርስቶስ። | » ፳፭፡ ፴፩፡ |
| ፷፪፡ | በእንተ፡ እንተ፡ ቀብአቶ፡ ለእግዚእ፡ ዕፍረተ። | » ፳፮፡ ፮፡ |
| ፷፫፡ | በእንተ፡ ዘከመ፡ ተስአልዎ፡ በኀበ፡ ያስተደልዉ፡ ሎቱ፡ ፋሥሐ። | » ፳፮፡ ፲፯፡ |
| ፷፬፡ | በእንተ፡ ሥርዐተ፡ ምሥጢር። | » ፳፮፡ ፳፮፡ |
| ፷፭፡ | በእንተ፡ ግብአቱ፡ ለክርስቶስ። | » ፳፮፡ ፵፯፡ |
| ፷፮፡ | በእንተ፡ ዘከመ፡ ክሕደ፡ ጴጥሮስ። | » ፳፮፡ ፷፱፡ |
| ፷፯፡ | በእንተ፡ ዘከመ፡ ነስሐ፡ ይሁዳ። | » ፳፯፡ ፫፡ |
| ፷፰፡ | በእንተ፡ ዘከመ፡ ሰአለ፡ ሥጋሁ፡ ለእግዚእ፡ ዮሴፍ። | » ፳፯፡ ፶፯፡ |

---

# የጌታችን ፡ የየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ቅዱስ ፡ ወንጌል ፡ እንደ ፡ ጻፈው ፡ ቅዱስ ፡ ማቴዎስ።

ምዕራፍ፡ ፩፡

፩፡ የየሱስ፡ክርስቶስ፡የልደቱ፡መጽሐፍ፡ የደዊት፡
ልጅ፡ የአብርሃም፡ ልጅ። ሉቃ፡ ፫፡ ፳፫፡—፴፰፡፡
፪፡ አብርሃም፡ ይስሐቅን፡ ወለደ። ይስሐቅም፡ ያ
ዕቅብን፡ ወለደ። ያዕቀብም፡ ይሁዳን፡ ወለደ፡ ወንድ
ሞቹንም። ዘፍ፡ ፳፩፡ ፫፡ ፲፪፡፡ ፳፭፡ ፳፮፡፡
ም፡ ፳፱፡ ፴፭፡፡ ም፡ ፵፱፡ ፲፡፡
፫፡ ይሁዳም፡ ፋሬስን፡ ዛራንም፡ ወለደ፡ ከትእማ
ር። ፋሬስም፡ኤስሮምን፡ወለደ፡ኤስሮምም፡አራም
ን፡ ወለደ። ዘፍ፡ ፴፰፡ ፳፱፡፴፡፡ ፩፡ ዜና፡ ፪፡ ፭፡ ፱፡፡
፬፡ አራምም፡አሚናዳብን፡ወለደ፡አሚናዳብም፡
ነአሶንን፡ ወለደ፡ ነአሶንም፡ ሰልሞንን፡ ወለደ።
፩፡ ዜና፡ ፪፡ ፲፡፡
፭፡ ሰልሞንም፡ ቦዔዝን፡ ወለደ፡ከራኬብ። ቦዔዝ
ም፡ ኦቤድን፡ ወለደ፡ ከሩት። ኦቤድም፡ እሤይን፡
ወለደ። ሩት፡ ፬፡ ፲፫፡—፳፪፡፡

፮፡ እሴይም፡ ዳዊትን፡ ንጉሥን፡ ወለደ። ዳዊት፡ ንጉሥም፡ ሰሎሞንን፡ ወለደ፡ ከኦሪያ፡ ምሽት።
፪፡ ሳሙ፡ ፲፪፡ ፳፬።

፯፡ ሰሎሞንም፡ ሮብዓምን፡ ወለደ፡ ሮብዓምም፡ አቢያን፡ ወለደ፡ አቢያም፡ አሣን፡ ወለደ።
፩፡ ዜና፡ ፫፡ ፲።

፰፡ አሣም፡ ኢዮሣፍጥን፡ ወለደ። ኢዮሣፍጥም፡ ኢዮራምን፡ ወለደ፡ ኢዮራምም፡ ዖዝያንን፡ ወለደ።
፩፡ ነገሥ፡ ፲፭፡ ፳፬። ፳፪፡ ፶፩። ፩፡ ዜና፡ ፫፡ ፲፩።

፱፡ ዖዝያንም፡ ኢዮአታምን፡ ወለደ። ኢዮአታምም፡ አካዝን፡ ወለደ። አካዝም፡ ሕዝቅያስን፡ ወለደ።

፲፡ ሕዝቅያስም፡ ምናሴን፡ ወለደ። ምናሴም፡ አሞንን፡ ወለደ። አሞንም፡ ኢዮስያስን፡ ወለደ።

፲፩፡ ኢዮስያስም፡ ኢኮንያንን፡ ወለደ፡ ወንድሞቹንም፡ በባቢሎን፡ ምርኮ፡ ጊዜ።

፲፪፡ ከባቢሎንም፡ ምርኮ፡በኋላ፡ ኢኮንያን፡ ሰላትያልን፡ ወለደ፡ ሰላትያልም፡ ዘሩባቤልን፡ ወለደ።
ዕዝ፡ ፫፡ ፪።

፲፫፡ ዘሩባቤልም፡ አቢዩድን፡ ወለደ፡ አቢዩድም፡ ኤልያቄምን፡ ወለደ፡ ኤልያቄምም፡አዞርን፡ወለደ።

፲፬፡ አዞርም፡ ሳዶቅን፡ ወለደ፡ሳዶቅም፡አኪምን፡ ወለደ፡ አኪምም፡ ኤልዩድን፡ ወለደ።

፲፭፡ ኤልዩድም፡ አልዓዛርን፡ ወለደ፡አልዓዛርም፡ ማታንን፡ ወለደ፡ ማታንም፡ ያዕቆብን፡ ወለደ።

፲፮፡ ያዕቆብም፡ ዮሴፍን፡ወለደ፡የማርያምን፡ ባሏን። ከርሷ፡የሱስ፡የተወለደ* ክርስቶስ፡የተባለው።
* ም፡ ፳፯፡ ፲፯፡ ፳፪።

፲፯፡ ትውልድም፡ ሁሉ፡ ከአብርሃም፡ እስከ፡ ዳዊት፡ አሥራ፡ አራት፡ ትውልድ። ከዳዊትም፡ እስከ፡ ባቢሎን፡ ምርኮ፡አሥራ፡ አራት፡ ትውልድ። ከባቢሎንም፡ ምርኮ፡ እስከ፡ ክርስቶስ፡ አሥራ፡ አራት፡ ትውልድ።

፲፰፡ የየሱስ፡ ክርስቶስም፡ ልደቱ፡ እንደዚህ፡ ነበረ። እናቱ፡ማርያም፡ ለዮሴፍ፡ በታጨች፡ ጊዜ፡ ሳይገናኙ፡ ከመንፈስ፡ ቅዱስ፡ ፀንሳ፡ ተገኘች። ሉቃ፡ ፩፡ ፴፭።

፲፱፡ ባሏዋም፡ ዮሴፍ፡ ጻድቅ፡ ነበረ፡ በሕዝብም፡ ፊት፡ ሊገልጻት፡ አልወደደም፡ አሰበም፡በውር፡ ሊተዋት።

፳፡ እርሱ፡ ግን፡ ይህነን፡ ሲያስብ፡ እነሆ፡ የእግዚአብሔር፡ መልክተኛ፡ በሕልም፡ታየው፡ እንደዚህ፡ሲል። ዮሴፍ፡ ሆይ፡ የዳዊት፡ ልጅ፡ ሚስትህን፡ ማርያምን፡ ለመውሰድ፡ አትፍራ። በርሷ፡ የሚወለደው፡ ከመንፈስ፡ ቅዱስ፡ ነውና። ቍ፡ ፲፰።

፳፩፡ ልጅም፡ ትወልዳለች፡* ስሙንም፡ የሱስ፡ ትለዋለህ፡† ሕዝቡን፡ከኃጢአታቸው፡ ያድናቸዋልና።
*ሉቃ፡ ፩፡ ፴፩። ፪፡ ፳፩። †የሐዋ፡ ፬፡ ፲፪።

፳፪፡ ይህም፡ ሁሉ፡ ሆነ፡ ከእግዚአብሔር፡ ዘንድ፡* በነቢይ፡የተባለው፡ሊፈጸም፡የሚል። *ኢሳ፡ ፯፡ ፲፬።

፳፫፡ እነሆ፡ ድንግል፡ ትፀንሳለች፡ ልጅም፡ ትወልዳለች፡ ስሙንም፡ አማኑኤል፡ ይሉታል፡ ትርጓሜው፡ እግዚአብሔር፡ ከኛ፡ ጋራ፡ የሆነ። ሉቃ፡ ፩፡ ፴፩።

፳፬፡ ዮሴፍም፡ ከንቅልፉ፡ ተነሥቶ፡ የእግዚአብሔር፡ መልክተኛ፡ እንዳዘዘው፡ አደረገ፡ሚስቱንም፡ ማርያምን፡ ወሰዳት።

፳፭፡አላወቃትምም፡*የበኵር፡ልጅዋን፡እስክትወልድ፡ድረስ። ስሙንም፡የሱስ፡አለው።* ሉቃ፡ ፪፡ ፯።

ምዕራፍ፡ ፪፡

፩፡ *የሱስም፡ በቤተ፡ ልሔም፡ በተወለደ፡ ጊዜ፡ በይሁዳ፡ ዕፃ፡ በንጉሡ፡ በሄሮድስ፡ ዘመን። እነሆ፡ ሰብአ፡ ሰገል፡ ከምሥራቅ፡ ወደ፡ የሩሳሌም፡ መጡ።
*ሉቃ፡ ፪፡ ፩—፯።

፪፡ ኢያሉ። ወደት፡ነው፡የተወለደው፡የአይሁድ፡ ንጉሥ።* ኮከቡን፡ በምሥራቅ፡ አይተናልና፡ መጥተንማልና፡ እንሰግድለት፡ ዘንድ፡ *ዘኍል፡ ፳፬፡ ፲፯።

፫፡ ሄሮድስ፡ ንጉሥም፡ ሰምቶ፡ ደነገፀ፡ የሩሳሌምም፡ ሁሉ፡ ከርሱ፡ ጋራ።

፬፡ የካህናትንም፡ አለቆች፡ ሁሉ፡የሕዝብንም፡ጻፎች፡ ሰበሰበ፡ ጠየቃቸውም፡ በወዴት፡ ይወለዳል፡ክርስቶስ፡ብሎ።

፭፡ እርሳቸውም፡አሉት፡በቤተ፡ልሔም፡በይሁዳ፡ ዕፃ። እንደዚህ፡ *በነቢይ፡ተጽፏልና። *ሚክ፡ ፭፡ ፩።
ዮሐ፡ ፯፡ ፵፪።

፮፡ አንቺም፡ቤተ፡ልሔም፡ የይሁዳ፡ምድር፡ከይሁዳ፡ አለቆች፡ ሁሉ፡ ከቶ፡ አታንሺም። ካንቺ፡ መስፍን፡ ይወጣልና፥ ሕዝቤ፡ እሥራኤልን፡ የሚጠብቅ።

፯፡ ከዚያ፡ በኋላ፡ሄሮድስ፡ የሰገልን፡ሰዎች፡በስውር፡ ጸራቸው፡ ከርሳቸውም፡ የታያቸውን፡ የኮከብን፡ ዘመን፡ ቲረዳ።

፰፡ወደ፡ቤተ፡ልሔምም፡ሰደዳቸው፡አላቸውም። ሒዱ፡ ስለ፡ ተወለደውም፡ ሕፃን፡ እጅግ፡መርምሩ። ባገኛችሁትም፡ ጊዜ፡ ንገሩኝ፡ እኔም፡ ደግሞ፡ መጥቼ፡ እሰግድለት፡ ዘንድ።

፱፡ እርሳቸውም፡ ከንጉሡ፡ ሰምተው፡ ሔዱ። እነሆ፡በምሥራቅም፡ ያዩት፡ ኮከብ፡ይመራቸው፡ ነበር፡ ሕፃኑ፡ ባለበቱ፡ ላይ፡ መጥቶ፡ እስኪቆም፡ ድረስ።

፲፡ ኮከቡንም፡ ባዩ፡ ጊዜ፡ እጅግ፡ ታላቅ፡ ደስታ፡ ደስ፡ አላቸው።

፲፩፡ ወደ፡ ቤትም፡ መጡ፡ ሕፃኑንም፡ ከናቱ፡ ከማርያም፡ ጋራ፡ አገኙት። ወድቀውም፡ ሰገዱለት፡ ሣፅናቸውንም፡ ከፈቱ፡ እጅ፡ መንሻም፡ ሰጡት፡ ወርቅ፡ ዕጣንም፡ከርቤም። መዝ፡ ፸፪፡ ፲፡ ፲፭። ኢሳ፡ ፷፡ ፮።

፲፪፡ በሕልምም፡ ተገለጠላቸው፡ ወደ፡ ሄሮድስ፡ እንዳይመለሱ። በሌላም፡ መንገድ፡ ወደገራቸው፡ ሔዱ።

፲፫፡ እርሳቸውም፡ ካለፉ፡ በኋላ፡ እነሆ፡ የእግዚአብሔር፡ መልክተኛ፡ ለዮሴፍ፡ በሕልም፡ ታየው፡ እንደዚህ፡ ሲል። ተነሣ፡ ሕፃኑን፡ ያዘህ፡ ከናቱ፡ ጋራ፡ ወደ፡

---

# የጌታችን ፡ የየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ቅዱስ ፡ ወንጌል ፡ እንደ ፡ ጻፈው፡ ቅዱስ ፡ ማቴዎስ።

ምዕራፍ፡ ፩፤

፩፤ የየሱስ፡ክርስቶስ፡የልደቱ፡መጽሐፍ፡ የዳዊት፡ ልጅ፡ የአብርሃም፡ ልጅ። ሉቃ፡ ፫፤ ፳፫፤—፴፰።

፪፤ አብርሃም፡ ይስሐቅን፡ ወለደ። ይስሐቅም፡ ያዕቅብን፡ ወለደ። ያዕቀብም፡ ይሁዳን፡ ወለደ፡ ወንድሞቹንም። ዘፍ.ጥ፡ ፳፩፤ ፫፤ ፲፪። ፳፭፤ ፳፮። ም፡ ፳፱፤ ፴፭። ም፡ ፵፱፤ ፲።

፫፤ ይሁዳም፡ ፋሬስን፡ ዛራንም፡ ወለደ፡ ከትእማር። ፋሬስም፡ኤስሮምን፡ወለደ፡ኤስሮምም፡አራምን፡ ወለደ። ዘፍ.ጥ፡ ፴፰፤ ፳፱፤ ፴። ፩፤ ዜና፡ ፪፡ ፭፡ ፱።

፬፤ አራምም፡አሚናዳብን፡ወለደ፡አሚናዳብም፡ ነአሶንን፡ ወለደ፡ ነአሶንም፡ ሰልሞንን፡ ወለደ። ፩፤ ዜና፡ ፪፡ ፲።

፭፡ ሰልሞንም፡ ቦዔዝን፡ ወለደ፡ከራኬብ። ቦዔዝም፡ ዮቤድን፡ ወለደ፡ ከሩት። ዮቤድም፡ እሤይን፡ ወለደ። ሩት፡ ፬፡ ፲፫፤—፳፪።

፮፡ እሴይም፡ ዳዊትን፡ ንጉሥን፡ ወለደ። ዳዊት፡
ንጉሥም፡ ሰሎሞንን፡ ወለደ፡ ከኦሪያ፡ ምሽት።
፪፡ ሳሙኤ፡ ፲፪፡ ፳፬።
፯፡ ሰሎሞንም፡ ሮብዓምን፡ ወለደ፡ ሮብዓምም፡
አቢያን፡ ወለደ፡ አቢያም፡ አሳን፡ ወለደ።
፩፡ ዜና፡ ፫፡ ፲።
፰፡ አሳም፡ ዮሣፍጥን፡ ወለደ። ዮሣፍጥም፡ ዮራ
ምን፡ ወለደ፡ ዮራምም፡ ዖዝያንን፡ ወለደ።
፩፡ ነገሥ፡ ፲፭፡ ፳፬። ፳፪፡ ፶፩። ፩፡ ዜና፡ ፫፡ ፲፩።
፱፡ ዖዝያንም፡ ዮአታምን፡ ወለደ። ዮአታምም፡
አካዝን፡ ወለደ። አካዝም፡ ሕዝቅያስን፡ ወለደ።
፲፡ ሕዝቅያስም፡ ምናሴን፡ ወለደ። ምናሴም፡ አ
ሞንን፡ ወለደ። አሞንም፡ ዮስያስን፡ ወለደ።
፲፩፡ ዮስያስም፡ ኢኮንያንን፡ ወለደ፡ ወንድሞቹን
ም፡ በባቢሎን፡ ምርኮ፡ ጊዜ።
፲፪፡ ከባቢሎንም፡ ምርኮ፡ በኋላ፡ ኢኮንያን፡ ሰላት
ያልን፡ ወለደ፡ ሰላትያልም፡ ዘሩባቤልን፡ ወለደ።
ዕዝ፡ ፫፡ ፪።
፲፫፡ ዘሩባቤልም፡ አቢዩድን፡ ወለደ፡ አቢዩድም፡
ኤልያቄምን፡ ወለደ፡ ኤልያቄምም፡ አዞርን፡ ወለደ።
፲፬፡ አዞርም፡ ሳዶቅን፡ ወለደ፡ ሳዶቅም፡ አኪምን፡
ወለደ፡ አኪምም፡ ኤልዩድን፡ ወለደ።
፲፭፡ ኤልዩድም፡ አልዓዛርን፡ ወለደ፡ አልዓዛርም፡
ማታንን፡ ወለደ፡ ማታንም፡ ያዕቆብን፡ ወለደ።
፲፮፡ ያዕቆብም፡ ዮሴፍን፡ ወለደ፡ የማርያምን፡ ባ
ል፡። ክርሰቶስ፡ የሱስ፡ የተወለደ* ክርስቶስ፡ የተባለው።
* ም፡ ፳፯፡ ፲፯፡ ፳፪።
፲፯፡ ትውልድም፡ ሁሉ፡ ከአብርሃም፡ እስከ፡ ዳዊ
ት፡ አሥራ፡ አራት፡ ትውልድ። ከዳዊትም፡ እስከ፡ ባ
ቢሎን፡ ምርኮ፡ አሥራ፡ አራት፡ ትውልድ። ከባቢሎን
ም፡ ምርኮ፡ እስከ፡ ክርስቶስ፡ አሥራ፡ አራት፡ ትው
ልድ።
፲፰፡ የየሱስ፡ ክርስቶስም፡ ልደቱ፡ እንዲህ፡ ነበረ።
እናቱ፡ ማርያም፡ ለዮሴፍ፡ በታጨች፡ ጊዜ፡ ሳይገናኙ፡
ከመንፈስ፡ ቅዱስ፡ ፀንሳ፡ ተገኘች። ሉቃ፡ ፩፡ ፴፭።
፲፱፡ ባሏዋም፡ ዮሴፍ፡ ጻድቅ፡ ነበረ፡ በሕዝብም፡
ፊት፡ ሊገልጻት፡ አልወደደም፡ አሰበም፡ ሰውር፡ ሊተ
ዋት።
፳፡ እርሱ፡ ግን፡ ይህነን፡ ሲያስብ፡ እነሆ፡ የእግዚአ
ብሔር፡ መልክተኛ፡ በሕልም፡ ታየው፡ እንዲህ፡ ሲል።
ዮሴፍ፡ ሆይ፡ የዳዊት፡ ልጅ፡ ሚስትህን፡ ማርያምን፡ ለ
መውሰድ፡ አትፍራ። በርስዋ፡ የሚወለደው፡ ከመን
ፈስ፡ ቅዱስ፡ ነውና። ቍ፡ ፲፰።
፳፩፡ ልጅም፡ ትወልዳለች፡* ስሙንም፡ የሱስ፡ ት
ለዋለህ፡† ሕዝቡን፡ ከኃጢአታቸው፡ ያድናቸዋልና።
*ሉቃ፡ ፩፡ ፴፩። ፪፡ ፳፩። †የሐዋ፡ ፬፡ ፲፪።
፳፪፡ ይህም፡ ሁሉ፡ ሆነ፡ ከእግዚአብሔር፡ ዘንድ፡*
በነቢይ፡ የተባለው፡ ሊፈጸም፡ የሚል። *ኢሳ፡ ፯፡ ፲፬።
፳፫፡ እነሆ፡ ድንግል፡ ትፀንሳለች፡ ልጅም፡ ትወልዳ
ለች፡ ስሙንም፡ አማኑኤል፡ ይሉታል፡ ትርጓሜው፡
እግዚአብሔር፡ ከኛ፡ ጋራ፡ የሆነ። ሉቃ፡ ፩፡ ፴፩።
፳፬፡ ዮሴፍም፡ ከንቅልፉ፡ ተነሥቶ፡ የእግዚአብ
ሔር፡ መልክተኛ፡ እንዳዘዘው፡ አደረገ፡ ሚስቱንም፡
ማርያምን፡ ወሰዳት።
፳፭፡ አላወቃትምም፡ *የበክር፡ ልጅዋን፡ እስክትወ
ልድ፡ ድረስ። ስሙንም፡ የሱስ፡ አለው።* ሉቃ፡ ፪፡ ፯።

## ምዕራፍ፡ ፪፡

፩፡ *የሱስም፡ በቤተ፡ ልሔም፡ በተወለደ፡ ጊዜ፡ በ
ይሁዳ፡ ዕፃ፡ በንጉሡ፡ በሄሮድስ፡ ዘመን። እነሆ፡ ሰብ
አ፡ሰገል፡ ከምሥራቅ፡ ወደ፡ የሩሳሌም፡ መጡ።
*ሉቃ፡ ፪፡ ፩—፯።
፪፡ ኢያሉ። ወደት፡ ነው፡ የተወለደው፡ የአይሁድ፡
ንጉሥ።* ኮከቡን፡ በምሥራቅ፡ አይተናልና፡ መጥተ
ንማልና፡ እንሰግድለት፡ ዘንድ። *ዘኍል፡ ፳፬፡ ፲፯።
፫፡ ሄሮድስ፡ ንጉሥም፡ ሰምቶ፡ ደነገፀ፡ የሩሳሌም
ም፡ ሁሉ፡ ከርሱ፡ ጋራ።
፬፡ የካህናትንም፡ አለቆች፡ ሁሉ፡ የሕዝብንም፡ ጻ
ፎች፡ ሰበሰበ፡ ጠየቃቸውም፡ በወዴት፡ ይወለዳል፡ ክ
ርስቶስ፡ ብሎ።
፭፡ እርሳቸውም፡ አሉት፡ በቤተ፡ ልሔም፡ በይሁዳ፡
ዕፃ። እንዲህ፡ *በነቢይ፡ ተጽፎዋልና። *ሚካ፡ ፭፡ ፩።
ዮሐ፡ ፯፡ ፵፪።
፮፡ አንቺም፡ ቤተ፡ ልሔም፡ የይሁዳ፡ ምድር፡ ከይሁ
ዳ፡ አለቆች፡ ሁሉ፡ ከቶ፡ አታንሺም። ካንቺ፡ መስፍ
ን፡ ይወጣልና፡ ሕዝቤ፡ እሥራኤልን፡ የሚጠብቅ።
፯፡ ከዚያ፡ በኋላ፡ ሄሮድስ፡ የሰገልን፡ ሰዎች፡ በስው
ር፡ ጸራቸው፡ ከርሳቸውም፡ የታያቸውን፡ የኮከብን፡
ዘመን፡ ቲረዳ።
፰፡ ወደ፡ ቤተ፡ ልሔምም፡ ሰደዳቸው፡ አላቸውም።
ሒዱ፡ ስለ፡ ተወለደውም፡ ሕፃን፡ እጅግ፡ መርምሩ።
ባገኛችሁትም፡ ጊዜ፡ ንገሩኝ፡ እኔም፡ ደግሞ፡ መጥቼ፡
እሰግድለት፡ ዘንድ።
፱፡ እርሳቸውም፡ ከንጉሥ፡ ሰምተው፡ ሔዱ።
እነሆ፡ በምሥራቅም፡ ያዩት፡ ኮከብ፡ ይመራቸው፡ ነበ
ር፡ ሕፃኑ፡ ባለበቱ፡ ላይ፡ መጥቶ፡ እስኪቆም፡ ድረስ።
፲፡ ኮከቡንም፡ ባዩ፡ ጊዜ፡ እጅግ፡ ታላቅ፡ ደስታ፡ ደ
ስ፡ አላቸው።
፲፩፡ ወደ፡ ቤትም፡ መጡ፡ ሕፃኑንም፡ ከናቱ፡ ከማ
ርያም፡ ጋራ፡ አገኙት። ወድቀውም፡ ሰገዱለት፡ ሣፅ
ኖቸውንም፡ ከፈቱ፡ እጅ፡ መንሻም፡ ሰጡት፡ ወርቅ፡
ዕጣንም፡ ከርቤም። መዝ፡ ፸፪፡ ፲፡ ፲፭። ኢሳ፡ ፷፡ ፮።
፲፪፡ በሕልምም፡ ተገለጠላቸው፡ ወደ፡ ሄሮድስ፡
እንዳይመለሱ። በሌላም፡ መንገድ፡ ወደ፡ ገራቸው፡
ሔዱ።
፲፫፡ እርሳቸውም፡ ካለፉ፡ በኋላ፡ እነሆ፡ የእግዚአ
ብሔር፡ መልክተኛ፡ ለዮሴፍ፡ በሕልም፡ ታየው፡ እን
ዲህ፡ ሲል። ተነሣ፡ ሕፃኑን፡ ያዘህ፡ ከናቱ፡ ጋራ፡ ወደ፡

ምስርም፡ ሽሽ፡ ከዚያም፡ ተቀመጥ፡ እስክነግርህ፡ ድረስ፡ ሄሮድስ፡ ሕፃኑን፡ ሊገድለው፡ ይሻዋልና።

፲፬፤ እርሱም፡ ተነሥቶ፡ ሕፃኑንና፡ እናቱን፡በሌት፡ ወሰደ፡ ወደ፡ ምስርም፡ ሔደ።

፲፭፤ ከዚያም፡ ተቀመጠ፡ ሄሮድስ፡ እስኪሞት፡ ድረስ። ከእግዚአብሔር፡ዘንድ፡ *በነቢይ፡የተባለው፡ ይፈጸም፡ ዘንድ፡ እንዲህ፡ ሲል። ከምስር፡ ልጄን፡ ጸራሁት።
*ሆሴ፡ ፲፩፤ ፩፡፡

፲፮፤ ከዚያ፡ወዲያ፡ሄሮድስ፡የሰገል፡ሰዎች፡እንደ፡ ተሣለቁበት፡ ባየ፡ ጊዜ፡ እጅግ፡ ተቈጣ፡ ሰደደም፡ በቤተ፡ልሔም፡ባጠገብዋም፡ያሉትን፡ሕፃናትን፡ሁሉ፡ ገደለ። ሁለት፡ አመት፡ የሆነውን፡ ሁሉ፡ ከዚያም፡ የሚያንሰውን። ከሰብአ፡ ሰገል፡ በጠየቀው፡ ዘመን፡ ቍጥር።

፲፯፤ በዚያን፡ ጊዜ፡ ተፈጸመ፡ በነቢዩ፡ *በኤርምያስ፡ የተባለው፡ እንዲህ፡ ሲል።
*ኤር፡ ፴፩፤ ፲፭፡፡

፲፰፤ ድምፅ፡ በራማ፡ ተሰማ፡ ልቅሶ፡ዋይታም፡ ዉኸትም፡ እጅግ። *ራሔል፡ ስለ፡ ልጆችዋ፡ አለቀሰች፡ መጽናናትም፡ አልተቻላትም፡ የሉምና።
*ዘፍ.ጥ፡ ፴፭፤ ፲፱፡፡

፲፱፤ ሄሮድስም፡ በሞተ፡ ጊዜ፡ እነሆ፡ የእግዚአብሔር፡ መልክተኛ፡ ለዮሴፍ፡ በሕልም፡ ታየ፡ በምስር።

፳፤ እንዲህ፡ ሲል። ተነሣ፡ሕፃኑንና፡እናቲቱን፡ ውሰድ፡ ወደ፡ እሥራኤልም፡ምድር፡ሒድ። *የሕፃኑን፡ ነፍስ፡ የሚሹ፡ ሙተዋልና።
*ዘፀአ፡ ፬፤ ፲፱፡፡

፳፩፤ እርሱም፡ ተነሥቶ፡ ሕፃኑን፡እናቲቱንም፡ ወሰደ፡ ወደ፡ እሥራኤልም፡ ምድር፡ መጣ።

፳፪፤ አርኬላዎስም፡ በይሁዳ፡ ባባቱ፡ በሄሮድስ፡ ፈንታ፡ እንደ፡ ነገሠ፡ ሰምቶ፡ ከዚያ፡ እንዲሔድ፡ ፈራ። በሕልምም፡ ተገለጠለት፡ ወደ፡ ገሊላም፡ አገር፡ ሔደ።

፳፫፤ መጣም፡ ናዝሬትም፡ በምትባል፡ አገር፡ ተቀመጠ።በነቢያት፡የተባለው፡እንዲፈጸም፡ *ናዝራዊ፡ ይባል፡ዘንድ። *ሉቃ፡ ፩፤ ፳፮፡፡ ኢሳ፡ ፲፩፤ ፩፡፡ ፶፫፤ ፪፡፡
ዮሐ፡ ፩፤ ፵፮፡፡ ዘካ፡ ፮፤ ፲፪፡፡

## ምዕራፍ፡ ፫፤

፩፤ በዚያ፡ ዘመን፡ ዮሐንስ፡ መጥምቁ፡ መጣ፡በይሁዳ፡ ምድረ፡ በዳ፡ኢየሰበከ፡ ኢያለም።
ማር፡ ፩፤ ፩፤—፰፡፡ ሉቃ፡ ፫፤ ፩—፰፡፡

፪፤ ንስሑ፡ ግቡ፡ መንግሥተ፡ሰማያት፡ቀርባለችና።
ም፡ ፬፤ ፲፯፡፡

፫፤ እንዲሁ፡ *በኢሳይያስ፡ ነቢይ፡ ተብሎዋልና፡ ባለ፡ ጊዜ። ያዋጅ፡ነጋሪ፡ቃል፡በምድረ፡ በዳ፡የሚጮህ። የእግዚአብሔርን፡ መንገድ፡ አብጁ፡ ጎዳናውንም፡ አቅኑለት።
*ኢሳ፡ ፵፤ ፫፡፡

፬፤ የዮሐንስም፡ *ልብሱ፡ የግመል፡ ጸጕር፡ ነበረ፡ የቀርበትም፡ መታጠቂያ፡ በወገቡ፡ላይ። ምግቡም፡ አንበጣ፡ የጣዝማም፡ ማር።
*፪፤ ነገሥ፡ ፩፤ ፰፡፡

፭፤ የዚያን፡ ጊዜ፡ ወደርሱ፡ ይወጡ፡ ነበር፡ የሩሳሌም፡ ይሁዳም፡ ሁሉ፡ በዮርዳኖስም፡ዙርያ፡ያለ፡አገር፡ ሁሉ።

፮፤ በዮርዳኖስም፡ ይጠመቁ፡ ነበሩ፡ ኃጢአታቸውን፡ አስታውቀው።

፯፤ ከፈሪሳውያንና፡ ከሰዱቃውያንም፡ እጅግ፡ ሁነው፡ ወደ፡ ጥምቀቱ፡ ሲመጡ፡ ባየ፡ ጊዜ፡ አላቸው። እላንተ፡ *የእባብ፡ ልጆች፡ ማን፡ አመለከታችሁ፡ ከሚመጣው፡ ቍጣ፡ እንድትሸሹ።
*ም፡ ፳፫፤ ፴፫፡፡

፰፤ አሁንም፡ ለንስሐ፡ የሚገባ፡ ፍሬ፡ አድርጉ።

፱፤ በነፍሳችሁም፡ ትሉ፡ ዘንድ፡ *አባታችን፡ አብርሃም፡ነው፡ አይምሰላችሁ። እኔ፡እነግራችኋለሁና፡ እግዚአብሔር፡ ቻይ፡ እንደሆነ፡ከነዚህ፡ ደንጎች፡ ለአብርሃም፡ ልጆች፡ ለማስነሣት።
*ዮሐ፡ ፰፤ ፴፫፤ ፴፱፡፡
ሮሜ፡ ፪፤ ፳፰፤ ፳፱፡፡

፲፤ አሁንም፡ ደግሞ፡ ምሳር፡ በዛፎች፡ስር፡ ላይ፡ ተቀምጦዋል። ዛፉም፡ ሁሉ፡መልካም፡ፍሬ፡ የማታፈራ፡ ትቈረጣለች፡ ወደ፡ እሳትም፡ ትጨመራለች።
ሉቃ፡ ፲፫፤ ፯፤ ፱፡፡

፲፩፤ እኔ፡ በውኃ፡ አጠመቃችኋለሁ፡ለንስሐ። ከኔ፡ በኋላ፡ግን፡የሚመጣው፡እርሱ፡ከኔ፡ይበረታል።ጫማውን፡መሸከም፡የማይገባኝ። እርሱ፡በመንፈስ፡ቅዱስ፡ በእሳትም፡ ያጠምቃችኋል። ዮሐ፡ ፩፤ ፳፮፤ ፳፯፡፡

፲፪፤ መሽን፡ በጁ፡ ያለ፡ አውድማውን፡ የሚያነጸበት። ስንዴውንም፡ በጎታው፡ ይሰበስባል፡ †ገለባውን፡ግን፡በማይጠፋ፡እሳት፡ያቃጥለዋል። ም፡ ፲፫፤ ፴፡፡
†መዝ፡ ፩፤ ፬፡፡

፲፫፤ በዚያን፡ ጊዜ፡ የሱስ፡ ከገሊላ፡ ወደ፡ ዮርዳኖስ፡ መጣ፡ ወደ፡ዮሐንስ፡ ከርሱ፡ለመጠመቅ።
ማር፡ ፩፤ ፱—፲፩፡፡ ሉቃ፡ ፫፤ ፳፩፤ ፳፪፡፡
ዮሐ፡ ፩፤ ፴፩፤—፴፬፡፡

፲፬፤ ዮሐንስም፡ እምቢ፡ አለው፡ እንዲህ፡ ሲል። እኔ፡ ካንተ፡ለመጠመቅ፡ እሻለሁ፡አንተንም፡ ወደኔ፡ ትመጣለህ።

፲፭፤ የሱስም፡ መለሰለት፡ አለውም። ተው፡ ዛሬስ፡ እንዲሁ፡ ይገባናልና፡ ጽድቅን፡ ሁሉ፡ እንፈጽም፡ ዘንድ። ከዚያ፡ ወዲያ፡ ተወው።

፲፮፤ የሱስም፡ ከተጠመቀ፡ በኋላ፡ የዚያን፡ ጊዜ፡ ከውኃው፡ ወጣ። እነሆም፡ ሰማዮች፡ ተከፈቱለት፡ የእግዚአብሔርም፡መንፈስ፡እንደ፡ ርግብ፡ ሲወርድ፡ አየ፡ በርሱም፡ ላይ፡ ሲቀመጥ።

፲፯፤ ከሰማዮችም፡ *ድምፅ፡መጣ፡እንዲህ፡ሲል። ይህ፡ ነው፡ ልጄ፡ የምወደው፡ በርሱ፡ ደስታዬን፡ የማይበት። *ም፡ ፲፯፤ ፭፡፡ ኢሳ፡ ፵፪፤ ፩፡፡

## ምዕራፍ፡ ፬፤

፩፤ ከዚያ፡ወዲያ፡ መንፈስ፡የሱስን፡ወደ፡ ምድረ፡ በዳ፡ አወጣው፡ ከዲያብሎስ፡ሊፈተን።
ማር፡ ፩፤ ፲፪፤ ፲፫፡፡ ሉቃ፡ ፬፤ ፩—፲፫፡፡ ዕብ፡ ፬፤ ፲፭፡፡

፪፥ *አርባ፡ቀንም፡አርባ፡ ሌሊትም፡ ከጾመ፡በኋላ፡ ተራበ።
*ዘፀአ፡ ፴፬፥ ፳፰።

፫፥ ፈታኙም፡ መጣበት፡ አለውም። የእግዚአብሔርስ፡ ልጅ፡ እንደ፡ ሆንህ፡ በል፡ እሌህ፡ ደንጎች፡ እንጀራ፡ እንዲሆኑ።
ዘፀአ፡ ፫፥ ፩፥—፰።

፬፥ እርሱም፡መለሰለት፡ አለውም። *ተጽፍዋል፡ ሰው፡ በንጀራ፡ ብቻ፡ እንደይድን፡ ከእግዚአብሔር፡ አፍ፡በምትወጣው፡ቃል፡ሁሉ፡እንጂ። *ዘዳግ፡ ፰፥ ፫።

፭፥ ከዚያም፡በኋላ፡ ሰይጣን፡ ወደ፡ *ቅድስት፡ አገር፡ ወሰደው፡ በቤተ፡ መቅደስም፡ ጫፍ፡ ላይ፡ አቆመው።
*ም፡ ፳፯፥ ፶፫።

፮፥ አለውም።የእግዚአብሔር፡ልጅ፡እንደ፡ሆንህ፡ ሰውነትህን፡ ጣል፡ ወደ፡ ታች። መልክተኞቹን፡ ስላንተ፡ እንዲያስ፡ *ተጽፍዋልና፡ በጃቸውም፡ ያነሡኻል፡ እግርህ፡በደንጊያ፡ እንደትሰናከል።
*መዝ፡ ፺፩፥ ፲፩፥—፲፮።

፯፥ የሱስም፡ አለው። ደግሞ፡*ተጽፍዋል፡ አምላክህን፡ እግዚአብሔርን፡ አትፈታተነው።
*ዘዳግ፡ ፮፥ ፲፮።

፰፥ ደግሞም፡ ሰይጣን፡ ወደ፡ ረጅጅም፡ ተራራ፡ ወሰደው፡ የዓለምንም፡ ሁሉ፡ መንግሥታትና፡ክብራቸውን፡ አሳየው፡

፱፥ አለውም። ይህነን፡ ሁሉ፡እሰጥሃለሁ፡ለኔ፡ ሰግደህ፡ ብትወድቅ።

፲፥ የዚያን፡ጊዜ፡ የሱስ፡ አለው። ከኔ፡ ራቅ፡ አንተ፡ ሰይጣን። *ተጽፍዋልና፡ ለእግዚአብሔር፡ለአምላክህ፡ ስገድ፡ እርሱንም፡ ብቻውን፡ አምልክ።
*ዘዳግ፡ ፮፥ ፲፫።

፲፩፥ ከዚያ፡ ወዲያ፡ ሰይጣን፡ ተወው፡ መላእክትም፡ እነሆ፡ መጡ፡ ለርሱም፡ *ያገለግሉ፡ ነበሩ።
*ዮሐ፡ ፩፥ ፶፩። ዕብ፡ ፩፥ ፮፥ ፲፬።

፲፪፥ የሱስም፡ ዮሐንስ፡ እንደ፡ ተያዘ፡ በሰማ፡ ጊዜ፡ ወደ፡ ገሊላ፡ ሔደ። ም፡ ፲፩፥ ፫።

፲፫፥ ናዝሬትንም፡ተወ፡መጥቶም፡በቅፈርናሆም፡ በባሕር፡ አጠገብ፡ ባለች፡ ተቀመጠ፡ በዛብሎንና፡ በንፍታሌም፡ ድርቻ።

፲፬፥ ይፈጸም፡ዘንድ፡ *በኢሳይያስ፡በነቢዩ፡ የተባለው፡ እንደዚህ፡ሲል። *ኢሳ፡ ፱፥ ፩፥—፪።

፲፭፥ የዛብሎን፡ ምድርና፡ የንፍታሌም፡ ምድር፡ በባሕር፡ መንገድ፡በዮርዳኖስ፡ ማዶ፡ የአሕዛብ፡ገሊላ።

፲፮፥ በጨለማ፡ የሚኖር፡ ወገን፡ ታላቅ፡ ብርሃን፡ አየ። በጨለማና፡ በሞትም፡ ጽላ፡ ለሚኖሩ፡ ብርሃን፡ ወጣላቸው።

፲፯፥ ከዚያ፡ ዘመን፡ በኋላ፡ የሱስ፡ ማስተማር፡ ጀመረ፡ እንደዚህ፡ ሲል። ንስሐ፡ ግቡ፡ መንግሥተ፡ ሰማያት፡ ቀርባለችና። ም፡ ፫፥ ፪። ሉቃ፡ ፬፥ ፲፭።

፲፰፥ የሱስም፡ በገሊላ፡ባሕር፡አጠገብ፡ ሲመላለስ፡ ሁለት፡ ወንድማማች፡ አየ፡ ሲሞንን፡ ጴጥሮስ፡ የሚሉትን፡ እንድርያስንም፡ ወንድሙን፡ መረባቸውን፡ ወደ፡ ባሕር፡ ሲጥሉ፡ አፅማጆች፡ ነበሩና።
ማር፡ ፩፥ ፲፮፥—፲፱። ሉቃ፡ ፭፥ ፩፥—፲፩።

፲፱፥ አላቸውም። በኋላዬ፡ ኑ፡ ሰውም፡ እንድታፀምዱ፡ አድርጋችኋለሁ። ም፡ ፲፫፥ ፵፯። ሕዝ፡ ፵፯፥ ፲።

፳፥ እርሳቸውም፡የዚያን፡ጊዜውን፡መረባቸውን፡ ትተው፡ ተከተሉት። ም፡ ፲፱፥ ፳፯።

፳፩፥ ከዚያም፡ ጥቂት፡ አልፎ፡ ሌሎችን፡ ሁለት፡ ወንድማማች፡ አየ። ያዕቆብን፡ የዘብዴዎስን፡ ልጅ፡ ዮሐንስንም፡ ወንድሙን፡ በታንኳ፡ ካባታቸው፡ ከዘብዴዎስ፡ ጋራ፡ መረባችውን፡ ሲያበጁ፡ጸራቸውም።

፳፪፥ እርሳቸውም፡ የዚያን፡ጊዜውን፡ ታንኳቸውንና፡ አባታቸውን፡ ትተው፡ ተከተሉት።

፳፫፥ *የሱስም፡ ገሊላን፡ሁሉ፡ ይዞር፡ ነበረ፡ በመስጊዳቸውም፡ ያስተምር፡ ነበር፡የመንግሥትንም፡ ወንጌል፡ ይሰብክ፡ ነበር፡ ደዌንም፡ ሁሉ፡ ድካምንም፡ ሁሉ፡ በሕዝብ፡ ያለውን፡ ይፈውስ፡ ነበረ።
*ሉቃ፡ ፬፥ ፲፭፥ ፴፩። የሐዋ፡ ፲፥ ፴፰።

፳፬፥ ወሬውም፡ በሶርያ፡ሁሉ፡ወጣ። ወደርሱም፡ የታመሙትን፡ ሁሉ፡ *አመጡ፡ ደውያቸውምና፡ ሥቃያቸው፡ ልዩ፡ ልዩ፡ የሆነ። አጋንንትም፡የነበሩባቸውን፡ በወር፡በወርም፡የሚነሣባቸውን፡ወድቀው፡የሚኖሩትንም። ፈወሳቸውም። *ማር፡ ፮፥ ፶፭።

፳፭፥ ብዙም፡ ጉባኤ፡ ተከተሉት፡ ከገሊላ፡ ካሥሩም፡ አገር፡ ከየሩሳሌም፡ ከይሁዳም፡ ከዮርዳኖስም፡ ማዶ። *ሉቃ፡ ፮፥ ፲፯።

## ምዕራፍ፡ ፭፥

፩፥ ብዙ፡ የተሰበሰቡም፡ ባየ፡ ጊዜ፡ወደ፡ ተራራ፡ ወጣ። በተቀመጠም፡ ጊዜ፡ደቀ፡መዛሙርቱ፡ወደርሱ፡ ቀረቡ። ሉቃ፡ ፮፥ ፳፥—፵፱።

፪፥ አፉንም፡ ከፈተ፡ ያስተምራቸውም፡ ነበር፡ እንደዚህ፡ ሲል።

፫፥ በነፍሳቸው፡የተቸገሩ፡የተመሰገኑ፡ናቸው። መንግሥተ፡ሰማያት፡የርሳቸው፡ናትና። ኢሳ፡ ፶፯፥ ፲፭።

፬፥ የሚያለቅሱ፡ የተመሰገኑ፡ ናቸው፡ ይስ፡ ይላቸዋልና። መዝ፡ ፻፳፮፥ ፭። ኢሳ፡ ፷፩፥ ፪። ራእ፡ ፯፥ ፲፯።

፭፥ ገሮች፡የተመሰገኑ፡ናቸው። እርሳቸው፡ምድርን፡ ይወርሳሉና። መዝ፡ ፴፯፥ ፲፩።

፮፥ ጽድቅን፡ የሚራቡ፡የሚጸሙም፡የተመሰገኑ፡ ናቸው። እርሳቸው፡ ይጸግባሉና። መዝ፡ ፶፯፥ ፱።
ኢሳ፡ ፵፩፥ ፲፯። ፶፭፥ ፩፥ ፪። ምሳ፡ ፳፩፥ ፳፩።

፯፥ የሚራሩ፡የተመሰገኑ፡ናቸው፡ ምሕረት፡ያገኛሉና። ም፡ ፳፭፥ ፴፭። ም፡ ፲፩፥ ፳፭። ያዕ፡ ፪፥ ፲፫።

፰፥ ልባቸው፡ የነጻ፡ የተመሰገኑ፡ ናቸው፡ እርሳቸው፡እግዚአብሔርን፡ ያዩታልና። መዝ፡ ፶፩፥ ፲፪።
፩፥ ዮሐ፡ ፫፥ ፪፥ ፫።

፱፥ ዕርቅ፡ የሚያደርጉ፡የተመሰገኑ፡ናቸው። እርሳቸው፡የእግዚአብሔር፡ ልጆች፡ይባላሉና።
ዕብ፡ ፲፪፥ ፲፬። መዝ፡ ፴፬፥ ፲፭።

፲፡ ስለ፡ ጽድቅ፡ የተሰደዱ፡ የተመሰገኑ፡ ናቸው። መንግሥተ፡ ሰማያት፡ የርሳቸው፡ ናትና።

፩፡ ጴጥ፡ ፫፡ ፲፬። ፪፡ ጢሞ፡ ፪፡ ፲፪።

፲፩፡ እላንተ፡ የተመሰገናችሁ፡ ናችሁ፡ በሰደብዋችሁ፡ ባሳደድዋችሁም፡ ጊዜ፡ በላያችሁም፡ ክፋውን፡ ሁሉ፡ ባሉ፡ ጊዜ፡ በሐሰት፡ ስለኔ።

፩፡ ጴጥ፡ ፬፡ ፲፬። ኢሳ፡ ፶፩፡ ፯፡ ፰።

፲፪፡ ደስ፡ ይበላችሁ፡ ሐሤትም፡ አድርጉ። ዋጋችሁ፡ በሰማያት፡ ታላቅ፡ ነውና። *እንዲሁ፡ ነቢያትን፡ ከላንት፡ በፊት፡ የነበሩትን፡ አሳደዋልና።

*ያዕ፡ ፭፡ ፲። ዕብ፡ ፲፩፡ ፴፭—፵።

፲፫፡ እላንተ፡ የምድር፡ ጨው፡ ናችሁ። ጨው፡ ግን፡ አልጫ፡ ከሆነ፡ በምን፡ ይጣፍጣል። የሚረባው፡ የለም፡ ሜዳ፡ ይጣላል፡ እንጂ፡ ሰውም፡ ይረግጠዋል።

ማር፡ ፱፡ ፶። ሉቃ፡ ፲፬፡ ፴፬።

፲፬፡ እላንተ፡ የዓለም፡ ብርሃን፡ ናችሁ። አገር፡ በተራራ፡ ላይ፡ ተሰርታ፡ መሰወር፡ አይቻላትም።

ዮሐ፡ ፰፡ ፲፪። ፊል፡ ፪፡ ፲፭።

፲፭፡ መብራትም፡ አያበሩም፡ በንቅብ፡ ውሥጥ፡ ሊያኖሩት፡ በመቅረዙ፡ ላይ፡ እንጂ፡ በቤት፡ ላሉት፡ ሁሉ፡ እንዲያበራ።

ማር፡ ፬፡ ፳፩—፳፫።

፲፮፡ እንዲሁ፡ *ብርሃናችሁ፡ በሰው፡ ፊት፡ ይብራ፡ መልካሙን፡ ስራችሁን፡ አይተው፡ የሰማዩን፡ አባታችሁን፡ ያመሰግኑት፡ ዘንድ።

*፩፡ ጴጥ፡ ፪፡ ፲፪።

፲፯፡ አይምሰላችሁ፡ የመጣሁ፡ ኦሪትንና፡ ነቢያትን፡ ለመሻር። ለመሻር፡ አልመጣሁም፡ ልፈጽም፡ እንጂ።

ም፡ ፫፡ ፲፭። ሮሜ፡ ፫፡ ፴፩። ፲፡ ፬።

፲፰፡ እውነት፡ እነግራችኋለሁና። ሰማይና፡ ምድር፡ እስኪያልፍ፡ ድረስ፡ የውጣ፡ አንዲቱ፡ ወይም፡ ጽፈትዋ፡ አንዲቱ፡ ከኦሪት፡ አታልፍም፡ ሁሉ፡ እስኪሆን፡ ድረስ።

ሉቃ፡ ፲፮፡ ፲፯። ኢሳ፡ ፵፡ ፮—፰።

፲፱፡ *አንዲቱንም፡ ከለዚህ፡ ትእዛዛት፡ ከጥቃቅኑ፡ የሻረ፡ ለሰውም፡ እንዲሁ፡ ያስተማረ፡ በመንግሥተ፡ ሰማያት፡ ታናሽ፡ ይባላል። †ኢያደረገ፡ ግን፡ የሚያስተምር፡ ይህ፡ በመንግሥተ፡ ሰማያት፡ ታላቅ፡ ይባላል።

*ያዕ፡ ፪፡ ፲። †ዕዝ፡ ፯፡ ፲።

፳፡ እኔ፡ እነግራችኋለሁና፡ ጽድቃችሁ፡ ከጻፎችና፡ ከፈሪሳውያን፡ ጽድቅ፡ ካልበለጠ፡ ወደ፡ መንግሥተ፡ ሰማያት፡ አትገቡም።

፳፩፡ ለቀደሙት፡ የተባለውን፡ ሰማችሁ። አትግደል። የገደለ፡ ይፈረድበታልና።

ዘፀአ፡ ፳፡ ፲፫።

ዘሌዋ፡ ፳፬፡ ፲፯። ዘዳግ፡ ፲፯፡ ፰።

፳፪፡ እኔ፡ ግን፡ እላችኋለሁ። በወንድሙ፡ ላይ፡ በከንቱ፡ የተቈጣ፡ ሁሉ፡ በፍርድ፡ ይፈረድበታል። ወንድሙን፡ ግን፡ ጨርቅ፡ ለባሽ፡ የሚለው፡ በሸንጎ፡ ይፈረድበታል። ደንቆሮም፡ የሚለው፡ በገሃነም፡ እሳት፡ ይፈረድበታል።

፩፡ ዮሐ፡ ፫፡ ፲፭። ኢሳ፡ ፷፮፡ ፳፬።

፳፫፡ ቍርባንህንም፡ በመሠዊያው፡ ላይ፡ ብታቀርብ፡ ከዚያም፡ ብታስብ፡ ለወንድምህ፡ አንዳች፡ በላይህ፡ እንዳለው።

ማር፡ ፲፩፡ ፳፭።

፳፬፡ ቍርባንህን፡ ከዚያ፡ በመሠዊያው፡ ፊት፡ ተወው፡ አስቀድመህም፡ ሒድ፡ ከወንድምህም፡ ጋራ፡ ታረቅ። ኋላም፡ ተመልሰህ፡ ቍርባንህን፡ አቅርብ።

፳፭፡ ከጸላትህ፡ ፈጥነህ፡ ተስማማ፡ ከርሱ፡ ጋራ፡ በመንገድ፡ ሳለህ፡ ጸላትህ፡ ለመኰንን፡ አሳልፎ፡ እንዳይሰጥህ፡ መኰንንም፡ ለአሣሪ፡ ይሰጥሃል፡ ወደ፡ ግዞትም፡ ትጨመራለህ።

ም፡ ፮፡ ፲፬። ፲፰፡ ፴፭።

ሉቃ፡ ፲፱፡ ፶፰፡ ፶፱።

፳፮፡ በውነት፡ እነግርሃለሁ፡ ከዚያ፡ እንዳትወጣ፡ የኋለኛውን፡ ዲናሪ፡ እስክትከፍል፡ ድረስ።

፳፯፡ ሰማችሁ፡ ለቀደሙት፡ እንደ፡ ተባለ፡ አታመንዝር።

ዘፀአ፡ ፳፡ ፲፬።

፳፰፡ እኔ፡ ግን፡ እላችኋለሁ፡ ወደ፡ ሴት፡ ያየ፡ ሁሉ፡ የተመኛትም፡ ፈጽሞ፡ በልቡ፡ አመነዘረባት።

ኢዮብ፡ ፴፩፡ ፩። ፪፡ ጴጥ፡ ፪፡ ፲፬።

፳፱፡ የቀኝ፡ ዓይንህም፡ ብታስትህ፡ አውጥተህ፡ ካንተ፡ ጣለት። ይሻልሃልና፡ አንድ፡ ብልትህ፡ ቢጠፋ፡ አካልህ፡ ሁሉ፡ ገሃነም፡ እንዳይገባ።

ም፡ ፲፰፡ ፱።

ማር፡ ፱፡ ፵፯። ቆል፡ ፫፡ ፭።

፴፡ የቀኝ፡ እጅህም፡ ብታስትህ፡ ቍርጠህ፡ ካንተ፡ ጣላት። ይሻልሃልና፡ አንድ፡ ብልትህ፡ ቢጠፋ፡ አካልህ፡ ሁሉ፡ ገሃነም፡ እንዳይገባ።

፴፩፡ ተባለም። ምሽቱን፡ የፈታ፡ የፍችዋን፡ መጽፍ፡ ይስጣት።

ም፡ ፲፱፡ ፫—፱። ዘዳግ፡ ፳፬፡ ፩።

፴፪፡ እኔ፡ ግን፡ እላችኋለሁ። ምሽቱን፡ የፈታ፡ ሁሉ፡ ያለ፡ ዝሙት፡ መክንያት፡ እርሱ፡ አመንዝራ፡ አደረጋት። የተፈታችውንም፡ ያገባ፡ አመነዘረ።

ሉቃ፡ ፲፮፡ ፲፰። ፩፡ ቆሮን፡ ፯፡ ፲።

፴፫፡ ደግሞ፡ ለቀደሙት፡ የተባለው፡ ሰማችሁ። በሐሰት፡ አትማል፡ መሐላህን፡ ለእግዚአብሔር፡ ፈጽም፡ እንጂ።

ዘፀአ፡ ፳፡ ፯። ዘሌዋ፡ ፲፱፡ ፲፪።

ዘኍል፡ ፴፡ ፫—፲፯።

፴፬፡ እኔ፡ ግን፡ እላችኋለሁ፡ ከቶ፡ አትማሉ። በሰማይ፡ ስንኳ፡ የእግዚአብሔር፡ ዙፋን፡ ናትና።

ኢሳ፡ ፷፮፡ ፩። የሐዋ፡ ፯፡ ፵፱።

፴፭፡ በምድርም፡ የእግሩ፡ ጫማ፡ ናትና። በየሩሳሌምም፡ *የታላቁ፡ ንጉሥ፡ ከተማ፡ ናትና።

*መዝ፡ ፵፰፡ ፫።

፴፮፡ በራስህም፡ አትማል። አንዲት፡ ጸጕር፡ ነጭም፡ ሁና፡ ጥቁርም፡ ሁና፡ ታደርግ፡ ዘንድ፡ አትችልምና።

ም፡ ፳፫፡ ፲፮።

፴፯፡ ነገራችሁ፡ ግን፡ እንዲሁ፡ ይሁን። አዎን፡ አዎን፡ እንኳን፡ እንኳን፡ ከለዚህ፡ የወጣ፡ የክፉ፡ ነውና።

፪፡ ቆሮን፡ ፩፡ ፲፯። ያዕ፡ ፭፡ ፲፪።

፴፰፡ ሰማችሁ፡ እንደ፡ ተባለ። ዓይን፡ በዓይን፡ ጥርስም፡ በጥርስ።

ዘፀአ፡ ፳፩፡ ፳፫፡ ፳፬።

፴፱፡ እኔ፡ ግን፡ እላችኋለሁ። ክፉን፡ አትቃወሙ፡

ነገር፡ ግን፡ ቀኝ፡ ፊትህን፡ ለጸፋህ፡ ሁለተኛውን፡ ደግ
ሞ፡መልስለት። ዮሐ፡፲፰፡ ፳፪፡፳፫። ዘሌዋ፡፲፱፡፲፰።
፵፤ በፍርድም፡ ሊያጣልህ፡ ቀሚስህን፡ሊወስድ
ብህ፡ ለወደደ፡ ደግሞ፡ ዓፅፋህን፡ ተውለት።
፵፩፤ አንድ፡ ምዕራፍም፡ የጐተተህ፡ ከርሱ፡ ጋራ፡
ሒድ፡ ሁለት።
፵፪፤ ለለመነህ፡ ስጥ፡ ካንተ፡ ሊበደርም፡ የወደደ፡
እምቢ፡ አትበለው። ዘዳግ፡ ፲፭፡ ፯—፲፩።
፵፫፤ ሰማችሁ፡ እንደ፡ተባለ። ባልንጀራህን፡ ውደ
ድ፡ ጸላትህንም፡ ጥላ። ዘፀአ፡ ፳፫፡ ፵፭።
ዘሌዋ፡ ፲፱፡ ፲፰።
፵፬፤ እኔ፡ ግን፡ እላችኋለሁ። ጸላቶቻችሁን፡ ውደ
ዱ፡ የሚረግሙዋችሁን፡ ግርኩ፡ ለሚጸልዋችሁም፡
መልካም፡ አድርጉ። ስለሚበድልዋችሁም፡ ስለሚ
ያሳድዋችሁም፡ *ጸልዩ። ሉቃ፡ ፳፫፡ ፴፬።
የሐዋ፡ ፯፡ ፶፱። ሮሜ፡ ፲፪፡ ፲፬፡ ፳።
፵፭፤ በሰማያት፡ ላለ፡ ላባታችሁ፡ *ልጆች፡ ትሆኑ፡
ዘንድ፡ እርሱ፡ ፀሐዩን፡ ለበጎቹም፡ ለክፉቹም፡ ያወ
ጣልና፡ ዝናሙንም፡ በጻድቃንና፡ በኃጥአን፡ ላይ፡ ያዘ
ንማልና። *ኤፌ፡ ፭፡ ፩።
፵፮፤ የሚወድዋችሁንም፡ከወደዳችሁ፡የታለ፡ዋ
ጋችሁ። አጣርቾስ፡ እንደሁ፡ ያደርጉ፡ የለምን።
ሉቃ፡ ፮፡ ፴፪—፴፮።
፵፯፤ ከወንድሞቻችሁም፡ ጋራ፡ ብቻ፡ ብትገናኙ፡
ምን፡ ብልጥ፡ አደረጋችሁ። አጣርቾስ፡ ደግሞ፡እንደ
ሁ፡ ያደርጉ፡ የለምን።
፵፰፤ እንደሁ፡ እላንተ፡ *ፍጹማን፡ ሁኑ፡ የሰማዩ፡
አባታችሁ፡ ፍጹም፡ እንደ፡ ሆነ። *ዘሌዋ፡ ፲፱፡ ፪።

## ምዕራፍ፡ ፮፡

፩፤ ተጠንቀቁ፡ ምጽዋታችሁን፡ በሰው፡ ፊት፡ አታ
ድርጉ፡ ለርሳቸው፡ ትታዩ፡ ዘንድ። እንደሁ፡ካልሆነስ፡
በሰማይ፡ ባለው፡ባባታችሁ፡ ዘንድ፡ ዋጋ፡ የላችሁም።
ም፡ ፳፫፡ ፭፡ ፮።
፪፤ ምጽዋትም፡ ባደረግህ፡ መለከት፡ በፊትህ፡ አ
ታስነፋ። ግብዞች፡ በጉባዔ፡በገቢያም፡ እንዲያደርጉ፡
በሰው፡ፊት፡ ይመሰገኑ፡ ዘንድ። በውነት፡እነግራችኋ
ለሁ፡ ዋጋቸውን፡ ወሰዱ።
፫፤ አንተ፡ ግን፡ ምጽዋት፡ ባደረግህ፡ ጊዜ፡ ግራህ፡
አይወቅ፡ቀኝህ፡የሚሰራውን። ም፡ ፳፭፡፴፯—፵።
ሮሜ፡ ፲፪፡ ፰።
፬፤ ምጽዋትህ፡በስውር፡እንድትሆን።አባትህም፡
በስውር፡ የሚያይ፡ እርሱ፡ በግልጽ፡ ይሰጥሃል።
ደን፡ ፰፡ ፳፰።
፭፤ በጸለይህም፡ ጊዜ፡ እንደ፡ ግብዞች፡ አትሁን።
በጉባዔ፡ባደባባይም፡ ማዕዘን፡ ቁመው፡ ይጸልዩ፡ ዘን
ድ፡ ይወዳሉና፡ ለሰው፡ ሊታዩ። እውነት፡ እነግራችኋ
ለሁ፡ ዋጋቸውን፡ እንደ፡ ወሰዱ።
፮፤ አንተ፡ ግን፡ በጸለይህ፡ ጊዜ፡ ወደ፡ ቤትህ፡ ግባ፡
*ደጅህንም፡ ዝጋ፡ ላባትህም፡ በስውር፡ ለሚያይ፡ ጸ
ልይ። በስውር፡ የሚያይም፡ አባትህ፡ በግልጽ፡ ይሰ
ጥሃል። *፪፡ ነገሥ፡ ፬፡ ፴፫።
፯፤ በጸለያችሁም፡ ጊዜ፡ ነገር፡ አታብዙ፡ እንደ፡ አ
ሕዛብ። በነገራቸው፡ብዛት፡ የሚሰማላቸው፡ይመስ
ላቸዋልና። ኢሳ፡ ፩፡ ፲፭። ማቴ፡ ፳፫፡ ፲፬።
፰፤ አትምሰልዋቸው። *አባታችሁ፡የምትሹትን፡
ያውቃልና፡ እርሱን፡ ሳትለምኑት። እላንተስ፡ እንደ
ሁ፡ ጸልዩ። *ቆ፡ ፴፪።
፱፤ *አባታችን፡ ሆይ፡ በሰማይ፡ የምትኖር፡ ስምህ፡
ይቀደስ። *ሉቃ፡ ፲፩፡ ፪—፬። ዮሐ፡ ፲፯፡ ፬፡ ፮።
፲፤ *መንግሥትህ፡ ትምጻ። ፈቃድህ፡ በሰማይ፡ እ
ንደ፡ ሆነች፡ እንዲሁም፡ በምድር፡ ትሁን።
*ም፡ ፯፡ ፳፩። ሉቃ፡ ፳፪፡ ፵፪። ፲፯፡ ፳—፴፯።
፲፩፤ እንጀራችነን፡ የሚበቃነን፡ ስጠነ፡ ዛሬ።
፪፡ ተሰ፡ ፫፡ ፲፪።
፲፪፤ በደላችነንም፡ ይቅር፡ በለነ፡ እኛ፡ደግመን፡ ለበ
ደሉን፡ ይቅር፡ እንደምንል። ቆ፡ ፲፬፡ ፲፫።
ም፡ ፲፰፡ ፳፩—፴፭። መዝ፡ ፴፪፡ ፭፡ ፮።
፲፫፤ ወደ፡ ፈተናም፡ አታግባነ። ከክፉ፡ አድነነ፡ እን
ጂ። መንግሥት፡ ያንተ፡ ነውና፡ ኃይልም፡ ምስጋናም፡
ለዘላለሙ።አሜን። ፩፡ቆሮ፡፲፡፲፫። ፪፡ጢሞ፡ ፬፡፲፰።
፲፬፤ ለሰዎች፡ ኃጢአታቸውን፡ ይቅር፡ ብትሉ፡ የሰ
ማዩ፡አባታችሁ፡ ደግሞ፡ ይቅር፡ ይላችኋልና።
ማር፡ ፲፩፡፳፭፡ ፳፮።
፲፭፤ ለሰዎች፡ ግን፡ ኃጢአታቸውን፡ይቅር፡ ባትሉ።
አባታችሁም፡ኃጢአታችሁን፡ይቅር፡አይልላችሁም።
፲፮፤ በጾማችሁም፡ ጊዜ፡ አትጸውልጉ፡ እንደ፡ ግብ
ዞች። እርሳቸው፡ ይጸወልጋሉና፡ ፊታቸውንም፡ ይቋ
ጽራሉና፡ ለሰዎች፡እንዲጾሙ፡ ሊታዩ። እውነት፡ እነ
ግራችኋለሁ፡ ዋጋቸውን፡ እንደተቀበሉ።
ኢሳ፡ ፶፰፡ ፭፡ ፮።
፲፯፤ አንተ፡ ግን፡በጾምህ፡ ጊዜ፡ ራስህን፡ ተቀባ፡ ፊ
ትህንም፡ታፀብ። ፪፡ ሳሙኤ፡ ፲፪፡ ፳። መክ፡ ፱፡ ፰።
፲፰፤ ለሰው፡ እንደትታይ፡ ጾመኛ፡ መስለህ፡ ነገር፡
ግን፡ላባትህ፡ በምሥጢር፡ ለሚያይ። በምስጢርም፡
የሚያይ፡ አባትህ፡ በግልጽ፡ ይሰጥሃል። ቆ፡ ፮።
፲፱፤ ለላንተ፡መዝገብ፡አትሰብስቡ፡በምድር፡ላይ።
ትል፡ወደሚበላው፡ ነቀዝም፡ወደሚያነቅዘው፡ ሌቦ
ችም፡ ነድለው፡ ወደሚሰርቁት። ም፡ ፲፱፡ ፳፩፡ ፳፪።
፳፤ ነገር፡ ግን፡ ለላንተ፡ መዝገብ፡ ሰብስቡ፡ በሰማ
ይ። ትል፡ወደማይበላው፡ነቅዝም፡ወደማያነቅዘው፡
ሌቦችም፡ነድለው፡ወደማይሰርቁት። ሉቃ፡፲፪፡፴፫።
ቀለ፡ ፫፡ ፩፡ ፪።
፳፩፤ መዝገባችሁ፡ወደለበት፡ ልባችሁ፡ ከዚያው፡
ይሆናልና። መዝ፡ ፷፪፡ ፲፩።
፳፪፤ የሥጋ፡ መብራት፡ ዓይን፡ ነው። ዓይንህም፡
ጥሩ፡ ብትሆን፡ ሥጋህ፡ሁሉ፡ የበራ፡ ይሆናል።
ሉቃ፡ ፲፩፡ ፴፬—፴፮።

፳፫፤ ዓይንህ፡ግን፡ ታማሚ፡ብትሆን፡ሥጋህ፡ሁሉ፡ የጨለመ፡ ይሆናል። ባንተ፡ ያለውም፡ ብርሃን፡ ጨለማ፡ ከሆነ፡ ጨለማው፡ስንት፡ ይሆን።
መክ፡ ፪፡ ፲፫፡ ፲፬።

፳፬፤ አንድ፡ ባርያ፡ ለሁለት፡ ጌቶች፡ መገዛት፡ አይቻለውም። ወይም፡አንዱን፡ይጸላል፡አንዱንም፡ ይወድዋል። ወይም፡ አንዱን፡ ያከብራል፡ ሁለተኛውንም፡ ይንቃል። ለእግዚአብሔርና፡ ለከብት፡ ትገዙ፡ ዘንድ፡አትችሉም። ፩፡ነገሥ፡ ፲፰፡ ፳፩። ሉቃ፡ ፲፮፡ ፲፫።
፪፡ ቀሮ፡ ፮፡ ፲፬።

፳፭፤ ስለዚህ፡እላችኋለሁ፡ ለሕይወታችሁ፡ *አታስቡ፡ በምትበሉት፡በምጠጡትም፡ለሥጋችሁም፡ በምትለብሱት። ሕይወት፡ ከመብል፡ የምትበልጥ፡ አይደለችምን፡ ሥጋም፡ ከልብስ።
*ሉቃ፡ ፲፪፡፳፪—፴፩። ፊል፡ ፬፡ ፮። ፩፡ ጢሞ፡ ፮፡ ፮።
ዕብ፡ ፲፫፡ ፭።

፳፮፤ ወደ፡ ሰማይ፡ ወፎች፡ ተመልከቱ፡ እንደ፡ይዘሩ፡እንደ፡ያጭዱም፡ በጎታም፡ እንደ፡ይከቱ። የሰማዩም፡ አባታችሁ፡ ይመግባቸዋል። እላንት፡ ከርሳቸው፡ እጅግ፡አትሻሉዋቸውምን። ም፡ ፲፡ ፳፱—፴፩።

፳፯፤ ማነው፡ከላንት፡አስቦ፡በቁመቱ፡ላይ፡አንድ፡ ክንድ፡ መጨመር፡ የሚችል።

፳፰፤ ለምንስ፡ ለልብስ፡ ታስባላችሁ። የምድረ፡ በዳን፡ አበቦች፡ እዩ፡እንደ፡ያድጉ። አይደክሙም፡ አይፈትሉምም።

፳፱፤ እላችሁማለሁ፡ ሰሎሞንስ፡ እንኳ፡ በዚያ፡ ሁሉ፡ ክብሩ፡ ከርሰዋ፡ እንደ፡አንዱ፡ አለበሰም።
፩፡ ነገሥ፡ ፲፡ ፲፡—፳፫። መክ፡ ፪፡ ፬፡—፲፩።

፴፤ የምድረ፡ በዳንም፡ ሣር፡ ዛሬ፡ የሚገኝ፡ ነገም፡ ወደ፡ እቶን፡ የሚጣል፡ እግዚአብሔር፡ እንደሁ፡ የሚያለብሰው፡ ከሆነ። እላንትንን፡ ይልቅ፡ እጅግ፡ አያለብሳችሁም፡ እላንት፡ ሃይማኖት፡ የጐደላችሁ።
መዝ፡ ፺፡ ፮።

፴፩፤ አታስቡ፡ እንጊዴህ፡አትበሉም። ምን፡እንበላለን፡ ምንስ፡ እንጠጣለን፡ምንስ፡ እንለብሳለን።

፴፪፤ ይህነን፡ ሁሉ፡ አሕዛብ፡ ይሹታልና። እላንትስ፡ የሰማዩ፡ አባታችሁ፡ ያውቃል፡ ይህነን፡ ሁሉ፡ እንድትሹ።

፴፫፤ የእግዚአብሔርን፡ መንግሥት፡ ጽድቁንም፡ *አስቀድማችሁ፡እሹ፡ እንጂ፡ †ይህም፡ ሁሉ፡ ይጨመርላችኋል። *ሮሜ፡ ፲፬፡ ፲፯። †፩፡ ነግሥ፡ ፫፡ ፲፫።
መዝ፡ ፴፯፡ ፬።

፴፬፤ ለነገም፡ አታስቡ፡ ነገ፡ ለራሱ፡ ያስባልና። የቀኑስ፡ ክፋቱ፡ ይበቃዋል። ቊ፡ ፲፩። ዘፀአ፡ ፲፮፡ ፲፱።

## ምዕራፍ፡ ፯፤

፩፤ አትፍረዱ፡ እንደ፡ይፈረድባችሁ።
ሮሜ፡ ፪፡ ፩። ፩፡ ቀሮን፡ ፬፡ ፭።

፪፤ በፈረዳችሁት፡ ፍርድ፡ ይፈረድባችኋልና፡ በምትሰፍሩበትም፡ መስፈሪያ፡ ይሰፈርባችኋልና።
ማር፡ ፬፡ ፳፬።

፫፤ ለምንስ፡ በወንድምህ፡ ዓይን፡ ያለውን፡ ስንጣቂ፡ ታያለህ። ባይንህም፡ ያለውን፡ መሰሶ፡ አትመለከትም።

፬፤ እንዴትስ፡ ወንድምህን፡ ትለዋለህ፡ ተወኝ፡ ካይንህ፡ ስንጣቂ፡ ላውጣልህ። እነሆ፡ መሰሶም፡ባይንህ፡ ነው።

፭፤ አንተ፡ ግብዝ፡ አስቀድመህ፡ መሰሶ፡ ካይንህ፡ አውጣ። ከዚያ፡ በኋላም፡ ታያለህ፡ ስንጣቂውን፡ ከወንድምህ፡ ዓይን፡ ታውጣ፡ ዘንድ።

፮፤ *የተቀደሰውን፡ ለውሾች፡አትስጡ፡እንቊችሁንም፡ አትጣሉ፡ በእርያዎች፡ ፊት፡ በግሮቻቸው፡ እንደ፡ ይረግጡት፡ ተመልሰውም፡ እንደ፡ይነክሱዋችሁ።
*ሐጌ፡ ፪፡ ፲፪።

፯፤ ለምኑ፡ ይሰጣችኋልም። እሹ፡ታገኙማላችሁ። ደጅ፡ ምቱ፡ ይከፈትላችኋልም። ማር፡ ፲፩፡ ፳፬።
ሉቃ፡ ፲፩፡ ፱፡—፲፫። ኤር፡ ፳፱፡ ፲፫፡ ፲፬።

፰፤ የለመነ፡ሁሉ፡ይወስዳልና። የፈለገም፡ያገኛል። ደጅም፡ ለመታ፡ ይከፈትለታል።

፱፤ ወይስ፡ ምን፡ ሰው፡ ከላንት፡ ነው፡ ልጁ፡ እንጀራ፡ ቢለምነው፡ በውኑ፡ ደንጊያ፡ ይሰጠዋል።

፲፤ ዓሣስ፡ ቢለምነው፡ እባብን፡ ይሰጠዋል።

፲፩፤ እንኪያስ፡ እላንት፡ ክፉ፡ ስትሆኑ፡ ለልጆቻችሁ፡ መልካም፡ መስጠት፡ ካወቃችሁ፡ እንዴት፡ እጅግ፡ የሰማዩ፡ አባታችሁ፡ ለሚለምነው፡ መልካም፡ ነገር፡ ይሰጠዋል። ማቴ፡ ፲፭፡ ፲፱። ያዕ፡ ፩፡ ፲፯።

፲፪፤ ሰዎችም፡ ሊያደርጉላችሁ፡ የምትወዱትን፡ ሁሉ፡ እንደሁ፡ ደግሞ፡ እላንትም፡አድርጉላቸው፡ ኦሪትም፡ ነቢያትም፡ ይህ፡ ነውና። ም፡ ፳፪፡ ፵።
ሮሜ፡ ፲፫፡ ፰፡ ፲።

፲፫፤ በጨነቀቸው፡ ደጅ፡ ግቡ። ደጂ፡ የሰፋ፡ ነውና፡ መንገዱም፡የተዘረጋ፡ ነው፡ ወደ፡ጥፋት፡የሚወስድ፡ ወደርሱም፡የሚገቡ፡ብዙ፡ናቸው። ሉቃ፡ ፩፡ ፫፡ ፳፬።

፲፬፤ ደጂቱም፡ የጨነቀች፡ናት፡ መንገድም፡የፀበበች፡ ወደ፡ሕይወት፡ የምትመራ፡ ጥቂትም፡ ናቸው፡ የሚያገኙዋት። ማቴ፡ ፲፱፡ ፳፬። የሐዋ፡ ፲፬፡ ፳፪።

፲፭፤ ተጠንቀቁ፡ ካሰተኞች፡ ነቢያት። የበግ፡ ለምድ፡ ለብሰው፡ የሚመጡባችሁ። በውስጣቸው፡ግን፡ ነጣቆች፡ ጅቦች፡ ናቸው። ም፡ ፳፬፡ ፬፡ ፭፡ ፳፬።
የሐዋ፡ ፳፡ ፳፱።

፲፮፤ *ከፍሬያቸው፡ ታውቁዋቸዋላችሁ። ከሾህ፡ ወይን፡ ይለቀማልን፡ከአሜከላስ፡ በለስ።
*ገላት፡ ፭፡ ፲፱፡—፳፩። ያዕ፡ ፫፡ ፲፪።

፲፯፤ እንደሁ፡ መልካም፡ዛፍ፡ ሁሉ፡ መልካም፡ ፍሬ፡ ታፈራለች። ክፉም፡ ዛፍ፡ ክፉ፡ ፍሬ፡ ታፈራለች።
ም፡ ፲፪፡ ፴፫።

፲፰፤ መልካም፡ ዛፍ፡ ክፉ፡ ፍሬ፡ ማፍራት፡ አይቻ

ላትም። ከፉም፡ዛፍ፡መልካም፡ፍሬ፡ማፍራት፡አይቻላትም።

፲፱፥ ዛፍ፡ ሁሉ፡ መልካም፡ ፍሬ፡የማታፈራ፡ ትቈረጣለች፡ ወደ፡ እሳትም፡ ትጣመራለች። ም፡ ፫፥ ፲።
ዮሐ፡ ፲፭፥ ፪፥ ፮።

፳፥ ስለዚህም፡ ከፍሬያቸው፡ ታውቋቸዋላችሁ።

፳፩ አቤቱ፡ አቤቱ፡ የሚለኝ፡ *ሁሉ፡ መንግሥተ፡ ሰማያት፡ የሚገባ፡ አይደለም። በሰማይ፡ ያለውን፡ ያባቴን፡ ፈቃድ፡የሚያደርግ፡ እንጂ። *ሮሜ፡ ፪፥ ፲፫።
ያዕ፡ ፩፥ ፳፪፥ ፳፭።

፳፪፥ በዚያች፡ ቀን፡ብዙ፡ይሉኛል። አቤቱ፡ አቤቱ፡ በስምህ፡ ትንቢት፡ የተናገርን፡ አይደለምን። በስምህስ፡ አጋንንት፡ ያወጣን፡ አይደለምንምን። በስምህስ፡ ብዙ፡ ኃይል፡ አላደረግንምን።
ሉቃ፡ ፲፫፥ ፳፭—፳፯። ፩፥ ቆሮ፡ ፲፫፥ ፩፥ ፪።

፳፫፥ በዚያን፡ ጊዜም፡ በእውነት፡ እላቸዋለሁ። ከቶ፡ አላውቃችሁም። ከኔ፡ ራቁ፡ እላንት፡ ኃጢአት፡ የምትሰሩ። ም፡ ፳፭፥ ፵፩። ፪፡ጢሞ፡ ፪፥ ፲፱።

፳፬፥ ስለዚህም፡ ይህነን፡ ነገሬን፡ የሚሰማ፡ ሁሉ፡ የሚያደርገውም፡ጠቢብ፡ ሰው፡ ይመስላል፡ ቤቱን፡ በደንጊያ፡ ላይ፡ የሰራ። ቈ፡ ፳፩። ዮሐ፡ ፲፫፥ ፲፯።

፳፭፥ ዝናምም፡ ዘነበ፡ ጐርፍም፡ ጐረፈ፡ ነፋስም፡ ነፈሰ፡ ያነንም፡ቤት፡ መቱት። አልወደቀምም፡ በደንጊያ፡ላይ፡ ተመሥርትዋልና።

፳፮፥ ይህነንም፡ ነገሬን፡ ሰምቶ፡ የማያደርገው፡ ሰው፡ ሰነፍ፡ ሰው፡ ይመስላል፡ ቤቱን፡ ባሸዋ፡ ላይ፡ የሰራ። ም፡ ፲፯፥ ፲፰።

፳፯፥ ዝናምም፡ ዘነበ፡ ጐርፍም፡ ጐረፈ፡ ነፋስም፡ ነፈሰ፡ ያነንም፡ቤት፡መቱት፡ወደቀም፡አወዳደቁም፡ ታላቅ፡ ሆነ። ሕዝ፡ ፲፫፥ ፲፥ ፲፩።

፳፰፥ የሱስም፡ ይህነን፡ ነገር፡ በፈጸመ፡ጊዜ፡ የተሰበሰቡት፡ ከትምህርቱ፡ አደነቁ። ማር፡ ፩፥ ፳፪።
ሉቃ፡ ፬፥ ፴፪።

፳፱፥ ሥልጣን፡ እንዳለው፡ ያስተምራቸው፡ ነበርና፡ እንደ፡ ጻፎቻቸው፡ አይደለም። ዮሐ፡ ፯፥ ፵፮።
ኢሳ፡ ፶፥ ፬፥ ፭።

## ምዕራፍ፡ ፰፥

፩፥ ከተራራም፡በወረደ፡ጊዜ፡ ብዙ፡ አሕዛብ፡ ተከተሉት። ማር፡ ፩፥ ፵—፵፬። ሉቃ፡ ፭፥ ፲፪—፲፬።

፪፥ እነሆ፡ለምጻምም፡ መጣ፡ሰገደለትም፡ እንደሀ፡ ሲል። አቤቱ፡ ብትወድስ፡ እኔን፡ ማንጻት፡ ይቻልሃል።

፫፥ የሱስም፡ እጁን፡ ዘረጋ፡ ዳሰሰውም፡ እንደሀ፡ ሲል፡ ወድጀለሁ፡ንጻ። በዚያም፡ ጊዜ፡ ከለምጹ፡ነጻ።

፬፥ የሱስም፡ አለው። ተጠንቀቅ፡ለማንም፡ *አትናገር። ነገር፡ግን፡ሒድ፡ ራስህን፡ለካህን፡ አሳይ፡ †ሙሴም፡ ያዘዘውን፡ ቍርባኑን፡ አቅርብ፡ ምስክር፡ ይሆንባቸው፡ ዘንድ። *ም፡ ፱፥ ፴። ማር፡ ፯፥ ፴፮።
†ዘሌዋ፡ ፲፬፥ ፪።

፭፥ የሱስም፡ ወደ፡ ቅፍርናሆም፡ በገባ፡ ጊዜ፡ የመቶ፡ አለቃ፡ ወደርሱ፡ መጣ፡ ከርሱ፡ ሸተ።
ሉቃ፡ ፯፥ ፩—፲።

፮፥ ብሎም፡ አቤቱ፡ ብላቴናዬ፡ በቤት፡ ወድቋል፡ በጽኑ፡ ሥቃይ፡ ድውይ፡ ሆኖ።

፯፥ የሱስም፡ አለው። እኔ፡ መጥቼ፡ እፈውሰዋለሁ።

፰፥ የመቶ፡ አለቃም፡መልሶ፡ አለው። አቤቱ፡አይገባኝም፡ ወደ፡ ቤቴ፡ ጣራ፡ልትገባ። ነገር፡ ግን፡አንዲት፡ ነገር፡ ብቻ፡ በል፡ ብላቴናዬም፡ ይድናል።

፱፥ እኔም፡ ደግሞ፡ የምገዛ፡ ሰው፡ ነኝና፡ ከጁም፡ በታች፡ ጭፍራ፡ አለኝ። ይህነንም፡ ሒድ፡ እለዋለሁ፡ ይሔድማል፡ ሌላውንም፡ ና፡ እለዋለሁ፡ ይመጣማል። ባርያዬንም፡ ይህነ፡ አድርግ፡ ብለው፡ ያደርጋል።

፲፥ የሱስም፡ በሰማ፡ ጊዜ፡ ተደነቀ፡ ለሚከተሉትም፡ አለ። እውነት፡ እነግራችኋለሁ፡ በእሥራኤል፡ በንኳ፡ ይህነን፡ የሚያህል፡ ሃይማኖት፡ እንዳላገኘሁ።
ም፡ ፲፭፥ ፳፰።

፲፩፥ እላችሁማለሁ።ብዙ፡ *ከምሥራቅ፡ከምዕራብም፡ ይመጣሉ፡ †ከአብርሃምም፡ ከይስሐቅም፡ ከያዕቆብም፡ጋራ፡ ይረፈቃሉ፡ በመንግሥተ፡ሰማያት።
*ኢሳ፡ ፵፱፥ ፲፪። †ሉቃ፡ ፲፫፥ ፳፰፥ ፳፱።

፲፪፥ የመንግሥት፡ ልጆች፡ ግን፡ ወደ፡ ሜዳዊ፡ *ጨለማ፡ ይጣላሉ። ከዚያም፡ ልቅሶ፡ ጥርስም፡ መፋጨት፡ ይሆናል። *ም፡ ፳፪፥ ፲፫። ፳፬፥ ፶፩። ፳፭፥ ፴።

፲፫፥የሱስም፡ለመቶ፡አለቃ፡አለው።*ሒድ፡እንደ፡ሃይማኖትህም፡ይሁንልህ። ብላቴናውም፡ዳነ፡በዚያች፡ ሰዓት። *ም፡ ፱፥ ፳፱። ፲፭፥ ፳፰።

፲፬፥ የሱስም፡ ወደ፡ ጴጥሮስ፡ ቤት፡ በመጣ፡ ጊዜ፡ የምሽቱ፡ እናት፡በመንሾ፡ ወድቃ፡ አየ።
ማር፡ ፩፥ ፳፱፥ ፴፬። ሉቃ፡ ፬፥ ፴፰—፵፩።

፲፭፥ እጅዋንም፡ ዳሰሰ፡ መንሾዱቱም፡ ተወቻት። ቆመችም፡ ታገለግላቸውም፡ ነበረች።

፲፮፥ በመሸም፡ ጊዜ፡ ሰይጣን፡ ያለባቸውን፡ ብዙ፡ አመጡለት፡ በቃሉም፡ መናፍስቱን፡ ያወጣ፡ነበረ፡ በክፉም፡ ደዌ፡ የነበሩትን፡ ሁሉ፡ አዳነ።

፲፯፥ ይፈጸም፡ ዘንድ፡ *በኢሳይያስ፡ በነቢዩ፡ የተባለው፡ እንዲህ፡ ሲል። እርሱ፡ ድካማችነን፡ ወሰደ፡ ደዌያችነንም፡ ተሸከመ። *ኢሳ፡ ፶፫፥ ፬፥ ፭።

፲፰፥ የሱስም፡ ብዙ፡ የተሰበሰቡ፡ በዙርያው፡ባየ፡ ጊዜ፡ ወደ፡ ማዶ፡ ይሔዱ፡ ዘንድ፡ አዘዘ።
ማር፡ ፩፥ ፴፭።

፲፱፥ አንድ፡ ጻፊም፡ ወደርሱ፡ መጣ፡ አለውም። መምህር፡ ሆይ፡ ልከተልህ፡ ወደምትሔደው፡ ሁሉ።
*ሉቃ፡ ፱፥ ፶፯—፷።

፳፥ የሱስም፡ አለው፡ ለቀበሮች፡ ጕድጓድ፡ አላቸው፡ ለሰማይም፡ ወፎች፡ ማረፊያ። *የሰው፡ ልጅ፡ ግን፡ ራሱን፡ የሚያስጠጋበት፡ የለውም።
*፪፥ ቆሮ፡ ፰፥ ፱።

፳፩፡ ከደቀ፡ መዛሙርቱም፡ አንዱ፡ አለው። አቤቱ፡ አዘዘኝ፡ አስቀድሜ፡ ልሒድ፡ አባቴንም፡ ልቅበረው። ፩፡ ነገሥ፡ ፲፱፡ ፳።

፳፪፡ የሱስም፡ አለው። ተከተለኝ፡ ሙታንንም፡ ተዋቸው፡ ሙታኖቻቸውን፡ ይቅበሩ። ፩፡ ጢሞ፡ ፭፡ ፮።

፳፫፡ ወደ፡ ታንኳም፡ በወጣ፡ ጊዜ፡ ደቀ፡ መዛሙርቱ፡ ተከተሉት።

፳፬፡ እነሆም፡ ታላቅ፡ መናወጥ፡ በባሕር፡ ሆነ፡ በመውጂ፡ ታንኳው፡ እስኪደፈን፡ ድረስ። እርሱ፡ ግን፡ ተኝቶ፡ ነበረ። ማር፡ ፬፡ ፴፯። ዮና፡ ፩፡ ፬።

፳፭፡ ደቀ፡ መዛሙርትም፡ ወደርሱ፡ ቀረቡ፡ አስነሡትም፡ እንዲህ፡ ሲሉ። አቤቱ፡ አድነን፡ ልናልቅ፡ ነውና። ም፡ ፲፬፡ ፴፡

፳፮፡ አላቸውም። ምነው፡ ትፈራላችሁ፡ እላንተ፡ ሃይማኖታችሁ፡ *የጐደለ። የዚያን፡ ጊዜ፡ ተነሣ፡ ነፋሶችንና፡ ባሕሩንም፡ ገሠፀ። *ም፡ ፲፯፡ ፳።

፳፯፡ ታላቅ፡ ጸጥታም፡ ሆነ። ሰዎቹ፡ ግን፡ አደነቁ፡ እንዲህ፡ ሲሉ፡ ይህ፡ ማነው። ነፋሶች፡ ደግሞ፡ ባሕርም፡ ይታዘዙታልና። መዝ፡ ፹፱፡ ፱። ፻፯፡ ፳፱፡— ፴።
ም፡ ፴፡ ፱።

፳፰፡ ወደ፡ ማዶም፡ ወደ፡ ጌርጌሴኖች፡ አገር፡ በመጣ፡ ጊዜ፡ ሁለት፡ እብዶች፡ ከመቃብር፡ ወጥተው፡ ተቀበሉት፡ እጅግም፡ ክፉ፡ ነበሩ፡ አንድ፡ ሰው፡ በዚያች፡ መንገድ፡ ማለፍ፡ እስኪሳነው፡ ድረስ።
ማር፡ ፭፡ ፩፡— ፲፯።

፳፱፡ እነሆም፡ እንዲህ፡ ሲሉ፡ ጮሁ። ባንተና፡ በኛ፡ ምን፡ ነገር፡ አለ፡ የሱስ፡ ሆይ፡ የእግዚአብሔር፡ *ልጅ። ከዚህ፡ መጣኽን፡ መከራ፡ ልታመጣብን፡ †ጊዜው፡ ሳይደርስ። *ሉቃ፡ ፬፡ ፵፩። †፪፡ ጴጥ፡ ፪፡ ፬።

፴፡ ከርሳቸው፡ ርቃ፡ ግን፡ የብዙ፡ እርያ፡ መንጋ፡ ትሰማራ፡ ነበረች፡ ሰይጣኖችም፡ እንዲህ፡ ሲሉ፡ ከርሱ፡ ለመኑ። ዘሌዋ፡ ፲፩፡ ፯።

፴፩፡ ታወጣነስ፡ እንደ፡ ሆንህ፡ እዘዘን፡ ወደ፡ እርያው፡ መንጋ፡ እንግባ። ማር፡ ፭፡ ፱፡ ፲፡

፴፪፡ አላቸውም፡ ሒዱ። እርሳቸውም፡ ወጥተው፡ ወደ፡ እርያው፡ መንጋ፡ ሔዱ። እነሆም፡ የርያው፡ መንጋ፡ ሁሉ፡ ከገደል፡ አፋፍ፡ ወደ፡ ባሕር፡ ወደቀ፡ በውኃም፡ ሞተ።

፴፫፡ እረኞች፡ ግን፡ ሸሹ፡ ወደ፡ አገርም፡ ሔዱ፡ በነገሩም፡ ሁሉ፡ አወሩ፡ በብዶችም።

፴፬፡ እነሆም፡ አገር፡ ሁሉ፡ ወጣ፡ የሱስን፡ ለመቀበል። ባዩትም፡ ጊዜ፡ ካገራቸው፡ እንዲነሣ፡ ለመኑት። ኢዮብ፡ ፳፩፡ ፲፬። የሐዋ፡ ፲፮፡ ፴፱።

ምዕራፍ፡ ፱፡

፩፡ ወደ፡ ታንኳም፡ በወጣ፡ ጊዜ፡ ወደ፡ ማዶ፡ ተሻገረ፡ *ወደገሩም፡ መጣ። *ማቴ፡ ፬፡ ፲፫።
ማር፡ ፪፡ ፩፡— ፲፪። ሉቃ፡ ፭፡ ፲፯፡— ፳፮።

፪፡ እነሆም፡ ድውይ፡ አመጡለት፡ *ባልጋ፡ የወደቀ። የሱስም፡ †ሃይማኖታቸውን፡ ባየ፡ ጊዜ፡ ድውዩን፡ አለው፡ እመን፡ ልጂ፡ ሆይ። ኃጢአትህ፡ ቀረችልህ። *የሐዋ፡ ፱፡ ፴፫። †ሉቃ፡ ፯፡ ፬።

፫፡ እነሆም፡ ከጸፎች፡ ወገን፡ በልባቸው፡ አሉ፡ ይህ፡ ይሰድባል። ማር፡ ፪፡ ፯።

፬፡ የሱስም፡ አሳባቸውን፡ አይቶ፡ አለ። ለምን፡ እላንተ፡ በልባችሁ፡ ክፉ፡ ታስባላችሁ። ም፡ ፲፪፡ ፳፭።
ዮሐ፡ ፪፡ ፳፭።

፭፡ ማናቸው፡ ይቀልላል፡ ኃጢአትህ፡ ቀረችልህ፡ ማለት፡ ወይስ፡ ተነሣ፡ ሒድም።

፮፡ ነገር፡ ግን፡ ታውቁ፡ ዘንድ፡ ለሰው፡ ልጅ፡ ሥልጣን፡ እንደለው፡ ኃጢአት፡ ይቅር፡ ይል፡ ዘንድ፡ በምድር፡ ላይ። የዚያን፡ ጊዜ፡ ድውዮን፡ አለው። ተነሣ፡ አልጋህን፡ ተሸከም፡ ወደ፡ ቤትህም፡ ሒድ።

፯፡ ተነሥቶም፡ ወደ፡ ቤቱ፡ ሔደ።

፰፡ የተሰበሰቡትም፡ አይተው፡ አደነቁ፡ እግዚአብሔርንም፡ አመሰገኑ፡ እንዲህ፡ ያለ፡ ሥልጣን፡ ለሰው፡ የሰጠ።

፱፡ የሱስም፡ ከዚያ፡ ባለፈ፡ ጊዜ፡ በቀረጥ፡ የተቀመጠውን፡ ሰው፡ አየ፡ ስሙን፡ ማቴዎስ፡ የሚሉት። አለውም፡ ተከተለኝ። ተነሥቶም፡ ተከተለው።
ማር፡ ፪፡ ፲፫፡— ፲፯። ሉቃ፡ ፭፡ ፳፯፡— ፴፪።

፲፡ በቤቱም፡ ለምሳ፡ ተቀምጦ፡ ሳለ፡ ብዙ፡ ቀራጮች፡ ኃጢአተኞችም፡ መጡ፡ ለምሳም፡ ተቀመጡ፡ ከየሱስ፡ ጋራ፡ ከደቀ፡ መዛሙርቱም።

፲፩፡ ፈሪሳውያንም፡ አይተው፡ ደቀ፡ መዛሙርቱን፡ አሉዋቸው፡ ለምን፡ መምህራችሁ፡ ከቀራጮች፡ ከኃጢአተኞችም፡ ጋራ፡ ይበላል። ሉቃ፡ ፲፭፡ ፪።
፩፡ ቆሮ፡ ፭፡ ፲፩።

፲፪፡ የሱስም፡ በሰማ፡ ጊዜ፡ አላቸው። ባለ፡ ጤኖች፡ ባለ፡ መድኃኒት፡ አይሹም፡ ድውዮች፡ እንጂ።

፲፫፡ ሒዱ፡ ግን፡ አውቁ፡ ይህ፡ ምንድር፡ ነው፡ *ምህረት፡ እወዳለሁ፡ መሥዋዕትም፡ አይደለም። ጻድቃን፡ ለመጽራት፡ †አልመጣሁምና፡ ኃጥአንን፡ እንጂ፡ ወደ፡ ንስሐ። *፩፡ ሳሙ፡ ፲፭፡ ፳፪። ሆሴ፡ ፮፡ ፮።
†ም፡ ፲፰፡ ፲፩።

፲፬፡ በዚያ፡ ጊዜ፡ የዮሐንስ፡ ደቀ፡ መዛሙርት፡ ወደርሱ፡ መጡ፡ እንዲህ፡ ሲሉ። ስለ፡ ምን፡ እኛ፡ *ፈሪሳውያንም፡ እጅግ፡ እንጾማለን፡ ደቀ፡ መዛሙርትህ፡ ግን፡ አይጾሙም። ማር፡ ፪፡ ፲፰፡— ፳፪።
ሉቃ፡ ፭፡ ፴፫፡— ፴፰። *ሉቃ፡ ፲፰፡ ፲፪።

፲፭፡ የሱስም፡ አላቸው። በውኑ፡ የሰርግ፡ ልጆች፡ ያለቅሱ፡ ዘንድ፡ ይችላሉን፡ ሙሽራ፡ ከርሳቸው፡ ጋራ፡ ሳለ። ነገር፡ ግን፡ ዘመን፡ ይመጣል፡ *ሙሽራው፡ ከርሳቸው፡ በተነሣ፡ ጊዜ። በዚያን፡ ጊዜ፡ ይጾማሉ።
*ዮሐ፡ ፫፡ ፳፱።

፲፮፡ ማንም፡ ያዲስ፡ ጨርቅ፡ ቍራጭ፡ ባረጀ፡ ልብስ፡ ላይ፡ አይጥፍም። ደጎናውን፡ ሁሉ፡ ትወስድዋለችና፡ መቀደዱም፡ ታላቅ፡ ይሆናል። ዮሐ፡ ፩፡ ፲፯።

፲፮፡ አዲሱንም፡ ፀጕ፡ ባረጀ፡ጋኖች፡አያስቀምጡም። ከዚያ፡የቀረስ፡ ጋኖች፡ ይሰነጠቃሉ፡ፀጁንም፡ ይፈሳል፡ ጋኖችም፡ ይጠፋሉ። ነገር፡ ግን፡ አዲሱን፡ ፀጁ፡ ባዲስ፡ ጋን፡ ያደርጉታል፡ አንድም፡ ሁነው፡ ይጠባበቃሉ።

፲፰፡ ይህነንም፡ ሲነግራቸው፡ እነሆ፡ መኰንን፡ መጣ፡ ሰገደለትም፡እንደዚህ፡ሲል። ልጂ፡አሁን፡ሞተች። ነገር፡ግን፡ ና፡ እጅህን፡ ጫንባትና፡ ትድን።

ማር፡ ፭፡ ፳፪፡—፵፫፡፡ ሉቃ፡ ፰፡ ፵፩—፶፮፡፡

፲፱፡ የሱስም፡ ተነሥቶ፡ ተከተለው፡ ከደቀ፡ መዛሙርቱም፡ ጋራ።

፳፡ እነሆም፡ ቤት፡ ደም፡ የሚፈሳት፡ ካሥራ፡ ሁለት፡ አመት፡ ጀምራ፡ በኋላው፡ መጣች፡ የልብሱንም፡ ጫፍ፡ ነካች።

፳፩፡ በልብዋ፡ ብላለችና፡ *ልብሱን፡ብቻ፡ብነካው፡ እድናለሁ። *ምዕ፡ ፲፬፡ ፴፮፡፡

፳፪፡ የሱስም፡ ተመልሶ፡ አያት፡ አላትም። አመኝ፡ ልጂ። ሃይማኖትሽ፡ አደነሽ። ሴቲቱም፡ ደነች፡ ከዚያች፡ ሰዓት።

፳፫፡ የሱስም፡ ወደ፡ መኰንኑ፡ ቤት፡በመጣ፡ጊዜ፡ ነፎችንና፡ ብዙውን፡ ሕዝብ፡ ሲፈጁ፡ ባየ፡ ጊዜ፡ አላቸው።

፳፬፡ ራቁ፡ ብላቴናዪቱ፡ አልሞተችም፡ ነገር፡ ግን፡ ትኝታለች። ከነገሩም፡ የተነሣ፡ ሳቁ። ዮሐ፡ ፲፩፡ ፲፩፡፡ ፲፬፡ ፳፭፡፡

፳፭፡ እርሳቸውም፡በወጡ፡ጊዜ፡ ገባ፡ እጅዋንም፡ ያዛት፡ ብላቴናዪቱም፡ ተነሣች።

፳፮፡ ወሬውም፡ ወጣ፡ በዚያች፡ አገር፡ ሁሉ።

፳፯፡ የሱስም፡ ከዚያ፡ ባለፈ፡ ጊዜ፡ ሁለት፡ ዕውሮች፡ተከተሉት፡ኢየጮሁ፡እንደዚህም፡ኢያሉ። ማረነ፡ የዳዊት፡ ልጅ።

፳፰፡ ወደ፡ቤትም፡ በመጣ፡ ጊዜ፡ ዕውሮቹ፡ ወደርሱ፡ መጡ። የሱስም፡ አላቸው። ይህን፡ ማድረግ፡ እንዲቻለኝ፡ ታምናላችሁን። እርሳቸውም፡ አሉት፡ አዎን፡ አቤቱ።

፳፱፡ የዚያን፡ ጊዜ፡ ዓይናቸውን፡ ደሰሰ፡ እንደዚህ፡ ሲል። እንደ፡ *ሃይማኖታችሁ፡ ይሁንላችሁ። ምዕ፡ ፰፡ ፲፫፡፡

፴፡ ዓይናቸውም፡ ተከፈተ፡ የሱስም፡ ገሠጸ፡ አላቸው፡ ተጠንቀቁ፡ ማንም፡ አይወቅ። ምዕ፡ ፰፡ ፬፡፡

፴፩፡ እርሳቸው፡ ግን፡በወጡ፡ጊዜ፡ ይህነን፡ አወሩ፡ በዚያች፡ አገር፡ ሁሉ።

፴፪፡ ከወጡም፡ በኋላ፡እነሆ፡ ድዳ፡ አመጡለት፡ ሰይጣን፡ ያደረበት።

፴፫፡ ሰይጣንም፡ በወጣ፡ ጊዜ፡ድዳው፡ ተናገረ። አሕዛብም፡ ተደነቁ፡ እንደዚህ፡ ሲሉ።እንደዚህ፡ያለ፡ በእሥራኤል፡ከቶ፡ አልታየም።

፴፬፡ ፈሪሳውያን፡ ግን፡ አሉ። በሰይጣኖች፡ አለቃ፡ ሰይጣኖችን፡ያወጣል። ምዕ፡ ፲፪፡ ፳፬፡፡

፴፭፡ የሱስም፡ ከተማውን፡ ሁሉ፡ መንደሩንም፡ *ይዞር፡ ነበረ፡የመንግሥትም፡ወንጌል፡ይሰብክ፡ነበር፡ በሕዝብም፡ ያለውን፡ ደዌን፡ ሁሉ፡ ድካምንም፡ ሁሉ፡ይፈውስ፡ነበረ። *ምዕ፡ ፬፡ ፳፫፡፡

፴፮፡ ብዙ፡ የተከማቹም፡ባየ፡ ጊዜ፡ *አዘነላቸው። ደክመው፡ ተቅበዝብዘውም፡ ነበሩና፡እንደ፡ ተበጎች፡ ጠባቂ፡እንደ፡ሌላቸው።* ምዕ፡ ፲፬፡ ፬፡፡ ማር፡ ፮፡ ፴፬፡፡ ትሕዝ፡ ፴፬፡ ፭፡፡

፴፯፡ ለደቀ፡ መዛሙርቱም፡አላቸው። መከሩ፡ እጅግ፡ ነው፡ ሰራተኞች፡ ግን፡ ጥቂት፡ ናቸው። ሉቃ፡ ፲፡ ፪፡፡ ዮሐ፡ ፬፡ ፴፭፡ ፴፮፡፡

፴፰፡ እንኪያስ፡ የመከሩን፡ ባለቤት፡ ለምኑት፡ ሰራተኞች፡ ለመከሩ፡ ያወጣ፡ ዘንድ።

ምዕራፍ፡ ፲፡

፩፡ አሥራ፡ ሁለቱንም፡ ደቀ፡ መዛሙርቱን፡ ወደርሱ፡ ጸራ፡ ሥልጣንም፡ ሰጣቸው፡በርኩሳን፡አጋንንት፡ ላይ። ያወጥዋቸው፡ ዘንድ፡ ደዌንም፡ ሕማምንም፡ ሁሉ፡ ይፈውሱ፡ ዘንድ። ማር፡ ፮፡ ፯፡—፲፫፡፡ ሉቃ፡ ፱፡ ፩፡—፭፡፡

፪፡ ያሥራ፡ ሁለቱም፡ ሐዋርያት፡ ሰማቸው፡ ይህ፡ ነው። መጀመርያው፡ ሲሞን፡ ጴጥሮስ፡ የተባለው። እንድርያስም፡ ወንድሙ። ያዕቆብ፡ የዘብዲዎስ፡ ልጅ፡ ዮሐንስም፡ ወንድሙ። ማር፡ ፫፡ ፲፬፡፡ ሉቃ፡ ፮፡ ፲፬፡፡ ዮሐ፡ ፩፡ ፵፡፡

፫፡ ፊልጶስ፡ በርተሎሚዎስም። ቶማስ፡ ማቴዎስም፡ አጣሪው። ያዕቆብ፡ የእልፍዮስ፡ ልጅ፡ ልቤዎስም፡ ታዲዎስ፡ የተባለው።

፬፡ ሲሞን፡ቀነናዊ፡ይሁዳም፡ያስቆሮቱ፡እርሱም፡ ደግሞ፡ ያስያዘው።

፭፡ እሌህን፡ አሥራ፡ ሁለቱን፡ ላካቸው፡ የሱስ፡ አዘዛቸውም፡ እንደዚህ፡ ብሎ። የአሕዛብን፡ መንገድ፡ አትሒዱ፡ ወደ፡ ሰማራውያንም፡ አገር፡ አትግቡ።

፮፡ ከዚያ፡ የሚበልጥ፡ወደ፡ ጠፉ፡ በጎች፡ ከእሥራኤል፡ ቤት፡ ሒዱ፡ እንጂ። ምዕ፡ ፲፭፡ ፳፬፡፡ የሐዋ፡ ፲፫፡ ፵፮፡፡

፯፡ በሔዳችሁም፡ ጊዜ፡ አስተምሩ፡ ኢያላችሁ። መንግሥተ፡ ሰማያት፡ ቀረበች። ምዕ፡ ፬፡ ፲፯፡፡

፰፡ድውያንን፡ፈውሱ። ለምጻሞችን፡አንጹ። ሙታንን፡ አንሡ። አጋንንትን፡ አውጡ። በከንቱ፡ወሰዳችሁ፡ በከንቱ፡ ሰጡ። የሐዋ፡ ፰፡ ፳፡፡

፱፡ ወርቅ፡ ብርም፡ ናስም፡ በመቀነታችሁ፡ አትያዙ።

፲፡ ከረጢት፡ ስንኳ፡ ለመንገድ፡ ሁለትም፡ ልብስ፡ ጫማም፡በትርም። *የሰራተኛ፡ ሙብሉ፡ ይገባዋልና፡ *፩፡ ጢሞ፡ ፭፡ ፲፰፡፡

፲፩፡ ወደ፡ ማናቸውም፡ ከተማ፡መንደርም፡ ብትገቡ፡ ጠይቁ፡ ማነው፡ የሚገባው፡ በርስዋ፡ ያለ። ከዚያም፡ተቀመጡ፡እስክትወጡ፡ድረስ።የሐዋ፡፲፫፡፵፯፡፡

፲፪፡ ወደ፡ *ቤትም፡በገባችሁ፡ጊዜ፡ሰላም፡ስጡት።
*ሉቃ፡ ፲፡ ፭፡ ፮፡፡
፲፫፡ ቤቱም፡ የሚገባው፡ ቢሆን፡ ሰላማችሁ፡ይደር
በት። ባይገባው፡ ግን፡ ሰላማችሁ፡ ይመለስላችሁ።
ኢሳ፡ ፶፪፡ ፯፡፡
፲፬፡ የማይቀበላችሁም፡ ነገራችሁንም፡ የማይሰ
ማ፡ ከዚያው፡ ቤት፡ ወይም፡ ከዚያች፡ ከተማ፡ ወጥ
ታችሁ፡ የግራችሁን፡ ትቢያ፡ *አርግፉ።  ሉቃ፡ ፲፡ ፲፩፡፡
የሐዋ፡ ፲፫፡ ፶፩፡፡
፲፭፡ በውነት፡ እላችኋለሁ፡ ለሶዶምና፡ ለገሞራ፡
ምድር፡ ዕረፍት፡ እንዲሆን፡ በፍርድ፡ ቀን፡ ከዚያች፡
ከተማ፡ ይልቅ።  ም፡ ፲፩፡ ፳፬፡፡ ሉቃ፡ ፰፡ ፵፫፡፡
ሕዝ፡ ፲፮፡ ፵፰፡—፶፫፡፡
፲፮፡ እነሆ፡ *እኔ፡ እሰዳችኋለሁ፡ እንደ፡ በጎች፡ በተ
ኩሎች፡ መካከል። እንግዲህ፡ ተጠቢባን፡ሁኑ፡እንደ፡
እባብ፡ የዋሃንም፡ እንደ፡ ርግብ።  *ሉቃ፡ ፲፡ ፫፡፡
ሮሜ፡ ፲፮፡ ፲፱፡፡ ኤፌ፡ ፭፡ ፲፭፡፡
፲፯፡ ከሰው፡ ግን፡ ተጠበቁ። ወደ፡ ሸንጎ፡ይወስዱዋ
ችኋልና፡ በመስጊዳቸውም፡ ይገርፉዋችኋል።
ማቴ፡ ፳፬፡ ፱፡፡ ማር፡ ፲፫፡ ፱፡—፲፫፡፡
ሉቃ፡ ፳፩፡ ፲፪፡—፲፱፡፡
፲፰፡ ወደለቆችም፡ ወደ፡ ነገሥታትም፡ ይወስዱዋ
ችኋል፡ ስለኔ። ለርሳቸው፡ *ምስክር፡ ይሆን፡ዘንድ፡ ለ
ሕዛብም።  ም፡ ፳፬፡ ፲፬፡፡ የሐዋ፡ ፳፭፡ ፳፫፡፡
፳፯፡ ፳፬፡፡
፲፱፡ አሳልፈውም፡ በሰጥዋችሁ፡ ጊዜ፡ አታስቡ፡ እ
ንዴት፡ ወይስ፡ ምን፡ እንድትሉ። በዚያች፡ ጊዜ፡ ይሰ
ጣችኋልና፡ የምትናገሩት።  ሉቃ፡ ፲፪፡ ፲፩፡፡
፳፡ እላንት፡ የምትናገሩ፡ አይደላችሁምና፡ ነገር፡
ግን፡ ያባታችሁ፡ መንፈስ፡ነው፡ የሚናገርባችሁ።
፩፡ ቆሮ፡ ፪፡ ፬፡፡
፳፩፡ ወንድምም፡ ወንድሙን፡ ለሞት፡ አሳልፎ፡
ይሰጣል፡አባትም፡ልጁን። ልጆችም፡በወላጆቻቸው፡
ላይ፡ይነሣሉ፡ ይገድልዋቸዋልም።  ቀ፡ ፸፭፡፡
፳፪፡ በሁሉም፡ ዘንድ፡ የተጸላችሁ፡ ትሆናላችሁ፡
ስለ፡ ስሜ። እስከ፡ ፍጻሜ፡ ግን፡ *የሚታገሥ፡ እርሱ፡
ይድናል።  *ም፡ ፳፬፡ ፲፫፡፡
፳፫፡ በዚች፡ አገር፡ ግን፡ ቢያሳድዋችሁ፡ ወደ፡ ሌላ
ይቱ፡ ሽሹ። በውነት፡ እላችኋለሁና፡ *የእሥራኤልን፡
አገር፡ እንዳትጨርሱ፡ የሰው፡ ልጅ፡ እስኪመጣ፡ ድ
ረስ።  ም፡ ፲፮፡ ፳፰፡፡ የሐዋ፡ ፲፬፡ ፳፡ ፳፩፡፡
፳፬፡ ደቀ፡ መዝሙር፡ ከመምህሩ፡ የሚበልጥ፡ አ
ይደለም፡ ባርያም፡ ከጌታው፡ አይበልጥም።
ሉቃ፡ ፮፡ ፵፡፡ ዮሐ፡ ፲፫፡ ፲፮፡፡ ፲፭፡ ፳፡፡
፳፭፡ ለደቀ፡ መዝሙር፡ ይበቃል፡ እንደ፡ መምህ
ሩ፡ ቢሆን፡ ለባርያም፡ እንደ፡ ጌታው፡ ቢሆን። *ባለ፡
ቤቱን፡ የሰይጣናት፡ አለቃ፡ ካሉት፡ የቤቱን፡ ሰዎቹን
ስ፡ እንዴት፡ ይሁን።  *ም፡ ፲፪፡ ፳፬፡፡ ዮሐ፡ ፰፡ ፵፰፡፡

፳፮፡ አትፍሩዋቸው። የተሰወረ፡ የለምና፡ ሳይገለ
ጥ፡ የሚቀር፡ የተሸሸገውም፡ ሳይታወቅ።
ሉቃ፡ ፲፪፡ ፪፡—፱፡፡
፳፯፡ በጨለማ፡የምነግራችሁን፡በብርሃን፡ንገሩት።
በጆሮዋችሁም፡ የሰማችሁትን፡ በሰገነት፡ ላይ፡ አስተ
ምሩ።  ማር፡ ፬፡ ፳፪፡፡ ሉቃ፡ ፰፡ ፲፯፡፡
፳፰፡ አትፍሩም፡ ሥጋን፡ ከሚገድሉ፡ ነፍስን፡ ግን፡
መግደል፡ አይቻላቸውም። ነገር፡ ግን፡ ነፍስንና፡ ሥጋ
ን፡በገሃነም፡ ማጥፋት፡ከሚችል፡ከርሱ፡እጅግ፡ፍሩ።
፳፱፡ ሁለት፡ድንቢጦች፡በናስ፡ይሸጡ፡የለምን። አ
ንዱም፡ከርሳቸው፡ ያለ፡ አባታችሁ፡ፈቃድ፡ በምድር፡
ላይ፡ አይወድቅም።
፴፡ እላንትም፡ የራስ፡ ጸጕራችሁ፡ ሁሉ፡ የተቈጠ
ረ፡ ነው።
፴፩፡ እንግዲህም፡ አትፍሩ። እላንት፡ከብዙ፡ድን
ቢጥ፡ ትሻላላችሁና።
፴፪፡ በኔም፡ የሚያምንብኝ፡ ሁሉ፡ በሰው፡ ፊት፡
እኔም፡ ደግሞ፡አምንበታለሁ፡ በሰማያት፡ ባለው፡ ባ
ባቴ፡ ፊት።  ሮሜ፡ ፲፡ ፱፡ ፲፡፡
፴፫፡ በሰው፡ፊትም፡የካደኝን፡እኔም፡ደግሞ፡በሰ
ማያት፡ ባለው፡ ባባቴ፡ ፊት፡ እክደዋለሁ።
ሉቃ፡ ፱፡ ፳፮፡፡ ፪፡ ጢሞ፡ ፪፡ ፲፪፡፡
፴፬፡ አይምሰላችሁ፡ የመጣሁ፡ ሰላም፡ ለማድረ
ግ፡ በምድር፡ ላይ። ሰላም፡ለማድረግ፡አልመጣሁም፡
ነገር፡ ግን፡ ሰይፍን፡ ለማምጣት።  ሉቃ፡ ፲፪፡ ፶፩፡ ፶፫፡፡
፴፭፡ መጥቻለሁና፡ ሰውን፡ ካባቱ፡ እለይ፡ዘንድ።
ልጂቱንም፡ ካናትዋ፡ ዋርሳዪቱንም፡ ካማችዋ።
፴፮፡ የሰውም፡ ጸላቶቹ፡ ቤተሰቡ፡ ይሆናሉ።
፴፯፡ አባቱን፡እናቱንም፡ ከኔ፡ ይልቅ፡የወደደ፡ለኔ፡
ሊሆን፡ አይገባውም። ወንድ፡ ልጁንም፡ ሴት፡ልጁን
ም፡ ከኔ፡ ይልቅ፡ የወደደ፡ ለኔ፡ ሊሆን፡ አይገባውም።
ዘዳግ፡ ፴፫፡ ፱፡፡ ሉቃ፡ ፲፬፡ ፳፮፡፡
፴፰፡ መስቀሉንም፡ ተሸክሞ፡ በኋላዬ፡ያልተከተ
ለኝ፡ እኔን፡ ለማገልገል፡ አይገባውም።
ም፡ ፲፮፡ ፳፬፡ ፳፭፡፡ ማር፡ ፰፡ ፴፬፡—፴፰፡፡
ዮሐ፡ ፲፪፡ ፳፭፡፡
፴፱፡ ነፍሱን፡ የሚያገኝ፡ ሁሉ፡ይጥላታል። ነፍሱን
ም፡ ስለኔ፡ የሚጥል፡ ሁሉ፡ ያገኛታል። ሉቃ፡ ፲፯፡ ፴፫፡፡
ዮሐ፡ ፲፪፡ ፳፭፡፡
፵፡ እላንትን፡ የሚቀበላችሁ፡ እኔን፡ ተቀበለኝ።
እኔንም፡ የሚቀበለኝ፡ የላከኝን፡ ተቀበለ።
ም፡ ፲፰፡ ፭፡፡ ሉቃ፡ ፲፡ ፲፮፡፡ ዮሐ፡ ፲፫፡ ፳፡፡
፵፩፡ ነቢዩን፡ የተቀበለ፡ በነቢይ፡ ስም፡ የነቢዩን፡ ዋ
ጋ፡ ይወስዳል። ጻድቁንም፡ የተቀበለ፡ በጻድቅ፡ ስም፡
የጻድቁን፡ ዋጋ፡ ይወስዳል።
፵፪፡ ከለዚህ፡ ከተናናሾችም፡ ላንዱ፡ የበረደ፡ ው
ኃ፡ ጽዋ፡ ብቻ፡ የሚያጠጣ፡ በደቀ፡ መዝሙር፡ ስም።
እውነት፡ እላችኋለሁ፡ ዋጋው፡ እንደይጠፋ።
ም፡ ፳፭፡ ፵፡፡

## ምዕራፍ፡ ፲፩፤

፩፤ የሱስም፡ ለአሥራ፡ ሁለቱ፡ ደቀ፡ መዛሙርቱ፡ ት
እዛዙን፡ በፈጸመ፡ ጊዜ፡ ከዚያ፡ አለፈ፡ሊያስተምር፡
ሊሰብክም፡ ባገራቸው። ሉቃ፡ ፯፤ ፲፰፤—፴፭፤፤
፪፤ ዮሐንስም፡ የክርስቶስን፡ ሥራ፡ በሰማ፡ ጊዜ፡ *በ
ግዞት፡ ሳለ፡ ከደቀ፡ መዛሙርቱ፡ ሁለት፡ ላከበት፡ አ
ለም። ም፡ ፲፬፤ ፫፤፤
፫፤ *አንተን፡ ነህ፡ የሚመጣው፡ ወይስ፡ ሌላውን፡
እንጠብቅ። *ማል፡ ፫፤ ፩፤፤ ዮሐ፡ ፩፤ ፴፬፤፤
፬፤ የሱስም፡መለሰላቸው፡እንዲህም፡ አላቸው።
ሒዱ፡ ለዮሐንስም፡ ንገሩት፡የሰማችሁትንና፡ ያያች
ሁትን።
፭፤ ዕውሮች፡ያያሉ፡ አንካሶችም፡ይሔዳሉ። ለም
ጻሞችም፡ ይነጻሉ፡ ደንቆሮቹም፡ ይሰማሉ። የሞቱ
ት፡ ይነሣሉ፡ ለችጋረኞችም፡ በወንጌል፡ ይሰበካል።
ኢሳ፡ ፴፭፤ ፭፤፤ ፷፩፤ ፩፤፤
፮፤ በኔም፡ የማይጠራጠር፡ምስጉን፡ ነው።
ም፡ ፲፫፤ ፶፯፤፤ ፳፯፤ ፴፩፤፤
፯፤ እለዚያም፡ከሔዱ፡ በኋላ፡ የሱስ፡ ለተሰበሰቡ
ት፡ ስለ፡ ዮሐንስ፡ ይል፡ ዘንድ፡ጀመረ። ምን፡ ታዩ፡ ዘን
ድ፡ ወደ፡ *ምድረ፡ በዳ፡ ወጣችሁ። ሸምበቆን፡ ነፋስ፡
የሚያንቀሳቅሰውን። *ም፡ ፫፤ ፩፤፤ ዮሐ፡ ፭፤ ፴፭፤፤
፰፤ ነገር፡ ግን፡ ምን፡ ወጣችሁ፡ ልታዩ። ሰውንን፡ ቀ
ጭን፡ ልብስ፡ የለበሰውን። እነሆ፡ቀጭን፡ልብስ፡ የለበ
ሱ፡ በነገሥታት፡ ቤት፡ ናቸው።
፱፤ ነገር፡ግን፡ ምን፡ ወጣችሁ፡ ልታዩ። *ነቢይን። አ
ዎን፡ እላችኋለሁ፡ ከነቢይም፡ የሚበልጠውን።
ሉቃ፡ ፩፤ ፸፮፤፤
፲፤ እርሱ፡ነውና፡ ስለርሱ፡ የተጻፈለት። እነሆ፡ መ
ልክተኛዬን፡ በፊትህ፡ እሰዳለሁ፡ መንገድህን፡ባንተ፡
ፊት፡ የሚጸርግ። መል፡ ፫፤ ፩፤፤
፲፩፤ እውነት፡ እላችኋለሁ። ከሴቶች፡ልጆች፡ ከመ
ጥምቁ፡ ከዮሐንስ፡ የሚበልጥ፡ የተነሣ፡ አንድ፡ሌላ።
በመንግሥተ፡ ሰማያት፡ ግን፡ የሚያንሰው፡ ይበልጠ
ዋል። ዘካ፡ ፲፪፤ ፰፤፤ ም፡ ፲፫፤ ፲፯፤፤
፲፪፤ ከመጥምቁም፡ ከዮሐንስ፡ *ዘመን፡ ጀምሮ፡
እስከ፡ ዛሬ፡ መንግሥተ፡ ሰማያት፡ በብርቱ፡ ትዘረጋ
ለች። *ሉቃ፡ ፲፮፤ ፲፮፤፤ ፲፫፤ ፳፬፤፤
፲፫፤ ብርቶችም፡ ይናጠቋታል። ነቢያት፡ሁሉ፡ኦሪት
ም፡ እስከ፡ ዮሐንስ፡ ተናገሩ።
፲፬፤ ትቀበሉት፡ዘንድም፡ ትሹ፡ እንደ፡ ሆነ፡ እርሱ፡
ኤልያስ፡ ነው፡ ይመጣ፡ ዘንድ፡ ያለው። መል፡ ፬፤ ፭፤፤
ማቴ፡ ፲፯፤ ፲፤—፲፫፤፤
፲፭፤ ሰሚ፡ ጆሮ፡ ያለው፡ ይስማ።
፲፮፤ ይህነንም፡ ትውልድ፡ ግን፡ በምን፡ እመስለዋ
ለሁ። ገቢያ፡ የተቀመጡን፡ ሕፃናትን፡ ይመስላል፡ ባ
ልንጀሮቻቸውን፡ የሚጸሩ።
፲፯፤ የሚሉም። አጨበጨብንላችሁ፡አልዘፈናችሁ
ምም። አስለቀስንላችሁ፡ አላለቀሳችሁምም።
ምሳ፡ ፳፱፤ ፱፤፤
፲፰፤ ዮሐንስ፡ መጥትዋልና። *አልበላም፡አልጠጣ
ም። አሉትም፡ ጋኔን፡ አለበት። *ም፡ ፫፤ ፬፤፤
፲፱፤ የሰው፡ ልጅ፡ መጣ፡ይበላል፡ይጠጣል። አሉት
ም፡ እነሆ፡ የሚበላ፡ ጸጂም፡ የሚጠጣ፡ ሰው። ያጣ
ሮች፡ የኃጢአተኞችም፡ ወዳጅ፡ ነው። ጥበብም፡ ከል
ጆችዋ፡ ትጸድቃለች። *ም፡ ፱፤ ፲፬፤፤ ሉቃ፡ ፲፩፤ ፵፱፤፤
፳፤ ከዚህም፡ በኋላ፡ የሱስ፡ አገሮችን፡ ይነቅፍ፡ ጀ
መረ፡ ከሁሉ፡ የሚበዛ፡ኃይል፡ያደረገባቸውን፡ንስሐ፡
አልገቡምና። ሉቃ፡ ፲፤ ፲፫፤—፲፭፤፤
፳፩፤ ወዮልሽ፡ኮራዚን፡ሆይ። ወዮልሽ፡ ቤተ፡ ሰይ
ደ፡ ሆይ። በላንት፡የተደረገው፡ኃይል፡ በጢሮስና፡በሲ
ደን፡ ከተደረገ፡ አስቀድመው፡ *ንስሐ፡ በገቡ፡ ማቅ፡
ለብሰው፡ አመድም፡ ነስንሰው። *ዮና፡ ፫፤ ፮፤፤
ሉቃ፡ ፲፤ ፲፫፤፤
፳፪፤ ነገር፡ ግን፡ እላችኋለሁ። በፍርድ፡ቀን፡ ለጢሮ
ስና፡ለሲደና፡ ዕረፍት፡ እንዲሆን፡ከላንት፡ ይልቅ።
፳፫፤ አንችም፡ *ቅፍርናሆም፡ ሆይ፡እስከ፡ሰማይ፡
ከፍ፡ የምትዪ፡ ወደ፡ ሲኦል፡ ትወርጂለሽ። ባንች፡ የ
ሆኑ፡ ኃይል፡ †በሶደም፡ በሆኑ፡ እስከ፡ ዛሬ፡ በኖረች።
*ም፡ ፬፤ ፲፫፤፤ †ኢሳ፡ ፲፬፤ ፲፪፤ ፲፭፤፤ ሕዝ፡ ፲፮፤ ፵፰፤፤
፳፬፤ ነገር፡ ግን፡ እልሻለሁ። የሶደም፡ምድር፡ ዕረፍ
ት፡ እንድታገኝ፡ በፍርድ፡ቀን፡ ካንች፡ የሚበልጥ።
ም፡ ፲፤ ፲፭፤፤
፳፭፤ በዚያን፡ ጊዜ፡ መለሰ፡የሱስ፡ አለም። እገዛል
ሃለሁ፡ አባት፡ ሆይ፡የሰማይና፡ የምድር፡ ጌታ። ይህች
ን፡ ከብልሀተኞች፡ ካዋቂችም፡ ሰውርሃልና፡ ለሕፃና
ትም፡ ገለጥሃት። ሉቃ፡ ፲፤ ፳፩፤ ፳፪፤፤
፳፮፤ አዎን፡ አባት፡ ሆይ፡ እንደህ፡ ፈቃድህ፡ ነበረ
ችና፡ በፊትህ።
፳፯፤ ሁሉ፡ *ተሰጠኝ፡ ከባቴ፡ ዘንድ። አንድም፡ ል
ጅን፡ አያውቀውም፡ ከአብ፡ በቀር። አብንም፡ ማን
ም፡ አያውቀውም፡ ከልጅ፡ በቀር፡ ልጅም፡ ይገልጽለ
ት፡ዘንድ፡ከሚሻው። *ም፡ ፳፰፤ ፲፰፤፤ ዮሐ፡ ፫፤ ፴፭፤፤
ፊል፡ ፪፤ ፱፤፤
፳፰፤ ወደኔ፡ ኑ፡ እላንት፡ ደካሞች፡ ሁሉ፡ ሸክማች
ሁም፡ *የከበደ፡እኔም፡አሳርፋችኋለሁ።
*ም፡ ፲፪፤ ፰፤፤ ኢሳ፡ ፵፭፤ ፳፪፤፤ ኤር፡ ፴፩፤ ፳፭፤፤
፳፱፤ ቀምበሬን፡ በላያችሁ፡ ተሸከሙ፡ ከኔም፡ ተ
ማሩ። እኔ፡ የዋህ፡ነኝና፡ልቤም፡ትሑት፡ ነውና። *ዕረ
ፍትም፡ ለነፍሳችሁ፡ታገኛላችሁ። *ኤር፡ ፮፤ ፲፮፤፤
፴፤ ቀምበሬ፡ መልካም፡ነውና፡ ሸክሜም፡ቀሊል፡
ነውና። ፩፤ ዮሐ፡ ፭፤ ፫፤፤

## ምዕራፍ፡ ፲፪፤

፩፤ በዚያ፡ ዘመን፡የሱስ፡ በቅዳሜ፡ ቀን፡ በርሻ፡ መ
ካከል፡ አለፈ፡ ደቀ፡ መዛሙርቱም፡ ተራቡ፡ እሸት

ም፡ ኢያኙ፡ ይበሉ፡ ጀመሩ። ማር፡ ፪፡ ፳፫፡—፳፰።
ሉቃ፡ ፮፡ ፩፡—፭።
፪፡ ፈሪሳውያንም፡ ባዩዋቸው፡ ጊዜ፡ አሉት። እነ
ሆ፡ ደቀ፡ መዛሙርትህ፡ ያደርጋሉ፡ ማድረጉ፡ የማይገ
ባውን፡ በቅዳሜ። ዘፀአ፡ ፳፡ ፲።
፫፡ እርሱም፡ አላቸው። አላነበባችሁምን፡ *ዳዊት፡
ያደረገውን፡ እርሱ፡ በተራበ፡ ጊዜ፡ ከርሱም፡ ጋራ፡ የነ
በሩ። *፩፡ ሳሙኤ፡ ፳፩፡ ፮።
፬፡ ወደ፡ ቤተ፡ እግዚአብሔር፡ እንደ፡ ገባ፡ የመሥ
ዋዕት፡ እንጀራም፡ እንደ፡ በላ። መብሉ፡ የማይገባው
ን፡ ለርሱ፡ ከርሱ፡ ጋራም፡ ላሉ፡ ለካህናት፡ *ብቻ፡ እ
ንጂ። *ዘሌዋ፡ ፳፬፡ ፱።
፭፡ በኦሪትስ፡ ያለውን፡ አላነበባችሁም፡ ካህናት፡
ቅዳሜ፡ በመቅደስ፡ ቅዳሜን፡ እንዲያረክሱ፡ ኃጢአ
ትም፡ የለባቸውም። ዘኊል፡ ፳፰፡ ፱።
፮፡ እኔም፡ እላችኋለሁ። ከመቅደስ፡ የሚበልጥ፡
ከዚህ፡ አለ።
፯፡ ብታውቁስ፡ ምን፡ እንደ፡ ሆነ። *ምሕረት፡ እወ
ዳለሁ፡ መሥዋዕትም፡ አይደለም፡ ኃጢአት፡ በሌላቸ
ው፡ ላይ፡ ባልፈረዳችሁም። *ም፡ ፱፡ ፲፫።
፩፡ ሳሙኤ፡ ፲፭፡ ፳፪።
፰፡ የቅዳሜው፡ ጌታ፡ ደግሞ፡ የሰው፡ ልጅ፡ ነውና።
ማር፡ ፪፡ ፳፰።
፱፡ የሱስም፡ ከዚያ፡ ባለፈ፡ ጊዜ፡ ወደ፡ መስጊዳቸ
ው፡ መጣ። ማር፡ ፫፡ ፩፡—፮። ሉቃ፡ ፮፡ ፮፡—፲፩።
፲፡ እነሆም፡ እጁ፡ የሰለለች፡ ሰው፡ ነበረ። ጠየቁት
ም፡ እንዲህ፡ ሲሉ። በቅዳሜ፡ ቀን፡ ይፈወስ፡ ዘንድ፡
ይገባልን። ያጸሉት፡ ዘንድ። ሉቃ፡ ፲፬፡ ፫።
፲፩፡ እርሱም፡ አላቸው። ማን፡ ሰው፡ ከእላንት፡
ነው፡ አንድ፡ በግ፡ ያለው፡ ወደ፡ ገደል፡ ቢወድቅ፡ የማ
ይዘው፡ የማያስነሣውስ፡ በቅዳሜ፡ ቀን።
፲፪፡ ሰውም፡ እንደ፡ ምን፡ ከበግ፡ ይልቅ፡ ይሻል። እ
ንኪያስ፡ በቅዳሜ፡ መልካም፡ መሰራት፡ ይገባል።
ሉቃ፡ ፲፬፡ ፭።
፲፫፡ የዚያን፡ ጊዜ፡ ያነን፡ ሰው፡ አለው፡ እጅህን፡ዘር
ጋ። ዘረጋትም፡ ደነች፡ እንደ፡ ሁለተኛዪቱም፡ ደኅና፡
ሁና፡ ቀረች።
፲፬፡ ፈሪሳውያን፡ ግን፡ በወጡ፡ ጊዜ፡ ሊያጠፉት፡ ተ
ማከሩ። ዮሐ፡ ፭፡ ፲፮።
፲፭፡ የሱስም፡ አውቀ፡ ከዚያ፡ ወጥቶ፡ ሔደ። ብዙ
ም፡ አሕዛብ፡ ተከተሉት፡ ሁላቸውንም፡ ፈወሳቸው።
፲፮፡ ገሥጸም፡ አዘዛቸው፡ እንዲይገልጡት።
ማር፡ ፫፡ ፯፡—፲፪። ም፡ ፰፡ ፬።
፲፯፡ ይፈጸም፡ ዘንድ፡ *በኢሳይያስ፡ በነቢዩ፡ የተባ
ለው፡ እንዲህ፡ ሲል። *ኢሳ፡ ፵፪፡ ፩፡—፬።
፲፰፡ እነሆ፡ ብላቴናዬ፡ የመረጽሁት። *ወዳጄ፡ ነፍ
ሴ፡ የወደደችው። መንፈሴን፡ በርሱ፡ አኖራለሁ፡ ፍር
ድንም፡ የአሕዛብ፡ ይነግራል። *ም፡ ፫፡ ፲፯፡
፲፱፡ አይከራከርም፡ አይጮህም፡ ድምፁንም፡ ባደ
ባባይ፡ አንድ፡ የሚሰማው፡ የለም።
፳፡ የተቀጠቀጠ፡ ሸምበቆ፡ አይሰብርም፡ የሚጤ
ሰንም፡ የተልባ፡ እግር፡ አያጠፋም። ፍርድን፡ በማሸ
ነፍ፡ እስኪያወጣ፡ ድረስ።
፳፩፡ በስሙም፡ አሕዛብ፡ ይታመናሉ።
፳፪፡ *በዚያን፡ ጊዜ፡ ዕውር፡ መጣበት፡ ድዳ፡ በርሱ
ም፡ ሰይጣን፡ ነበረበት። ፈወሰውም፡ ዕውሩ፡ ድዳው፡
እስኪናገር፡ እስኪያይም፡ ድረስ።
*ማር፡ ፫፡ ፳፪፡—፴። ሉቃ፡ ፲፩፡ ፲፬፡—፴፪።
፳፫፡ አሕዛብም፡ ሁሉ፡ ይደነቁ፡ እንዲህም፡ ይሉ፡
ነበሩ፡ ይህ፡ የዳዊት፡ ልጅ፡ አይደለምን።
፳፬፡ ፈሪሳውያኝ፡ ግን፡ ሰምተው፡ አሉ። ይህ፡ አጋ
ንንትን፡ አያወጣም፡ *በብዔል፡ ዜቡል፡ በቀር፡ በሰይ
ጣናት፡ አለቃ። *ም፡ ፱፡ ፴፬። ፪፡ ንገሥ፡ ፩፡ ፪።
፳፭፡ የሱስም፡ አሳባቸውን፡ አወቀ፡ አላቸውም።
መንግሥት፡ ሁልዋ፡ እርስዋ፡ የምትከፈል፡ ትጠፋለ
ች። ቤትም፡ ሆነ፡ አገርም፡ ሆነ፡ እርሱ፡ በርሱ፡ የሚከ
ፈል፡ አይጸናም።
፳፮፡ ሰይጣንም፡ ሰይጠንን፡ ካወጣ፡ እርሱ፡ በርሱ፡
ተለያየ። እንዴትስ፡ መንግሥቱ፡ ትጸናለች።
፳፯፡ እኔስ፡ በብዔል፡ ዜቡል፡ ሰይጣናትን፡ ካወጣ
ሁ፡ ልጆቻችሁ፡ በማን፡ ያወጥዋቸዋል። ስለዚህም፡
እርሳቸው፡ ፈራጆች፡ ይሆኑባችኋል።
፳፰፡ እኔ፡ ግን፡ በእግዚአብሔር፡ መንፈስ፡ *ሰይጣ
ናትን፡ የማወጣ፡ ከሆንሁ። እነሆ፡ እርግጥ፡ የእግዚአ
ብሔር፡ መንግሥት፡ ወደላንት፡ ቀረበች።
፩፡ ዮሐ፡ ፫፡ ፰።
፳፱፡ ወይስ፡ እንዴት፡ ሰው፡ ይችላል፡ ወደ፡ ብርቱ፡
ቤት፡ ይገባ፡ ዘንድ፡ ከብቱንም፡ *ይነጥቅ፡ ዘንድ፡ አስ
ቀድሞ፡ ብርቱውን፡ ካላሠረ። ከዚያም፡ በኋላ፡ ቤቱ
ን፡ ይበዘብዛል። *ኢሳ፡ ፵፱፡ ፳፬፡ ፳፭።
፴፡ ከኔ፡ ጋራ፡ ያይደለ፡ በላዬ፡ ነው። ከኔ፡ ጋራም፡ ያ
ላከማች፡ እርሱ፡ ይበትናል። ማር፡ ፱፡ ፬።
፴፩፡ ስለዚህ፡ እላችኋለሁ። ኃጢአት፡ ሁሉ፡ ስድብ
ም፡ ለሰው፡ እንዲሰረይ። ስድብ፡ ግን፡ በመንፈስ፡ ቅ
ዱስ፡ ላይ፡ ለሰው፡ *አይሰረይም። *ዕብ፡ ፮፡ ፬፡ ፮።
፲፡ ፳፮። ፩፡ ዮሐ፡ ፭፡ ፲፮።
፴፪፡ አንዲትም፡ ቃል፡ የሚናገር፡ በሰው፡ ልጅ፡ ላ
ይ፡ ይሰረይለታል። በመንፈስ፡ ቅዱስ፡ ላይ፡ ግን፡ የሚ
ናገር፡ አይሰረይለትም፡ በዚህም፡ ዓለም፡ ቢሆን፡ በ
ሚመጣውም። ሉቃ፡ ፲፪፡ ፲። ፩፡ ጢሞ፡ ፩፡ ፲፫።
፩፡ ጴጥ፡ ፬፡ ፮።
፴፫፡ መልካም፡ ዛፍ፡ አድርጉ፡ ፍሬዋንም፡ መልካ
ም። ወይም፡ ክፉ፡ ዛፍ፡ አድርጉ፡ ፍሬዋንም፡ ክፉ።
ዛፍ፡ ከፍሬዋ፡ ትታወቃለችና። ም፡ ፯፡ ፲፯።
፴፬፡ እላንት፡ የባብ፡ ልጆች። እንዴት፡ መልካም፡
መናገር፡ ትችላላችሁ፡ እላንትም፡ ክፉ፡ ስትሆኑ። ልብ
ን፡ የመላውን፡ አፍ፡ ይናገራልና። ኢሳ፡ ፶፱፡ ፲፫።

፴፭፡ መልካምም፡ ሰው፡ከመልካምም፡ ከልቡ፡ መዝገብ፡ መልካምም፡ ያወጣል። ክፉም፡ ሰው፡ከክፉ፡ መዝገቡ፡ ክፉ፡ ያወጣል።

፴፮፡ እኔ፡ ግን፡ እላችኋለሁ። ምናምን፡ ነገር፡ ሁሉ፡ ሰዎች፡ የሚናገሩበት፡ ምላሽ፡ ይሰጡበታል፡በፍርድ፡ ቀን።

፴፯፡ ከነገርህ፡የተነሣ፡ትጸድቃለህና። ከነገርህም፡ የተነሣ፡ ይፈረድብሃልና።

፴፰፡ በዚያን፡ ጊዜ፡ከጻፎች፡ከፈሪሳውያን፡ወገን፡ ሰዎች፡ መለሱ፡ እንዲህ፡ ሲሉ። መምህር፡ ሆይ፡ ካንተ፡ *ምልክት፡ እናይ፡ ዘንድ፡ እንወዳለን።

ምዕ፡ ፲፮፡ ፩።

፴፱፡ እርሱም፡መለሰ፡አላቸውም። *ክፉና፡ አመንዝራ፡ ትውልድ፡ ምልክት፡ ይሻል፡ መልክትም፡ አይሰጠውም፡ ከዮናስ፡ ከነቢዩ፡ ምልክት፡ በቀር።

ሉቃ፡ ፲፩፡ ፳፱። *ኢሳ፡ ፶፯፡ ፫። ዮሐ፡ ፰፡ ፴፱።

፵፡ ዮናስ፡ ባሣ፡ ሆድ፡ ሶስት፡ ቀን፡ ሶስትም፡ ሌት፡ እንደ፡ነበረ። እንዲሁ፡የሰው፡ ልጅ፡ በምድር፡ ሆድ፡ ሶስት፡ ቀን፡ ሶስት፡ ሌሊትም፡ይኖራልና።

ዮና፡ ፪፡ ፩፡ ፪። ምዕ፡ ፲፮፡ ፳፩። ኤፌ፡ ፬፡ ፱።

፵፩፡ የነዌ፡ ሰዎች፡ ከዚህ፡ ትውልድ፡ ጋራ፡ በፍርድ፡ ይነሣሉ፡ ይፈረዱታልም፡ በዮናስ፡ ማስተማር፡ ተመልሰዋልና፡ከዚህም፡ እነሆ፡ ከዮናስ፡የሚበልጥ፡ አለ። ምዕ፡ ፲፩፡ ፲፮። ሮሜ፡ ፪፡ ፳፯። ዮና፡ ፫፡ ፭።

፵፪፡ ንግሥተ፡ አዜብ፡ከዚህ፡ ትውልድ፡ ጋራ፡ በፍርድ፡ ትነሣለች፡ ትፈረድዋለችም። *ከምድር፡ ዳር፡ መጥታለችና፡የሰሎሞንን፡ ጥበብ፡ ለመስማት፡ ከዚህም፡ እነሆ፡ ከሰሎሞን፡ የሚበልጥ፡ አለ።

*፩፡ ነገሥ፡ ፲።

፵፫፡ ርኩስ፡ መንፈስም፡ ከሰው፡ ከወጣ፡ በኋላ፡ ውኃ፡ በሌለበት፡ ስፍራ፡ ይዞራል፡ ዕረፍት፡ሊሻ፡አያገኝምም።

፵፬፡ ከዚያ፡ በኋላ፡ይላል። ወደ፡ወጣሁበት፡ቤቴ፡ ልመለስ። መጥቶም፡ ባዶ፡ ሁኖ፡ ያገኘዋል፡ ተጸርጎ፡ ተሸልሞ።

፵፭፡ ከዚያ፡ ወዲያም፡ ይሔዳል፡ ከርሱ፡ ጋራም፡ ሰባት፡ አጋንንት፡ ሌሎች፡ ይወስዳል፡ ከርሱ፡ የከፉትን። ይገቡበታልም፡ ከዚያም፡ ይኖራሉ። *የዚያም፡ ሰው፡ የኋለኛው፡ ከፊተኛው፡ ይከፋል። እንደዚህም፡ ይሆናል፡ለዚህ፡ክፉ፡ትውልድ። *፪፡ ጴጥ፡ ፪፡ ፳።

፵፮፡ ይህነንም፡ ለሕዝብ፡ሲነግር፡ እነሆ፡እናቱ፡ ወንድሞቹም፡ በሜዳ፡ ቁመው፡ ነበሩ፡ ይናገሩት፡ ዘንድ፡ሲሹ። ማር፡ ፫፡ ፴፩—፴፭። ሉቃ፡ ፰፡ ፲፱—፳፩።

ምዕ፡ ፲፫፡ ፶፭።

፵፯፡ ከሰዎችም፡ አንዱ፡ አለው። እነሆ፡ እናትህ፡ ወንድሞችህም፡ በሜዳ፡ ቁመዋል፡ ሊናገሩህ፡ ሲሹ።

፵፰፡ እርሱ፡ ግን፡ መለሰ፡ ለነገረውም፡ አለ። ማናት፡ እናቴ፡ ወንድሞቼስ፡ እለማን፡ ናቸው።

ሉቃ፡ ፪፡ ፱።

፵፱፡ እጁንም፡ ወደ፡ ደቀ፡ መዛሙርቱ፡ ዘረጋ፡ አለም። እነሆ፡ እናቴ፡ ወንድሞቼም።

፶፡ በሰማይ፡ ያለውን፡ያባቴን፡ፈቃድ፡ *የሚያደርግ፡ ሁሉ፡ እርሱ፡ ወንድሜ፡ እቴም፡ እናቴም፡ ነውና።

ሮሜ፡ ፰፡ ፳፱።

## ምዕራፍ፡ ፲፫፡

፩፡ የሱስም፡በዚያ፡ ቀን፡ ከቤት፡ወጣ፡በባሕርም፡ አጠገብ፡ተቀመጠ።

፪፡ እጅግ፡ ሰዎችም፡ ወደርሱ፡ ተከማቹ፡ ወደ፡ መርከብ፡ ወጥቶ፡ እስኪቀመጥ፡ ድረስ፡ ሰውም፡ ሁሉ፡ በደር፡ ቁመው፡ ነበር።

፫፡ እጅግም፡በምሳሌ፡ነገራቸው፡እንዲህ፡ሲል። እነሆ፡ ዘሪ፡ ሊዘራ፡ ወጣ። ማቴ፡ ፬፡ ፪—፳።

ሉቃ፡ ፰፡ ፬—፲፭።

፬፡ እርሱም፡ ሲዘራ፡ ጥቂት፡ በመንገድ፡ ወደቀ፡ ወፎችም፡ መጣና፡ በላው።

፭፡ ጥቂትም፡ በደንጊያ፡ ላይ፡ ወደቀ፡እጅግ፡ ምድር፡ ወደ፡ ሌለበት። የዚያን፡ ጊዜም፡ በቀለ፡ጥልቅ፡ ምድር፡ አልነበረውምና።

፮፡ ፀሐይ፡ ግን፡ በወጣች፡ጊዜ፡ ነደደ፡ ስርም፡ ስላልነራውም፡ ደረቀ።

፯፡ ጥቂትም፡ በሾህ፡ላይ፡ወደቀ፡እሾህም፡ ወጣና፡ አነቀው። ኤር፡ ፬፡ ፫።

፰፡ ሌላውም፡በመልካም፡ምድር፡ወደቀ፡ ፍሬውንም፡ ሰጠ። አንዱ፡ መቶ፡ ሌላውም፡ ስድሳ፡ ሌላውም፡ ሠላሣ። ዘፍ፡ ፳፮፡ ፲፪።

፱፡ የሚሰሙ፡ ጆሮች፡ ያሉት፡ይስማ።

ማር፡ ፯፡ ፲፮። ራእ፡ ፪፡ ፯።

፲፡ ደቀ፡ መዛሙርቱም፡ ወደርሱ፡ ቀረቡ፡ እንዲህም፡ አሉት። ስለ፡ ምን፡ በምሳሌ፡ ትነግራቸዋለህ።

፲፩፡ እርሱም፡ መለሰ፡ አላቸውም። ለእናንተ፡ የመንግሥተ፡ ሰማያትን፡ ምሥጢር፡ማወቅ፡ ተሰጥዋችኋልና። ለርሳቸው፡ ግን፡ አልተሰጣቸውም።

፲፪፡ ያለው፡ይሰጣል፡ *ይጨመርለታልምና። የሌለው፡ ግን፡ያውም፡ቅሉ፡ ያለው፡ ይሔድበታል።

ምዕ፡ ፳፭፡ ፳፱።

፲፫፡ ስለዚህ፡በምሳሌ፡ እነግራቸዋለሁ። ኢያዩ፡ አያዩምና፡ ኢየሰሙም፡ አይሰሙምና፡ አያስተውሉምም። ዘዳግ፡ ፳፱፡ ፬።

፲፬፡ የኢሳይያስም፡ትንቢት፡በርሳቸው፡ተፈጸመ፡ የሚለው። መስማት፡ትሰማላችሁ፡አታስተውሉምም፡ ማየትም፡ ታያላችሁ፡ አታዩምም።

ኢሳ፡ ፮፡ ፱፡ ፲።

፲፭፡ የዚህ፡ ወገን፡ ልብ፡ ደንድንዋልና፡ ጆሮዋቸውም፡ ከመስማት፡ ደንቍርዋልና፡ ዓይናቸውንም፡ ጨፍነዋልና። ባይናቸው፡ እንዳያዩ፡ በጆሮዋቸውም፡ እንዳይሰሙ፡ በልባቸውም፡ እንዳያስተውሉ፡እንዳይመለሱም፡ እፈውሳቸው፡ ዘንድ።

፲፮፤ እላንት፡ግን፡ ምስጋና፡ ላይናችሁ፡ ታያለችና። ለጀሮዋችሁም፡ ትሰማለችና። ሉቃ፡ ፲፤ ፳፫።

፲፯፤ እውነት፡እላችኋለሁና። ብዙ፡ከነቢያት፡ከጻድቃንም፡ እላንት፡ያያችሁትን፡ያዩ፡ዘንድ፡ ተመኙ፡ አላዩትምም። እላንትም፡የሰማችሁትን፡ይሰሙ፡ዘንድ፡ አልሰሙምም።

፲፰፤ ስሙ፡እንግዴህ፡እላንት፡የዘሪውን፡ምሳሌ።

፲፱፤ የመንግሥትን፡ነገር፡ሰው፡ቢሰማ፡ ባያስተውለውም፡ክፉው፡ ይመጣል፡ በልቡም፡ የተዘራውን፡ ይነጥቃል። ይህ፡ ነው፡ በመንገድ፡ ዳር፡ የተዘራ።

፳፤ በድንጊያም፡ ላይ፡ የተዘራ፡ ይህ፡ ነው፡ ነገርን፡ የሚሰማ፡ ፈጥኖም፡ በደስታ፡ የሚቀበል።

፳፩፤ ስርም፡ በርሱ፡ የለበትም፡ ነገር፡ ግን፡ ለጊዜው፡ነው። መከራም፡ በሆነ፡ ጊዜ፡ወይም፡ስደት፡ስለ፡ ነገር፡በዚያን፡ ጊዜ፡ ይክዳል።

፳፪፤ በሾህም፡ ላይ፡ የተዘራ፡ ይህ፡ ነው፡ ነገርን፡ የሚሰማ፡ይህነንም፡ዓለም፡ *ማሰብ፡ባለተግነትንም፡ መውደድ፡ነገርን፡ ያንቃል፡ ያለ፡ ፍሬም፡ ይሆናል። ፩፤ ጢሞ፡ ፮፤ ፱።

፳፫፤ በመልካም፡ ምድርም፡ የተዘራ፡ ይህ፡ ነው። ነገር፡ የሚሰማ፡ የሚያስተውለውም፡ ፍሬም፡ ይሰጣል። አንዱም፡ መቶ፡ ያደርጋል፡ ሌላውም፡ ስድሳ፡ ሌላውም፡ ሠላሣ።

፳፬፤ ሌላም፡ ምሳሌ፡ መሰለላቸው፡ እንደህ፡ ቢል። መንግሥተ፡ ሰማያት፡ መልካም፡ ዘር፡ በርሻው፡ የዘራ፡ ሰው፡ ትመስላለች። ቍ፡ ፴፯።

፳፭፤ ሰዎችም፡ በተኙ፡ ጊዜ፡ ጸላቱ፡ መጣ፡ እንክርዳድም፡ በስንዴው፡ መካከል፡ ዘርቶ፡ ሔደ።

፳፮፤ ስንዴውም፡ በበቀለና፡ ባፈራም፡ጊዜ፡ ያዚያን፡ ጊዜ፡ እንክርዳዱ፡ ደግሞ፡ ታየ።

፳፯፤ የባለ፡ ቤቱም፡ባሮች፡መጡ፡አሉትም። ጌታ፡ ሆይ፡ መልካም፡ ዘር፡ በርሻህ፡ ዘርትህ፡ አልነበርህምን። እንክርዳዱ፡ ከወዴት፡ መጣ።

፳፰፤ እርሱ፡ግና፡ አላቸው፡ጸላት፡ሰው፡ ይህነን፡ አደረገ። ባሮቹም፡ አሉት፡ ትወዳለህን፡ ሒደን፡ ብንለቅመው።

፳፱፤ እርሱ፡ግን፡አለ። አይሆንም። እንክርዳዱን፡ ስትለቅሙ፡ ስንዴውን፡ ከርሱ፡ ጋራ፡ እንዳትነቅሉ። ኢሳ፡ ፳፭፤ ፳።

፴፤ ተዋቸው፡ባንድ፡ ይደጉ፡እስኪታጨድ፡ድረስ። በመታጨዱም፡ ዘመን፡ አጫጆችን፡እላላሁ። እንክርዳዱን፡ቀድማችሁ፡ ሰብስቡ፡እሠሩትም፡ኢየነደው፡ እንዲቃጠል። ስንዴውን፡ ግን፡ በጎተራዬ፡ *አከማቹት። *ም፡ ፫፤ ፲፪።

፴፩፤ ሌላም፡ ምሳሌ፡ መሰለላቸው፡ እንደሁ፡ ብሎ። መንግሥተ፡ ሰማያት፡ የሰናፍጭ፡ ቅንጣት፡ ትመስላለች፡ ሰው፡ የወሰደት፡ በርሻውም፡ ዘራት። ሉቃ፡ ፲፫፤ ፲፰፤ ፲፱።

፴፪፤ እርስዋም፡ ከዘሮች፡ ሁሉ፡ ታናሽ፡ ናት። ባደገች፡ ጊዜ፡ግን፡ ከብቋያ፡ ሁሉ፡ ትበልጣለች፡ ዛፍም፡ ትሆናለች፡ የሰማይ፡ ወፎች፡ መጥተው፡ በጫፎችዋ፡ እስኪሰፍሩ፡ ድረስ።

፴፫፤ በሌላም፡ ምሳሌ፡ ነገራቸው። *መንግሥተ፡ ሰማያት፡ እርሾ፡ ትመስላለች፡ ሴት፡ የወሰደችው፡ በሶስትም፡ መስፈርያ፡ ደቄት፡ሸሸጋችው፡ሁሉ፡ እስኪመጥ፡ ድረስ። *ሉቃ፡ ፲፫፤ ፴፩።

፴፬፤ ይህነን፡ *ሁሉ፡ የሱስ፡ ለተሰበሰቡት፡ በምሳሌ፡ ተናገረ። ያለ፡ ምሳሌ፡ ግን፡ አልነገራቸውም። *ማር፡ ፬፤ ፴፫፤ ፴፬።

፴፭፤ ይፈጸም፡ዘንድ፡ *በነቢይ፡ የተባለው፡ እንደህ፡ ቢል። አፈን፡ በምሳሌ፡ እገልጣለሁ። ከዓለም፡ መሠረት፡ ጀምሮ፡ የተሰወረውን፡ እነግራለሁ። መዝ፡ ፸፰፤ ፪።

፴፮፤ የዚያን፡ጊዜ፡ የሱስ፡ አሕዛብን፡አሰናበተ፡ ወደ፡ ቤትም፡ ገባ። ደቀ፡ መዛሙርቱም፡ ወደርሱ፡ መጡ፡እንደህ፡ቢሉ። ተርጉምልን፡ የእርሻውን፡ እንክርዳድ፡ ምሳሌ።

፴፯፤ እርሱ፡ግን፡ መለሰ፡ አላቸውም። መልካም፡ ዘር፡ የዘራ፡ እርሱ፡ የሰው፡ ልጅ፡ ነው።

፴፰፤ እርሻውም፡ይህ፡ዓለም፡ነው። *መልካሙም፡ ዘር፡እሌህ፡የመንግሥት፡ልጆች፡ናቸው። እንክርዳዱም፡እርሳቸው፡የክፉ፡ልጆች፡ናቸው። *፩፤ ቆሮ፡ ፫፤ ፱።

፴፱፤ የዘራውም፡ ጸላት፡ እርሱ፡ዲያብሎስ፡ነው። መከሩም፡ የዘመን፡ፍጻሜ፡ነው። አጫጆችም፡ መላእክት፡ ናቸው።

፵፤ እንክርዳዱም፡ እንዲሰበሰብ፡ በሳትም፡ እንዲቃጠል። እንደሁ፡ይሆናል፡በዚህ፡ዓለም፡ፍጻሜ።

፵፩፤ የሰው፡ ልጅ፡ መልክተኞቹን፡ ይልካል፡ ከመንግሥቱም፡ እንቅፋትን፡ ሁሉ፡ ይሰበስባሉ፡ ዓመፃም፡ የሚያደርጉን። ም፡ ፳፭፤ ፴፩፤—፵፮።

፵፪፤ ወደ፡እቶነ፡ እሳትም፡ ይጥልዋቸዋል፡ ልቅሶ፡ ጥርስ፡ ማፏጨትም፡ ወደለበት። ም፡ ፰፤ ፲፪።

፵፫፤ በዚያን፡ጊዜ፡ *ጻድቃን፡እንደ፡ ፀሐይ፡ ይበራሉ፡ ባባታቸው፡ መንግሥት። የሚሰማ፡ ጆሮ፡ ያለው፡ ይሰማ። ዳን፡ ፲፪፤ ፫።

፵፬፤ ደግሞ፡መንግሥተ፡ሰማያት፡ በርሻ፡ውሥጥ፡ የተቀበረ፡ መዝገብ፡ትመስላለች፡ሰው፡ ያገኘው፡የሰወረውም፡ ከደስታውም፡ የተነሣ፡ሔደ፡ያለውንም፡ ሁሉ፡ ሸጠ፡ያነንም፡ እርሻ፡ *ገዛ። *ም፡ ፲፱፤ ፳፱። ፊል፡ ፫፤ ፯።

፵፭፤ ደግሞ፡ መንግሥተ፡ ሰማያት፡ ነጋዴ፡ ትመስላለች፡ መልካም፡ ዕንቍ፡ የሚሻ።

፵፮፤ አንዲትም፡*ዕንቍ፡ዋጋዋ፡የበዛ፡ባገኘ፡ጊዜ፡ ሔደ፡ ከብቱንም፡ ሁሉ፡ ሸጠ፡ ገዛትም። *ምሳ፡ ፰፤ ፲፤ ፲፩።

፵፯፤ ደግሞ፡ መንግሥተ፡ ሰማያት፡ ወጽመድ፡ ትመስላለች፡ ወደ፡ ባሕር፡ የተጣለች፡ ከዓሣም፡ወገን፡ ሁሉ፡ የሰበሰበች። ም፡ ፳፪፤ ፱፤ ፲።

፵፰፤ በመላችም፡ጊዜ፡ ወደ፡ ዳር፡ አወጥዋት፡ ተቀመጡም፡ መልካሙንም፡በከፈራቸው፡አከማቹ፡ ክፉ፡ክፉውን፡ግን፡ ወደ፡ ሚደ፡ ጣሉት።

፵፱፤ እንደሁ፡ ይሆናል፡ በፍጻሜ፡ ዘመን። መላእክት፡ ይወጣሉ፡*ክፉችንም፡ ከጻድቃን፡ መካከል፡ ይለያሉ። *ም፡ ፳፭፡ ፴፪።

፶፤ ወደ፡እቶኑ፡እሳትም፡ ይጨምርዋቸዋል። ከዚያም፡ ልቅሶ፡ ጥርስ፡ ማፋጨትም፡ ይሆናል።

፶፩፤ የሱስም፡ አላቸው። ይህነን፡ ሁሉ፡ አስተዋላችሁን። እርሳቸውም፡ አሉት። አዎን፡ አቤቱ።

፶፪፤ እርሱም፡ አላቸው። ስለዚህ፡ ጻፊ፡ ሁሉ፡ ለመንግሥተ፡ ሰማያት፡ የተማረ፡ ባለቤት፡ ሰው፡ ይመስላል፡ ከመዝገቡ፡ አዲሱን፡ ለሮጌውንም፡ የሚያወጣ። መዝ፡ ፻፵፬፡ ፲፫።

፶፫፤ የሱስም፡እነዚህን፡ምሳሌዎች፡በፈጸመ፡ጊዜ፡ ከዚያ፡ተለወሰ። ማር፡ ፮፡ ፩፡—፯። ሉቃ፡ ፬፡ ፲፮፡—፴።

፶፬፤ ወደገሩም፡ መጣ፡ በመስጊደቸውም፡ አስተማረ። እስኪደነቁ፡ድረስ፡ እስኪሉም። ከወዴት፡ ለርሱ፡ ይህ፡ ጥበብ፡ ተሰጠው፡ ይህ፡ ኃይልስ።

፶፭፤ ይህ፡ የንጨት፡ ጸራቢ፡ልጅ፡ አይደለምን። እናቱስ፡ ማርያም፡ትባል፡የለችምን። ወንድሞቹስ፡ ያዕቆብ፡ዮሴስም፡ሲሞንም፡ይሁዳም፡አይደሉምን። ም፡ ፲፪፡ ፵፯።

፶፮፤ እኅቶቹስ፡ ሁሉ፡ ከኛ፡ ጋራ፡ አይደሉምን። ከወዴት፡ ለዚህ፡ ይህ፡ ሁሉ፡ መጣለት። ዮሐ፡ ፯፡ ፲፭፡ ፶፪።

፶፯፤ ይጠራጠሩበትም፡ ነበር። የሱስ፡ ግን፡ አላቸው። *ነቢይ፡ አይከብርም፡ ባገሩ፡ በቤቱም፡ በቀር። *ዮሐ፡ ፬፡ ፵፬።

፶፰፤ ከዚያም፡ ብዙ፡ ኃይል፡ አላደረገም፡ ካለማመናቸው፡ የተነሣ።

ምዕራፍ፡ ፲፬፤

፩፤ በዚያም፡ ዘመን፡ ሄሮድስ፡ የገሊላ፡ ንጉሥ፡ የየሱስን፡ ነገር፡ ሰማ። ማር፡ ፮፡ ፲፬፡ ፲፯፡—፳፱። ሉቃ፡ ፫፡ ፲፱፡ ፳።

፪፤ ለሎላልቱም፡ አለ። ይህ፡ ነው፡ ዮሐንስ፡ መጥምቁ። እርሱ፡ከሙታን፡ተነሣ፡ ስለዚህም፡ እንደሁ፡ ያሉ፡ ኃይላት፡ ይደረጉበታል።

፫፤ ሄሮድስ፡ ዮሐንስን፡ ይዞ፡ አሥሮት፡ በግዞትም፡ አኑሮት፡ ነበርና፡ ስለ፡ሄሮድያደ፡ስለ፡ ወንድሙ፡ ስለ፡ ፊልጶስ፡ ምሽት።

፬፤ ዮሐንስ፡ ይለው፡ ነበርና፡ ላንተ፡ትሆንህ፡ዘንድ፡ *አይገባህም። *ዘሌዋ፡ ፲፰፡ ፲፮።

፭፤ ሊገድለውም፡ ይወድ፡ ነበር። ሕዝብን፡ ግን፡ ፈራቸው፡ እርሱ፡ በርሳቸው፡ ዘንድ፡ እንደ፡ *ነቢይ፡ ነበርና። *ም፡ ፳፩፡ ፳፮።

፮፤ የሄሮድስ፡*የመወለደ፡ም፡ቀን፡በሆነ፡ጊዜ፡ የሄሮድያደ፡ ልጅ፡ በመካከል፡ዘፈነች፡ ሄሮድስንም፡ደስ፡ አሰኘች። *ሆሴ፡ ፯፡ ፭።

፯፤ ስለዚህም፡በመሐላ፡ ተስፋ፡ አስደረጋት፡ የምትሻውን፡ ሁሉ፡ እንዲሰጣት።

፰፤ እርስዋም፡ ከናትዋ፡ ዘንድ፡ ተመክራ፡ አለች። የዮሐንስን፡ የመጥምቁን፡ ራስ፡ ከዚህ፡ በሰፈድ፡ ስጠኝ።

፱፤ ንጉሡም፡ አዘነ። ነገር፡ ግን፡ ስለ፡ መሐላው፡ ከርሱ፡ጋራም፡ስለ፡ተቀመጡት፡እንዲሰጥዋት፡አዘዘ።

፲፤ ላከም፡ የዮሐንስንም፡ ራስ፡ አስቈረጠ፡ በግዞት፡ ሳለ።

፲፩፤ ራሱንም፡ በሰፈድ፡አመጡ፡ለብላቴናዪቱም፡ ሰጥዋት። እርስዋም፡ ለናትዋ፡ አመጣችው።

፲፪፤ ደቀ፡ መዛሙርቱም፡ መጡ፡ ሬሣውንም፡ አንሥተው፡ ቀበሩት። መጥተውም፡ ለየሱስ፡ ነገሩት። ም፡ ፳፯፡ ፶፯።

፲፫፤ የሱስም፡ በሰማ፡ ጊዜ፡ ከዚያ፡ ተነሥቶ፡ ወደ፡ ምድረ፡ በዳ፡ ብቻውን፡ በታንኳ፡ ሔደ። አሕዛብም፡ ሰምተው፡ ከከተሞች፡ ተከተሉት፡ በግራቸው። ማር፡ ፮፡ ፴፩፡—፵፬። ዮሐ፡ ፮፡ ፩፡—፲፭።

፲፬፤ የሱስም፡ በወጣ፡ ጊዜ፡ ብዙ፡አሕዛብ፡ አየ፡ አዘነላቸውም፡ ድውያናቸውም፡ አዳነ። ም፡ ፱፡ ፴፮።

፲፭፤ በመሸም፡ጊዜ፡ደቀ፡ መዛሙርቱ፡ወደርሱ፡መጡ፡ እንደህ፡ ሲሉ። ቦታው፡ ምድረ፡ በዳ፡ ነው፡ ጊዜውም፡ አለፈ። አሕዛብን፡ አሰናብት፡ ወደ፡ መንደር፡ ይሒዱ፡ ሲሳያቸውንም፡ ይግዙ።

፲፮፤ የሱስም፡አላቸው፡ ለመሔደቸው፡ ምን፡ አግድዋችሁ። እላንተ፡ ስጥዋቸው፡ ሊበሉ።

፲፯፤ እርሳቸውም፡ አሉት። ከዚህ፡ የለነም፡ካምስት፡ እንጀራና፡ ከሁለት፡ ዓሣ፡ በቀር።

፲፰፤ እርሱም፡ አላቸው፡ ወዲህ፡ ወደኔ፡ አምጥዋቸው።

፲፱፤ አሕዛብም፡ በመስክ፡ ላይ፡ እንዲቀመጡ፡ አዘዘ። አምስቱንም፡ እንጀራና፡ሁለቱን፡ዓሣ፡ ወሰደ፡ ወደ፡ ሰማይም፡ አየ፡ ባርከውም። እንጀራውንም፡ ቈረሰ፡ ለደቀ፡ መዛሙርቱም፡ ለአሕዛብ፡ ሰጡት።

፳፤ ሁሉም፡ በሉ፡ ጠገቡም፡ የተረፈውንም፡ ቍራሽ፡ አነሡ፡ አሥራ፡ ሁለት፡ ሞስብ፡ መልተው። ፪፡ ነገሥ፡ ፬፡ ፵፬።

፳፩፤ የበሉትም፡ አምስት፡ ሺህ፡ ሰዎች፡ነበሩ፡ ከሴቶችና፡ ከሕፃናቱ፡ ሌላ።

፳፪፤ የዚያን፡ ጊዜም፡ የሱስ፡ ደቀ፡ መዛሙርቱን፡ ግድ፡ አላቸው፡ ወደ፡ መርከብ፡እንዲወጡ፡ ወደ፡ ማዶም፡ ይቀድሙት፡ ዘንድ፡ አሕዛብን፡ እስኪያሰናብት፡ድረስ። ማር፡ ፮፡ ፵፭፡—፶፮። ዮሐ፡ ፮፡ ፲፮፡—፳፩።

፳፫፤ አሕዛብንም፡ አሰናብቶ፡ ወደ፡*ተራራ፡ወጣ፡ ብቻውን፡ ይጸልይ፡ ዘንድ። በመሸም፡ጊዜ፡ ከዚያ፡ ብቻውን፡ ነበረ። *ሉቃ፡ ፮፡ ፲፪። ም፡ ፱፡ ፲፰።

፳፬፤ ታንኳይቱም፡ በባሕር፡ መካከል፡ ነበረች፡ ከመውጀ፡ የተነሣ፡ ስትጨነቅ። ነፋስ፡ በፊቱ፡ ነበርና።

፳፭፤ በሌቱም፡ ባራተኛው፡ ሰዓት፡ የሱስ፡ መጣባቸው፡ በባሕር፡ ላይ፡ ሲሔድ።

፳፮፤ ደቀ፡ መዛሙርቱም፡ ባዩት፡ጊዜ፡ በባሕር፡ ሲሔድ፡ደነገጡ፡እንደህ፡ሲሉ፤ *ምትሐት፡ነው። ከፍርሃትም፡ የተነሣ፡ ጮሁ።

*ሉቃ፡ ፳፬፡ ፴፯።

፳፯፤ የሱስም፡ የዚያን፡ ጊዜ፡ ተናገራቸው፡ እንደህ፡ ሲል። እመኑ፡ እኔ፡ ነኝ፡ አትፍሩ።

፳፰፤ ጴጥሮስም፡ መለሰለት፡ አለም። አቤቱ፡ አንተስ፡ እንደ፡ ሆንህ፡ አዘዘኝ፡ ወደንተ፡ እንድመጣ፡ በውኃ፡ ላይ።

፳፱፤ እርሱም፡ አለው፡ ና። ጴጥሮስም፡ ከመርከብ፡ ወረደ፡ በውኃም፡ላይ፡ሔደ፡ወደ፡የሱስ፡ሊደርስ።

፴፤ የነፋሱን፡ ብርታት፡ ግን፡ ባየ፡ ጊዜ፡ ፈራ፡ ለመሥጠምም፡ ደርሶ፡ ጮኸ፡ እንደህ፡ ሲል፡ አቤቱ፡ አድነኝ።

ም፡ ፰፡ ፳፭።

፴፩፤ የሱስም፡ በዚያን፡ ጊዜ፡ እጁን፡ ዘረጋ፡ ያዘውም፡ እንደህም፡ አለው። አንተ፡ ሃይማኖትህ፡ ያነሰ፡ ምነው፡ ተጠራጠርህ።

ም፡ ፮፡ ፴። ያዕ፡ ፩፡ ፮።

፴፪፤ ወደ፡ መርከቡም፡ በሰረሩ፡ ጊዜ፡ ነፋሱ፡ ጸጥ፡ አለ።

፴፫፤ በመርከቡም፡ የነበሩ፡ መጥተው፡ ሰገዱለት፡ እንደህ፡ ሲሉ። አንተ፡ በውነት፡ የእግዚአብሔር፡ ልጅ፡ ነህ።

ም፡ ፰፡ ፳፱። ፲፮፡ ፲፮።

፴፬፤ ተሻግረውም፡ ወደ፡ ጌኔሰሬጥ፡ ምድር፡ መጡ።

፴፭፤ የዚያም፡ ቦታ፡ ሰዎች፡ ባወቁት፡ ጊዜ፡ ወደዚያች፡ አገር፡ ሁልዋ፡ ላኩ፡ ባጠገባቸው፡ ወደለቸው፡ ድውያንንም፡ ሁሉ፡ አመጡለት።

፴፮፤ ለመኑትም፡ የልብሱን፡ ጫፍ፡ *ብቻ፡ ይነኩ፡ ዘንድ። የነካውም፡ ሁሉ፡ ዳነ።

*ም፡ ፱፡ ፳፩።
ሉቃ፡ ፮፡ ፲፱።

ምዕራፍ፡ ፲፭፤

፩፤ በዚያን፡ ጊዜ፡ ጻፎች፡ ፈሪሳውያንም፡ ከየሩሳሌም፡ ወደ፡ የሱስ፡ መጡ፡ እንደህ፡ ሲሉ።

ማር፡ ፯፡ ፩—፳፫።

፪፤ ለምን፡ ደቀ፡ መዛሙርትህ፡ የሽማግሎችን፡ *ወግ፡ ይተላለፋሉ። እጃቸውን፡ †አይታጠቡምና፡ እንጀራ፡ ሲበሉ።

*ዘዳግ፡ ፬፡ ፪። †ሉቃ፡ ፲፩፡ ፴፰።

፫፤ እርሱም፡ መልሶ፡ አላቸው። ለምን፡ እላንትስ፡ የእግዚአብሔርን፡ ሥርዓት፡ ትተላለፋላችሁ፡ ስለ፡ ወጋችሁ።

፬፤ እግዚአብሔር፡ *እንደህ፡ ብሎ፡ አዝዋልና። አባትህንና፡ እናትህን፡ አክብር። ክፉ፡ ነገርም፡ ባባቱና፡ በናቱ፡ የሚናገር፡ ፈጽሞ፡ ይሙት።

*ዘፀአ፡ ፳፡ ፲፪። ፳፩፡ ፲፯።

፭፤ እላንተ፡ ግን፡ ትላላችሁ። አባቱን፡ ወይም፡ እናቱን፡ ያለ። ቍርባን፡ ይሁን፡ ከኔ፡ ትረባበት፡ ዘንድ። አባቱንና፡ እናቱን፡ አያከብርም።

፮፤ ስለ፡ ወጋችሁም፡ የእግዚአብሔርን፡ ሥርዓት፡ አላላችሁ።

፯፤ እላንተ፡ ግብዞች፡ መልካም፡ ተናገረባችሁ፡ *ኢሳይያስ፡ እንደህ፡ ሲል።

*ኢሳ፡ ፳፱፡ ፲፫።

፰፤ ይህ፡ ሕዝብ፡ ባፉ፡ ወደኔ፡ ይቀርባል፡ በከንፈሩም፡ ያከብረኛል፡ ልቡ፡ ግን፡ ከኔ፡ አስረዝሞ፡ ይርቃል።

፱፤ በከንቱም፡ ያመልኩኛል፡ የሰውን፡ ሥርዓት፡ ትምህርት፡ ኢያስተማሩ።

፲፤ ሕዝቡንም፡ ጸራ፡ እንደህም፡ አላቸው። ስሙ፡ አስተውሉም።

፲፩፤ ወደፉ፡ *የሚገባ፡ ሰውን፡ የሚያረክስ፡ አይደለም። ካፉ፡ †የሚወጣ፡ ግን፡ ይህ፡ ሰውን፡ ያረክሳል።

*፩፡ ጢሞ፡ ፬፡ ፬። †ም፡ ፲፪፡ ፴፬—፴፯።

፲፪፤ የዚያን፡ ጊዜ፡ ደቀ፡ መዛሙርቱ፡ መጡ፡ አሉትም። አወቅህን፡ ፈሪሳውያን፡ ይህነን፡ ነገር፡ በሰሙ፡ ጊዜ፡ እንደንጐረጐሩ።

፲፫፤ እርሱም፡ መልሶ፡ እንደህ፡ አለ። ተክል፡ ሁሉ፡ የሰማዩ፡ አባቴ፡ ያልተከለው፡ ይነቀላል።

፲፬፤ ተውዋቸው፡ ዕውሮች፡ ናቸው፡ *ዕውሮችን፡ የሚመሩ። ዕውርም፡ ዕውርን፡ ቢመራው፡ ሁለቱ፡ ተያይዘው፡ ወደ፡ ጕድጓድ፡ ይወድቃሉ።

*ሉቃ፡ ፮፡ ፴፱። ሮሜ፡ ፪፡ ፲፱።

፲፭፤ ጴጥሮስም፡ መለሰ፡ እንደህም፡ አለው። ይህነን፡ ምሳሌ፡ ተርጕምልን።

፲፮፤ የሱስም፡ እንደህ፡ አለ። እላንተም፡ ደግሞ፡ እስከ፡ ዛሬ፡ ድረስ፡ አታስተውሉምን።

፲፯፤ አታውቁምን፡ ወደ፡ አፍ፡ የሚገባ፡ ሁሉ፡ ወደ፡ ሆድ፡ እንደ፡ ወርድ፡ ወደ፡ ሚደም፡ ይወድቃል።

፲፰፤ ካፉ፡ ግን፡ የሚወጣ፡ ከልብ፡ ይወጣል። ሰውንም፡ የሚያረክሰው፡ እርሱ፡ ነው።

፲፱፤ *ከልብ፡ ይወጣልና፡ ክፉ፡ አሳብ። መግደል። ምንዝር። ዝሙት። መስረቅ። አሰት፡ መመስከር። ስድብ።

*ዘፍ፡ ፰፡ ፳፩።

፳፤ ይህ፡ ነው፡ ሰውን፡ የሚረክስ። እጅን፡ ሳይታጠብ፡ መብላትስ፡ ሰውን፡ አያረክሰም።

፳፩፤ የሱስም፡ ከዚያ፡ ወጥቶ፡ ወደ፡ ጢሮስና፡ ወደ፡ ሲደና፡ አገር፡ ሔደ።

ማር፡ ፯፡ ፳፬—፴።

፳፪፤ እነሆም፡ የከነዓን፡ ሴት፡ ከዚያ፡ አገር፡ ወጥች፡ ስትጮህ፡ እንደህም፡ ስትል። ማረኝ፡ አቤቱ፡ የዳዊት፡ ልጅ። ልጄን፡ ክፉ፡ ሰይጣን፡ ይዞ፡ ያሳብደታልና።

፳፫፤ እርሱ፡ ግን፡ አንድችም፡ አልመለሰላትም። ደቀ፡ መዛሙርቱም፡ መጡ፡ ለመኑትም፡ እንደህም፡ አሉት። አሰናብታት፡ በኋላችን፡ ትጮሃለችና።

፳፬፤ እርሱም፡ መለሰ፡ አላቸውም። አልተላክሁም፡ ወደ፡ *ጠፉ፡ በጎች፡ ወደ፡ እሥራኤል፡ ቤት፡ በቀር።

*ም፡ ፲፡ ፮።

፳፭፤ እርስዋ፡ ግን፡ መጣችና፡ ሰገደችለት፡ እንደህ፡ ስትል። አቤቱ፡ እርዳኝ።

፳፮፤ እረሱም፡ መለሰ፡ እንደህ፡ ሲል፡ መልካም፡

አይደለውም፡ የልጆችን፡ እንጀራ፡ ነሥቶ፡ ለውሾች፡ መስጠት።

፳፯፤ እርስዋም፡ አለች። አዎን፡ አቤቱ፡ ቡችሎችም፡ ደግሞ፡ ከጌቶቻቸው፡ ማዕድ፡ የወደቀውን፡ ፍርፋሪ፡ ይበላሉ።

፳፰፤ የዚያን፡ ጊዜ፡ መለሶ፡ የሱስ፡ አላትም። አንች፡ ሴት፡ *ሃይማኖትሽ፡ ታላቅ፡ ነው። ይሁንልሽ፡ እንደ፡ ወደድሽ። ልጅዋም፡ ደነች፡ በዚያች፡ ሰዓት።
*ም፡ ፰፤ ፲፤ ፲፫።

፳፱፤ *የሱስም፡ ከዚያ፡ ተነሥቶ፡ ወደ፡ ገሊላ፡ ባሕር፡ አጠገብ፡ መጣ። ወደ፡ ተራራም፡ ወጣ። ከዚያም፡ ተቀመጠ። *ማር፡ ፯፤ ፴፩።

፴፤ ብዙም፡ አሕዛብ፡ ወደርሱ፡ መጡ። ከርሳቸው፡ ጋራም፡ አንካሶች፡ ነበሩ፡ ዕውሮችም፡ ድደችም፡ ደካሞችም፡ ሌሎችም፡ ብዙ። በየሱስም፡ በግሩ፡ በታች፡ ጣልዋቸው፡ ፈወሳቸውም።

፴፩፤ አሕዛብ፡ እስኪደነቁ፡ ድረስ፡ ድደች፡ ሲናገሩ፡ አይተው፡ ደካሞችም፡ ሲበረቱ፡ አንካሶችም፡ ሲሔዱ፡ ዕውሮችም፡ ሲያዩ። የእሥራኤልንም፡ አምላክ፡ አመሰገኑ።

፴፪፤ የሱስም፡ ደቀ፡ መዛሙርቱን፡ ጸራ፡ አላቸውም። እኔ፡ ለዚህ፡ ሕዝብ፡ *እራራለሁ። ሶስት፡ ቀናቸው፡ ነውና፡ ከዚህ፡ ከኔ፡ ጋራ፡ ከዋሉ። የሚበሉትም፡ የላቸውም። ጾማቸውንም፡ እሰዳቸው፡ ዘንድ፡ አልወድም፡ በመንገድ፡ እንዳይዝሉ። *ማር፡ ፰፤ ፩፤—፲።

፴፫፤ ደቀ፡ መዛሙርቱም፡ አሉት። ከወዴት፡ በምድረ፡ በዳ፡ እንጀራ፡ እናመጣለን፡ ይህን፡ ለሚያህል፡ ሰው፡ የሚያጸግብ። ም፡ ፲፬፤ ፲፬፤ ፲፯።

፴፬፤ የሱስም፡ አላቸው፡ ስንት፡ እንጀራ፡ አላችሁ። እርሳቸውም፡ አሉ፡ ሰባት፡ ጥቂትም፡ ዓሣ።

፴፭፤ አዘዘም፡ አሕዛብ፡ በምድር፡ ላይ፡ እንዲቀመጡ። ሰባቱንም፡ እንጀራ፡ ወሰደ፡ ዓሣውንም።

፴፮፤ አመስግኖም፡ ቈረሰ፡ ለደቀ፡ መዛሙርቱም፡ ሰጠ። ደቀ፡ መዛሙርቱም፡ ለሕዝብ።
፩፡ ጢሞ፡ ፬፤ ፬፤ ፭።

፴፯፤ ሁሉም፡ በሉ፡ ጸገቡም። የተረፈውንም፡ ቍራሽ፡ ሰባት፡ ሞሰብ፡ መልተው፡ አነሡ። ም፡ ፲፬፤ ፳።

፴፰፤ የበሉትም፡ አራት፡ ሺህ፡ ነበሩ፡ ከሴቶችና፡ ከሕፃናቱ፡ ሌላ።

፴፱፤ አሕዛብንም፡ አሰናብቶ፡ ወደ፡ መርከብ፡ ወጣ፡ ወደ፡ መግደላ፡ አገርም፡ ሔደ። ም፡ ፲፬፤ ፴፫።

## ምዕራፍ፡ ፲፮፤

፩፤ ፈሪሳውያንና፡ ሰዱቃውያንም፡ መጡ፡ ሲፈትኑትም፡ ጠየቁት፡ ምልክት፡ ከሰማይ፡ ያሳያቸው፡ ዘንድ። ማቴ፡ ፲፪፤ ፴፰። ማር፡ ፰፤ ፲፩፤—፳፩።

፪፤ እርሱም፡ መለሰ፡ አላቸውም። በመሸ፡ ጊዜ፡ ትላላችሁ፡ ብራ፡ ይሆናል። ሰማዩ፡ ቀልትዋልና።
ሉቃ፡ ፲፪፤ ፶፬፤ ፶፮።

፫፤ ሲጸባም፡ ትላላችሁ፡ ዛሬ፡ ይዘንማል። ሰማዩ፡ ቀልትዋልና፡ ደምንዋልምና። እላንተ፡ ግብዞች፡ የሰማዩን፡ ፊት፡ መለየት፡ ታውቃላችሁ። የዘመኑንስ፡ *ምልክት፡ ትለዩ፡ ዘንድ፡ አትችሉምን። ም፡ ፲፩፤ ፬።

፬፤ ክፉ፡ ትውልድ፡ አመንዝራም፡ ምልክት፡ ይሻል። ምልክትም፡ አይሰጠውም፡ ከነቢዩ፡ ከዮናስ፡ ምልክት፡ በቀር። ትቶዋቸውም፡ ሔደ። ም፡ ፲፪፤ ፴፱፤ ፵።

፭፤ ደቀ፡ መዛሙርቱም፡ ወደ፡ ማዶ፡ ደርሰው፡ እንጀራ፡ መውሰድ፡ ረሱ።

፮፤ የሱስም፡ አላቸው። እዩ፡ ተጠበቁም፡ ከፈሪሳውያንና፡ ከሰዱቃውያን፡ እርሾ። ሉቃ፡ ፲፪፤ ፩።

፯፤ እርሳቸው፡ ግን፡ በልባቸው፡ አሰቡ፡ እንዲህ፡ ሲሉ። እንጀራ፡ ባንወሰድ፡ ነው።

፰፤ የሱስም፡ አውቀ፡ አላቸው። ለምን፡ በልባችሁ፡ ታስባላችሁ፡ እላንተ፡ ሃይማኖታችሁ፡ *የጐደለ፡ እንጀራን፡ ባትወስዱ፡ ነው። ም፡ ፮፤ ፴።

፱፤ እስከ፡ ዛሬ፡ ድረስ፡ አታስተውሉምን። አምስቱንም፡ እንጀራ፡ ላምስት፡ ሺህ፡ ከቶ፡ አታስቡምን፡ ስንት፡ ሞሰብም፡ እንዳነሣችሁ። ም፡ ፲፬፡ ፲፯።

፲፡ ሰባቱንስ፡ እንጀራ፡ *ላራት፡ ሺህ፡ ስንት፡ ሞሰብም፡ አነሣችሁ። *ም፡ ፲፭፤ ፴፪፤—፴፱።

፲፩፤ እንዴት፡ አታስተውሉምን፡ ስለ፡ እንጀራ፡ እንዳላልኋችሁ፡ ከፈሪሳውያንና፡ ከሳዱቃውያን፡ እርሾ፡ እንድትጠበቁ፡ ብዬ።

፲፪፤ ከዚያ፡ ወዲያ፡ አወቁ፡ እንዳላላቸው፡ ከንጀራ፡ እርሾ፡ ይጠበቁ፡ ዘንድ፡ ከፈሪሳውያን፡ ትምህርት፡ እንጂ።

፲፫፤ የሱስም፡ ወደ፡ ቂሣርያ፡ በመጣ፡ ጊዜ፡ ወደ፡ ፊልጶስ፡ አገር፡ ደቀ፡ መዛሙርቱን፡ ጠየቀ፡ እንዲህ፡ ብሎ። ምን፡ ይላሉ፡ ሰዎች፡ ከኔ፡ ከሰው፡ ልጅ።
ማር፡ ፰፤ ፳፯፤—፴። ሉቃ፡ ፱፤ ፲፰፤—፳፩።

፲፬፤ እርሳቸውም፡ አሉ። መጥምቁ፡ *ዮሐንስ፡ ነው፡ የሚሉህ፡ አሉ። እኩሉም፡ ኤልያስ። እኩሉም፡ ኤርምያስ፡ ወይም፡ ከነቢያት፡ አንዱ፡ ነው።
ም፡ ፲፬፤ ፪። ፲፯፤ ፲።

፲፭፤ አላቸውም፡ እላንተስ፡ ምን፡ ትላላችሁ፡ እኔ፡ እንደ፡ ሆንሁ።

፲፮፤ ሲሞን፡ ጴጥሮስም፡ መለሰ፡ አለም። *አንተ፡ ክርስቶስ፡ ነህ፡ የሕያው፡ የእግዚአብሔር፡ ልጅ።
*ዮሐ፡ ፮፤ ፷፱።

፲፯፤ የሱስም፡ መለሰ፡ እንዲህም፡ አለው። ምስጉን፡ ነህ፡ ሲሞን፡ ሆይ፡ የዮና፡ ልጅ። *ሥጋና፡ ደም፡ ይህነን፡ አልገለጠልህምና፡ ነገር፡ ግን፡ የሰማዩ፡ አባቴ።
*ገላ፡ ፩፤ ፲፭፤ ፲፮።

፲፰፤ እኔም፡ እልሃለሁ። አንተ፡ *ደንጊያ፡ ነህ፡ በዚችም፡ ደንጊያ፡ ቤቴ፡ ክርስቲያኔን፡ እሰራለሁ። የገሃነምም፡ ደጆች፡ አይገለብቱባትም። *ዮሐ፡ ፩፤ ፵፪።
ኤፌ፡ ፪፤ ፳።

፲፱፡ የመንግሥተ፡ ሰማያትንም፡ *መክፈቻ፡ እሰጥሃለሁ። በምድርም፡ ያሠርኸው፡ በሰማያት፡ የታሠረ፡ ይሆናል። በምድርም፡ የፈታኸው፡ በሰማያት፡ የተፈታ፡ ይሆናል። *ም፡ ፲፰፡ ፲፰።

፳፡ ከዚያ፡ ወዲያም፡ ደቀ፡ መዛሙርቱን፡ አዘዘ፡ ለማንም፡ እንደይናገሩ፡የሱስ፡ ክርስቶስ፡እንደ፡ሆነ። ም፡ ፲፯፡ ፱።

፳፩፡ ከዚያ፡ ቀን፡ጀምሮ፡ የሱስ፡ ለደቀ፡ መዛሙርቱ፡ ይገልጥላቸው፡ ጀመረ፡ እንዲገባው፡ ወደ፡ የሩሳሌም፡ ይሔድ፡ ዘንድ፡ ብዙም፡መከራ፡ከሽመግሌዎች፡ ከካህናትም፡ አለቆች፡ ከጻፎችም፡ ይቀበል፡ ዘንድ፡ እርሱም፡ በሦስተኛው፡ ቀን፡ከሙታን፡ይነሣ፡ዘንድ። ማር፡ ፰፡ ፴፩። ሉቃ፡ ፱፡ ፳፪፡ ፳፯።

፳፪፡ ጴጥሮስም፡ ይዞት፡ ይገሥጸው፡ ጀመረ፡ እንዲህ፡ ሲል። አያድርስብህ፡ አቤቱ፡ ይህ፡ አይሆንብህም። ም፡ ፲፪፡ ፵። ዮሐ፡ ፪፡ ፲፱።

፳፫፡ እርሱም፡ ዙሮ፡ ጴጥሮስን፡ ገሠጸው፡ አለውም፡ በኋላዬ፡ ሒድ፡ አንተ፡ ሰይጣን። ዕንቅፋት፡ሁነህብኸልና። ለእግዚአብሔር፡ የሚሆነውን፡አታስብምና፡ የሰውን፡ እንጂ።

፳፬፡ የዚያን፡ ጊዜ፡ የሱስ፡ ለደቀ፡ መዛሙርቱ፡ አለ። እኔን፡ መከተል፡የሚወድ፡ቢኖር፡ነፍሱን፡ይካድ፡ መስቀሉንም፡ ይሸከም፡ ይከተለኝም። ም፡ ፲፡ ፴፰።

፳፭፡ ነፍሱን፡ ማዳን፡ የሚወድ፡ ይጥላታልና። ነፍሱንም፡ የጣለ፡ ስለኔ፡ ያገኛታል።

፳፮፡ ለሰው፡ምን፡ ይጠቀመዋል፡ ዓለሙን፡ሁሉ፡ ቢያተርፍ፡ነፍሱን፡ግን፡ ቢያጐድል። ወይስ፡ ምን፡ ይሰጣል፡ ሰው፡የነፍሱን፡ቤዛ።

፳፯፡ የሰው፡ ልጅ፡ ይመጣልና፡ ባባቱ፡ ክብር፡ ከመልክተኞቹ፡ጋራ። የዚያን፡ ጊዜም፡ ለሁሉ፡ ፍዳውን፡ ይሰጣል፡ እንደ፡ ስራው። ሮሜ፡ ፪፡ ፮።

፳፰፡ እውነት፡ እላችኋለሁ። ከዚህ፡ የቆሙ፡ ሰዎች፡ አሉ፡ ሞትን፡ የማይቀምሱት፡ የሰው፡ ልጅ፡ በመንግሥቱ፡ ሲመጣ፡ እስኪያዩ፡ ድረስ። ም፡ ፲፡ ፳፫።

## ምዕራፍ፡ ፲፯፡

፩፡ ከስድስት፡ ቀንም፡ በኋላ፡ የሱስ፡ ጴጥሮስን፡ ያዕቆብንም፡ ዮሐንስንም፡ ወንድሙን፡ ይዞዋቸው፡ ወደ፡ ረጅም፡ ተራራ፡ ወጣ፡ ለብቻቸው።
ማር፡ ፱፡ ፪፡—፲፫። ሉቃ፡ ፱፡ ፳፰፡—፴፮።

፪፡ በፊታቸውም፡ ተለወጠ። ፊቱም፡ እንደ፡ ፀሐይ፡ አበራ፡ ልብሱም፡ እንደ፡ ብርሃን፡ ነጭ፡ ሆነ።
፪፡ ጴጥ፡ ፩፡ ፲፮፡ ፲፯።

፫፡ እነሆም፡ ሙሴና፡ ኤልያስ፡ ለርሳቸው፡ ታዩ፡ ከርሱ፡ ጋራ፡ ሲናገሩ። ማል፡ ፬፡ ፬፡ ፭።

፬፡ ጴጥሮስም፡ መለሰ፡ የሱስንም፡ አለ። አቤቱ፡ ከዚህ፡ ብንቀመጥ፡ ለኛ፡ መልካም፡ ነው። ብትሻም፡ ከዚህ፡ ሦስት፡ ደስ፡ እንስራ። አንዱን፡ ላንተ፡ አንዱንም፡ ለሙሴ፡ አንዱንም፡ ለኤልያስ።

፭፡ እርሱም፡ ይህነን፡ ሲናገር፡ እነሆ፡ የበራ፡ ደመና፡ መጣና፡ ሰወራቸው። ድምፅም፡ ከደመና፡ መጣ፡ እንዲህ፡ ሲል። *ይህ፡ ነው፡ የምወደው፡ ልጄ፡ በርሱ፡ ደስ፡ የሚለኝ። እርሱን፡ ስሙት። *ም፡ ፫፡ ፲፯።
ዘዳግ፡ ፲፰፡ ፲፭፡—፲፱።

፮፡ ደቀ፡ መዛሙርቱም፡ በሰሙ፡ ጊዜ፡ በግምባራቸው፡ ወደቁ፡ እጅግም፡ ፈሩ።

፯፡ የሱስም፡ ወደርሳቸው፡ መጥቶ፡ ዳሰሳቸው፡ አለም። ተነሡ፡ አትፍሩ። ዳን፡ ፰፡ ፲፰።

፰፡ ዓይናቸውንም፡ አነሡ፡ ማንንም፡ አላዩም፡ የሱስን፡ ብቻ፡ እንጂ።

፱፡ ከተራራም፡ በወረዱ፡ ጊዜ፡ የሱስ፡ እንዲህ፡ ሲል፡ አዘዛቸው። ያያችሁትን፡ *ለማንም፡ አትናገሩ፡ የሰው፡ ልጅ፡ ከሙታን፡ እስኪነሣ፡ ድረስ። *ም፡ ፲፮፡ ፳።

፲፡ ደቀ፡ መዛሙርቱም፡ እንዲህ፡ ሲሉ፡ ጠየቁት። ለምን፡ ይላሉ፡ ጻፎች፡ *ኤልያስ፡ አስቀድሞ፡ ይመጣ፡ ዘንድ፡ እንዲገባው። ም፡ ፲፩፡ ፲፬። ማል፡ ፬፡ ፭።

፲፩፡ የሱስም፡ መልሶ፡ አላቸው፡ ኤልያስ፡ አስቀድሞ፡ ይመጣል፡ ሁሉንም፡ ያቀናል። ዮሐዋ፡ ፫፡ ፳፩።

፲፪፡ እላችሁማለሁ፡ ኤልያስ፡ ፈጽሞ፡ መጣ። አላወቁትምም፡ የወደዱትን፡ ሁሉ፡ *አደረጉበት፡ እንጂ። እንዲሁም፡ ደግሞ፡ የሰው፡ ልጅ፡ ከርሳቸው፡ መከራ፡ ይቀበል፡ ዘንድ፡ ጊዜ፡ አለው። *ም፡ ፲፬፡ ፱፡—፲፪።

፲፫፡ ከዚያ፡ ወዲያም፡ ደቀ፡ መዛሙርቱ፡ አወቁ፡ ስለ፡ መጥምቁ፡ ስለ፡ ዮሐንስ፡ እንደ፡ ተናገረ።
ሉቃ፡ ፩፡ ፲፯።

፲፬፡ ወደ፡ አሕዛብም፡ በደረሱ፡ ጊዜ፡ ሰው፡ ወደርሱ፡ መጣ፡ ለርሱ፡ በጕልበቱ፡ ኢየሰገደ።
ማር፡ ፱፡ ፲፬፡—፲፱። ሉቃ፡ ፱፡ ፴፯፡—፵፪።

፲፭፡ ኢያለም። አቤቱ፡ ልጄን፡ ማረው። በየወሩ፡ መጀመርያ፡ በምታወድቅ፡ በሽታ፡ ተይዞ፡ እጅግ፡ ይሣቀያልና። ብዙ፡ ጊዜም፡ በሳት፡ ይወድቃል፡ ብዙም፡ ጊዜ፡ በውኃ።

፲፮፡ ወደ፡ ደቀ፡ መዛሙርትህም፡ ወሰድሁት፡ ሊፈውሱትም፡ አልቻሉም።

፲፯፡ የሱስም፡ መለሰ፡ እንዲህም፡ አለ። አንች፡ ያላመነች፡ ትውልድ፡ የምትጠራጠርም። እስከ፡ መቼ፡ ከላንት፡ ጋራ፡ እኖራለሁ። እስከ፡ መቼስ፡ እታገሣችኋለሁ። ወደዚህ፡ ወደኔ፡ አምጡት።

፲፰፡ የሱስም፡ ተቈጣው፡ ሰይጣኑም፡ ከርሱ፡ ወጣ። ብላቴናውም፡ ደነ፡ ከዚያች፡ ሰዓት።

፲፱፡ በዚያን፡ ጊዜ፡ ደቀ፡ መዛሙርቱ፡ ወደ፡ የሱስ፡ ለብቻቸው፡ መጡ፡ አሉትም። ስለ፡ ምን፡ እኛ፡ አልቻልነም፡ ልናወጣው። ም፡ ፲፡ ፩።

፳፡ የሱስም፡ አላቸው። ካለማመናችሁ፡ የተነሣ። እውነት፡ እላችኋለሁ። *የሰናፍጭ፡ ቅንጣት፡ ያህል፡ ሃይማኖት፡ ቢኖራችሁ፡ ይህነን፡ ተራራ፡ ከዚህ፡ ወደዚያ፡ ተነሣ፡ ብትሉት፡ ይነሣል። የሚሳናችሁም፡ የለም። *ም፡ ፳፩፡ ፳፩። ዘካ፡ ፬፡ ፯። ሉቃ፡ ፲፯፡ ፲፮።

፳፩፤ እንዲህ፡ ያለ፡ ኢይነት፡ ግን፡ አይወጣም፡ በጾምና፡ በጸሎት፡ እንጂ። ማር፡ ፱፡ ፴፤—፴፪።
ሉቃ፡ ፱፡ ፵፫፤—፵፭።

፳፪፤ በገሊላም፡ሲመላለሱ፡ የሱስ፡ አላቸው። የሰው፡ ልጅ፡ በሰው፡ እጅ፡ይወድቅ፡ ዘንድ፡ጊዜ፡አለው። ም፡ ፲፮፡ ፳፩።

፳፫፤ ይገድሉታልም፡በሦስተኛውም፡ቀን፡ይነሣል። እርሳቸውም፡ እጅግ፡ አዘኑ።

፳፬፤ ወደ፡ ቅፍርናሆምም፡በደረሱ፡ጊዜ፡ ግብር፡ የሚወስዱ፡ ወደ፡ ጴጥሮስ፡ መጡ፡ አሉትም። መምህራችሁስ፡ *ግብር፡ አይሰጥምን። *ዘፀአ፡ ፴፡ ፲፫።

፳፭፤ እርሱም፡ አለ፡ አዎን። ወደ፡ ቤትም፡ በገባ፡ ጊዜ፡ የሱስ፡ አስቀድሞ፡ አለው። ምን፡ ይመስልሃል፡ ሲሞን፡ ሆይ። የምድር፡ ነገሥታት፡ከማን፡ግብር፡ ዕድስ፡ ይወስዳሉ። ከልጆቻቸው፡ ወይስ፡ ከሌሎች።

፳፮፤ ጴጥሮስም፡ አለው፡ ከሌሎች። አለው፡ የሱስ። እንኪያስ. ልጆቻቸው፡ ጌቶች፡ ናቸው።

፳፯፤ ነገር፡ ግን፡ እንዳናሰናክላቸው። ወደ፡ ባሕር፡ ሒድ፡ መቃጥንም፡ ጣል፡በፊት፡ የወጣውንም፡ዓሣ፡ ውሰደው። አፉንም፡ ክፈት፡ በርሱም፡ አራት፡ ድሪም፡ ታገኛለህ፡ ወስደኽም፡ ስለኔና፡ ስላንተ፡ ስጣቸው። ፩፡ ቆር፡ ፰፡ ፱። ሮሜ፡ ፲፫፡ ፯። ሉቃ፡ ፳፫፡ ፪።

## ምዕራፍ፡ ፲፰፤

፩፤ በዚያች፡ ሰዓት፡ ጊዜ፡ ደቀ፡ መዛሙርቱ፡ ወደ፡ የሱስ፡መጡ፡እንዲህ፡ሲሉ። በመንግሥተ፡ሰማያት፡ የሚበልጥ፡ ማነው። ማር፡ ፱፡ ፴፫፤—፴፯።
ሉቃ፡ ፱፡ ፵፮፤—፶።

፪፤ የሱሰም፡ ሕፃን፡ ጸራ፡ በመካከላቸውም፡ አቀመው።

፫፤ አለም። እውነት፡ እላችኋለሁ። ካልተመለሳችሁ፡ እንደ፡ ሕፃናትም፡ ካልሆናችሁ፡ወደ፡ መንግሥት፡ ሰማያት፡አትገቡም። ም፡ ፲፱፡ ፲፬።

፬፤ እንደዚህም፡ ሕፃን፡ ራሱን፡ ያዋረደ፡ እርሱ፡ ነው፡ በመንግሥተ፡ ሰማያት፡ የሚበልጥ።

፭፤ እንዲህ፡ያለም፡ ሕፃን፡ በስሜ፡ የተቀበለ፡ እኔን፡ ይቀበላል። ም፡ ፲፡ ፵።

፮፤ ከለዚህም፡ ከታናሾች፡ በኔ፡ከሚያምኑት፡ አንዱን፡ ያሰናከለ፡ የወፍጮ፡ድንጊያ፡ ባንገቱ፡ ታሥሮ፡ ወደ፡ ጥልቅ፡ ባሕር፡ መሥጠም፡ ይሻለዋል።
ኤር፡ ፶፩፡ ፷፫። ሉቃ፡ ፲፯፡ ፩፡ ፪። ሮሜ፡ ፲፬፡ ፲፫።

፯፤ ወዮለት፡ ለዓለም፡ስለ፡ መሰናከያ። የግድ፡ መሰናከያ፡ ትመጣ፡ዘንድ፡ ጊዜ፡ አላትና። ነገር፡ ግን፡ወዮለት፡ ለዚያ፡ ሰው፡ በርሱ፡ ምክንያት፡ መሰናከያ፡ የምትመጣ።

፰፤ እጅህም፡አግርህ፡ብታስትህ፡ቊርጠህ፡ካንተ፡ ጣላት። ይሻልሃልና፡ወደ፡ሕይወት፡ብትገባ፡ አንካሳ፡ ወይም፡ጉንድሽ፡ ሁነህ፡ ሁለት፡ እጅ፡ ወይም፡ሁለት፡ እግር፡ ኑርህ፡ ወደ፡ ዘላለም፡ እሳት፡ ክትጣል።
ም፡ ፭፡ ፳፱፡ ፴።

፱፤ ዓይንህም፡ ብታስትህ፡ አውልቀህ፡ ጣላት። ይሻልሃልና፡ አንድ፡ ዓይን፡ ወደ፡ ሕይወት፡ ብትገባ፡ ሁለት፡ ዓይን፡ ኑርህ፡ ወደ፡ እሳት፡ ገሃነም፡ ክትጣል።

፲፤ እዩ፡ ከለዚህ፡ ከታናሾች፡አንዱን፡እንዳትንቁ። እላችኋለሁና፡ *መላእክተቻቸው፡ በሰማዮች፡ሁለጊዜ፡ የሰማዩን፡ያባቴን፡ፊት፡እንዲያዩ። *ዕብ፡ ፩፡ ፲፬።

፲፩፤ የሰው፡ ልጅ፡ መጥትዋልና፡ የጠፋውን፡ ለማደን። ም፡ ፱፡ ፲፫። ሉቃ፡ ፲፱፡ ፲። ፩፡ ጢሞ፡ ፩፡ ፲፭።

፲፪፤ ምን፡ ትላላችሁ። ለሰው፡መቶ፡ በግ፡ቢኖረው፡ ከርሳቸውም፡ አንዱ፡ ቢጠፋ። ዘጠና፡ ዘጠኙን፡ በተራራ፡ ትቶ፡ የጠፋውን፡ ለመሻት፡ አይሔድምን።
ኤር፡ ፶፡ ፮። ሕዝ፡ ፴፬፡ ፮፡ ፲፩፡ ፲፪። ሉቃ፡ ፲፭፡ ፬፤—፯።

፲፫፤ ቢያገኘውም፡ እውነት፡ እላችኋለሁ፡ በርሱ፡ ደስ፡እንዲለው፡ካልጠፋቱ፡ ከዘጠና፡ዘጠኙ፡ይልቅ።

፲፬፤ እንዲሁም፡ በሰማይ፡ ያለው፡ ያባታችሁ፡ ፈቃድ፡አይደለውም፡ከለዚህ፡ከታናሾች፡አንዱ፡ይጠፋ፡ ዘንድ።

፲፭፤ ወንድምህ፡ ቢበድልህ፡ ሒድ፡ አንተም፡ ከርሱ፡ ጋራ፡ሁነህ፡ ብቻውን፡ምከረው። ቢሰማህ፡ ወንድምህን፡ጠቀምኸው። ዘሌዋ፡ ፲፱፡ ፲፯። ገላት፡ ፮፡ ፩።

፲፮፤ ባይሰማህም፡ደግመህ፡ ካንተ፡ ጋራ፡አንድ፡ ወይም፡ ሁለት፡ ውሰድ። በሁለትና፡ በሦስት፡ ምስክር፡ አፍ፡ ነገር፡ ሁሉ፡ ትጸና፡ ዘንድ።

፲፯፤ እርሳቸውንም፡ ባይሰማ፡ ለቤተ፡ክርስቲያን፡ ንገራት። ደግሞም፡ ቤተ፡ ክርስቲያንን፡ ባይሰማት፡ *ካረማዊና፡ ካጣሪ፡ ቊጠረው። *፩፡ ቆሮ፡ ፭፡ ፲፫።

፲፰፤ እውነት፡ እላችኋለሁ። በምድር፡ ያሠራችሁት፡ ሁሉ፡ በሰማይ፡ የታሠረ፡ ይሆናል። በምድርም፡ የፈታችሁት፡ በሰማይ፡ የተፈታ፡ ይሆናል።
ም፡ ፲፮፡ ፲፱። ዮሐ፡ ፳፡ ፳፫።

፲፱፤ ደግሞ፡ እላችኋለሁ። ከላንተ፡ ሁለቱ፡ በምድር፡ አንድ፡ ቢሆኑ፡ በልመናቸው፡ የለመኑት፡ሁሉ፡ይሆንላቸዋል፡ ከሰማዩ፡ ካባቴ፡ ዘንድ። ማር፡ ፩፡ ፳፬።

፳፤ ሁለት፡ ሁነው፡ ወይም፡ ሦስት፡ ሁነው፡ በስሜ፡ ወደ፡ ተከማቹበት፡ ከዚያ፡ በመካከላቸው፡ እሆናለሁና። ም፡ ፳፰፡ ፳።

፳፩፤ የዚያን፡ ጊዜ፡ ጴጥሮስ፡ ወደርሱ፡ ቀረበ፡ አለም። አቤቱ፡ወንድሜ፡ቢበድለኝ፡ ስንት፡ ጊዜ፡ ይቅር፡ ልበለው። ሰባትን፡ጊዜ። ሉቃ፡ ፲፯፡ ፬።

፳፪፤ የሱስም፡ አለው። ሰባት፡ ጊዜ፡ አልልህም። ሰባ፡ ጊዜ፡ ሰባት፡ እንጂ። ዘፍ፡ ፬፡ ፳፬።

፳፫፤ ስለዚህ፡ መንግሥተ፡ሰማያት፡ ንጉሥ፡ሰው፡ ትመስላለች፡ባሮቹን፡ይቈጠራቸው፡ዘንድ፡የወደደ።

፳፬፤ መቈጠርም፡ ከርሳቸው፡ ጋራ፡በጀመረ፡ ጊዜ፡ አንዱን፡ ወደርሱ፡አመጡት፡አሥር፡ሺህ፡ምዝምዝ፡ ያለበት።

፳፭፡ የሚከፍለውም፡ ባይኖረው፡ ጌታው፡አዘዘ፡ እርሱ፡ ይሸጥ፡ ዘንድ፡ ምሽቱም፡ልጆቹም፡ ያለውም፡ ሁሉ፡ እስኪከፈል፡ ድረስ። ፪፡ ነገሥ፡ ፬፡ ፩።

፳፮፡ ያም፡ ባርያ፡ ወድቀ፡ሰገደለትም፡ እንዲህ፡ ሲል። አቤቱ፡ ጥቂት፡ ታገሠኝ፡ ከብትህንም፡ ሁሉ፡ እከፍልሃለሁ።

፳፯፡ የዚያም፡ የባርያው፡ ጌታ፡አዘነለት። ተወውም፡ ደግሞም፡ ዕዳውን፡ ተወለት። ሉቃ፡ ፯፡ ፵፪።

፳፰፡ ያም፡ ባርያ፡ ወጥቶ፡ ከባልንጀሮቹ፡ ከባሮች፡ አንዱን፡ አገኘ፡ መቶ፡ ወቄት፡ ያለበትን። ያዘውም፡ አነቀውም፡ እንዲህ፡ ሲል። በላይህ፡ ያለውን፡ ከብቴን፡ ስጠኝ።

፳፱፡ ባልንጀራውም፡እንደርሱ፡ያለው፡ ባርያ፡ በግሩ፡ በታች፡ ወድቀ፡ ለመነውም፡እንዲህ፡ ሲል። ታገሠኝ፡ እኔን፡ ከብትህን፡ ሁሉ፡ እከፍልሃለሁ።

፴፡ እርሱ፡ ግን፡እምቢ፡አለው፡ወስዶም፡ወደ፡ግዞት፡ አገባው፡ ዕዳውን፡ እስኪከፍል፡ ድረስ።

፴፩፡ ባሮችም፡ ባልንጀሮቹ፡ አይተው፡ እጅግ፡ አዘኑ። መጥተውም፡የሆነውን፡ሁሉ፡ለጌታቸው፡ነገሩት።

፴፪፡ ከዚያ፡ ወዲያም፡ ጌታው፡ጸራውና፡አለው። አንተ፡ ክፉ፡ ባርያ። ያነን፡ ሁሉ፡ ዕዳ፡ ተውሁልህ፡ስለ፡ ለመነህኝ።

፴፫፡ ላንተ፡ አይገባህምን፡ ደግሞ፡ ባርያውን፡ ባልንጀራህን፡ ትምር፡ ዘንድ፡ እኔ፡ አንተን፡ እንደ፡ ማርሁህ። ቆላ፡ ፫፡ ፲፫።

፴፬፡ ጌታውም፡ ተቈጣና፡ለሚሣቅዩት፡አሳልፎ፡ ሰጠው፡ ያለበትን፡ ሁሉ፡ *እስኪከፍል፡ ድረስ።

*ም፡ ፭፡ ፳፮። ያዕ፡ ፪፡ ፲፫።

፴፭፡ እንዲሁም፡ ደግሞ፡ የሰማዩ፡ አባቴ፡ ያደርግባችኋል፡ ከላንተ፡ ወገን፡ ሁሉ፡ ኢያንዳንዱ፡ የወንድሙን፡ ኃጢአት፡ ከልቡ፡ ይቅር፡ ካላለ።

ም፡ ፮፡ ፲፬፡ ፲፭።

ምዕራፍ፡ ፲፱፡

፩፡ የሱስም፡ ይህነን፡ ነገር፡ በፈጸመ፡ ጊዜ፡ ከገሊላ፡ ሔደ፡ ወደ፡ ይሁዳም፡ አገር፡ መጣ፡ ወደ፡ ዮርዳኖስ፡ ማዶ። ማር፡ ፲፡ ፩፡—፲፪።

፪፡ ብዙ፡ አሕዛብም፡ ተከተሉት፡ ከዚያም፡ፈወሳቸው።

፫፡ ፈሪሳውያንም፡ ወደርሱ፡ መጡ፡ሲፈትኑት፡ ሲሉትም። ለሰው፡ ይገባልን፡ ምሽቱን፡ ይፈታ፡ ዘንድ፡ በምክንያት፡ ሁሉ። ዘዳግ፡ ፳፬፡ ፩።

፬፡ እርሱ፡ ግን፡ መለሰ፡ አላቸውም። አላነበባችሁምን፡ የፈጠረ፡ አስቀድሞ፡ ወንድና፡ሴት፡ አድርጎ፡ እንደፈጠራቸው። ዘፍጥ፡ ፩፡ ፳፯።

፭፡ አለም። ስለዚህ፡ሰው፡አባቱንና፡ እናቱን፡ ይተዋል፡ ምሽቱንም፡ ይከተላል፡ ሁለቱም፡ አንድ፡ ሥጋ፡ ይሆናሉ። ዘፍጥ፡ ፪፡ ፳፬።

፮፡ ገና፡ ሁለትም፡ አይደሉም፡ አንድ፡ያደረገውን፡ *ሰው፡ አይለየው። *፩፡ ቆሮ፡ ፯፡ ፲።

፯፡ አሉትም። እንኪያስ፡ ለምን፡ ሙሴ፡ አዘዘ፡ የመፋቻዋን፡ መጽፉ፡ሰጥተው፡ ይፈትዋት፡ ዘንድ።

ም፡ ፭፡ ፴፩፡ ፴፪።

፰፡ እርሱም፡አላቸው። ሙሴስ፡ ስለ፡ ልባችሁ፡ ድንዳኔት፡ ምሽቶቻችሁን፡ ትፈቱ፡ ዘንድ፡ አዘዛችሁ። ከጥንት፡ ግን፡ እንዲህ፡ አልነበረም።

፱፡ እኔም፡ እላችኋለሁ። ምሽቱን፡ የፈታ፡ ሁሉ፡ ያለ፡ ዝሙት፡ ምክንያት፡ ሌላዪቱንም፡ ያገባ፡ ፈጽሞ፡ አመነዘረ። የተፈታችውንም፡ ያገባ፡ ፈጽሞ፡ አመነዘረ። *ሚል፡ ፪፡ ፲፬፡—፲፯። ዘዳግ፡ ፳፬፡ ፪።

፲፡ ደቀ፡ መዛሙርቱም፡ አሉት። እንዲህስ፡ ሰው፡ ቢሁን፡ ከምሽቱ፡ ጋራ፡ ቢያገባ፡ መልካም፡አይደለውም። ፩፡ ቆሮ፡ ፯፡ ፩።

፲፩፡ እርሱም፡አላቸው።ይህ፡ነገር፡ለሰዎች፡ሁሉ፡አይቻላቸውም፡ለተሰጣቸው፡በቀር። ፩፡ቆሮ፡፯፡፯፡፲፯፡

፲፪፡ ጃንደረባ፡ሁነው፡ ከናቶቻቸው፡ የተዋለዱ፡ ሰዎች፡ አሉና። ሌሎችንም፡ ሰዎች፡ ሰልበው፡ ጃንደረቦች፡ አደረግዋቸው። ስለ፡ መንግሥተ፡ ሰማያትም፡ ሰውነታቸውን፡ጃንደረባ፡ ያደረጉ፡ሰዎች፡አሉ። ማስተዋል፡ ግን፡ የሚችል፡ ያስተውል። ፩፡ ቆሮ፡ ፯፡ ፴፪።

፲፫፡ በዚያን፡ ጊዜ፡ ሕፃናትን፡ ወደርሱ፡ አመጡ፡ እጁን፡ይጭንባቸው፡ይጸልይላቸውም፡ዘንድ። ደቀ፡ መዛሙርቱም፡ተቈጥዋቸው። ማር፡ ፲፡ ፲፫፡—፴፩።

ሉቃ፡ ፲፰፡ ፲፭፡—፲፯።

፲፬፡ የሱስም፡ አለ። ሕፃናትን፡ ተው፡ አትከልክሉዋቸውም፡ወደኔ፡ ይመጡ፡ ዘንድ። መንግሥተ፡ ሰማያት፡ እንደለዚህ፡ ላሉት፡ ናትና። ም፡ ፲፰፡ ፪።

፲፭፡ እጁንም፡ ጫነባቸውና፡ ከዚያ፡ ሔደ።

፲፮፡ እነሆም፡ አንድ፡ ሰው፡ ወደርሱ፡ መጣና፡ እንዲህ፡አለው። አንተ፡ቸሩ፡ መምህር። ከበጐነት፡ ምንድር፡ ላድርግ፡የዘላለም፡ሕይወት፡ ትሆንልኝ፡ ዘንድ። ሉቃ፡ ፲፰፡ ፲፰፡—፴።

፲፯፡ እርሱም፡ አለው። ለምን፡ ቸር፡ ትለኛለህ። ማንም፡ ቸር፡ አይደለውም፡ካንዱ፡በቀር፡ እርሱም፡ እግዚአብሔር። ወደ፡*ሕይወት፡ ግን፡ ትገባ፡ ዘንድ፡ ብትወድ፡ትእዛዛትን፡ጠብቅ። *ሉቃ፡ ፲፡ ፳፮፡—፳፰።

፲፰፡ እርሱም፡ አለው፡ ማናቸው። የሱስም፡ አለው። አትግደል፡ አትስረቅ፡ አታመንዝር፡ ባሰት፡ አትመሰክር።

፲፱፡ አባትህን፡ እናትህንም፡ አክብር፡ *ባልንጀራህን፡ ውደድ፡ እንደ፡ ነፍስህ። *ዘሌዋ፡ ፲፱፡ ፲፰።

፳፡ ያም፡ ጐበዝ፡ አለው። ይህነን፡ ሁሉ፡ ከሕፃንነቴ፡ ጀምሬ፡ ጠብቅሁ። ደግሞ፡ ሌላ፡ ምን፡ ይጐድልብኛል።

፳፩፡ የሱስም፡ አለው። ፍጹም፡ ትሆን፡ ዘንድ፡ ብትወድስ። ሒድ፡ ያለህንም፡ ሁሉ፡ ሽጠህ፡ ለድኆች፡ ስጥ። ከብትም፡ በሰማይ፡ ተከማችቶ፡ ይቈይሃል። መጥተህም፡ ተከተለኝ። ም፡ ፮፡ ፳።

ሉቃ፡ ፲፪፡ ፴፫።

፳፪፤ ጕበዙም፡ ነገሩን፡ በሰማ፡ ጊዜ፡ አዝኖ፡ ሔደ፡ ብዙ፡ ከብት፡ ነበረውና። መዝ፡ ፶፪፡ ፲፩፡፡

፳፫፤ የሱስም፡ለደቀ፡ መዛሙርቱ፡አለ። እውነት፡ እላችኋለሁ። ባለ፡ጸጋ፡ ወደ፡ መንግሥተ፡ ሰማያት፡ ይገባ፡ ዘንድ፡ ጭንቅ፡ ነው። ፩፡ ጢሞ፡ ፮፡ ፱፡ ፲፯፡፡

፳፬፤ ደግሞ፡ እላችኋለሁ። ግመል፡ በመርፌ፡ቀዳዳ፡ ይገባ፡ ዘንድ፡ አያስቸግርም፡ ባለ፡ ጸጋ፡ ወደ፡ እግዚአብሔር፡ መንግሥት፡ ኪገባ።

፳፭፤ ደቀ፡ መዛሙርቱም፡ ሰምተው፡ እጅግ፡ አደነቁ፡እንደህ፡ ሲሉ። ማነው፡እንኪያ፡ የሚድን።

፳፮፤ የሱስም፡ አየና፡ አላቸው። በሰው፡ ዘንድ፡ ይህ፡ አይቻልም። በእግዚአብሔር፡ ዘንድ፡ ግን፡ ሁሉ፡ ይቻላል።

፳፯፤ የዚያን፡ጊዜም፡መለሰ፡ጴጥሮስ፡እንደህም፡ አለው። እነሆ፡እኛ፡ሁሉን፡ትተን፡ተከተልነህ። ምን፡ እናገኝ፡ ይሆን።

፳፰፤ የሱስም፡ አላቸው። እውነት፡ እላችኋለሁ። እላንተስ፡ የተከተላችሁኝ፡ በሐዲስ፡ ዓለም፡የሰው፡ ልጅ፡ በምስጋናው፡ ዙፋን፡ በተቀመጠ፡ ጊዜ። እላንተ፡ ደግሞ፡ ባሥራ፡ ሁለት፡ ዙፋን፡ ትቀመጣላችሁ፡ ባሥራ፡ሁለቱም፡በእሥራኤል፡ ነገድ፡ትፈርዳላችሁ። መዝ፡ ፻፳፪፡ ፭፡፡ ም፡ ፲፮፡ ፲፩፡፡ ሉቃ፡ ፳፪፡ ፴፡፡

፳፱፤ ቤትንም፡ የተወ፡ሁሉ፡ ወንድሞችንም፡ እኅቶችንም፡ አባትንም፡ እናትንም፡ ምሽትንም፡ ልጆችንም፡ እርሻንም፡ ስለ፡ ስሜ። መቶ፡ ዕጽፍ፡ ይወስዳል፡ የዘላለሙንም፡ ሕይወት፡ ይወርሳል። ዕብ፡ ፲፡ ፴፬፡፡

፴፤ ብዙ፡ የፊተኞች፡ ግን፡ በኋላ፡ ይሆናሉ፡ *የኋለኞቹም፡ በፊት። *ም፡ ፳፡ ፲፮፡፡ ሉቃ፡ ፲፫፡ ፴፡፡

ምዕራፍ፡ ፳፤

፩፤ መንግሥተ፡ ሰማያት፡ ባለ፡ ቤትን፡ ሰው፡ ትመስላለች፡ ማልዶ፡ የወጣን፡ ሰራተኞች፡ *ለወይኑ፡ ስፍራ፡ ሊሰማማ። *ም፡ ፳፩፡ ፴፫፡፡

፪፤ ሰራተኞችንም፡ ተሰማምቶ፡ በቀን፡ ድሪም፡ ሊሰጣቸው፡ ወደ፡ ወይኑ፡ ስፍራ፡ ሰደዳቸው።

፫፤ በሶስተ፡ሰዓት፡ጊዜም፡ወጣ፡ ሌሎችንም፡ አየ፡ ባደባባይ፡ ቁመው፡ ተግባር፡ ፈትተው።

፬፤ እሊያንም፡ አለ። እላንትም፡ ወደ፡ወይኑ፡ስፍራ፡ ሒዱ። እኔም፡ የሚገባችሁን፡ እሰጣችኋለሁ።

፭፤ እርሳቸውም፡ ሔዱ። ደግሞም፡ወጣ፡በስድስተ፡ ሰዓት፡ ጊዜ፡ በዘጠኝም፡ እንደሁም፡ አደረገ።

፮፤ ባሥራ፡ አንደኛውም፡ ሰዓት፡ ጊዜ፡ ወጣ፡ ሌሎችንም፡ ቁመው፡አገኘ፡ ተግባር፡ ፈትተው። አላቸውም። ምን፡ ሁናችሁ፡ ከዚህ፡ ቀኑን፡ ሁሉ፡ቁማችኋል፡ ተግባር፡ ፈታችሁ።

፯፤ እርሳቸውም፡ አሉት፡ ማንም፡ የሚገዛን፡ ብናጣ። እርሱም፡ አላቸው። እላንትም፡ ደግሞ፡ ወደ፡ ወይኑ፡ቦታ፡ ሒዱ፡ የሚገባችሁንም፡ትወስዳላችሁ።

፰፤ በመሸም፡ ጊዜ፡ የወይኑ፡ ባለ፡ ቤት፡ መጋቢውን፡ አለ፡ ሰራተኞችን፡ ጽራ፡ ዋጋቸውንም፡ ስጣቸው፡ ከኋለኞች፡ ጀምረህ፡ እስከ፡ ፊተኞች።

፱፤ በመጡም፡ ጊዜ፡ባሥራ፡ አንደኛዪቱ፡ ሰዓት፡ ጊዜ፡ የገዛቸው፡ ኢየራሳቸው፡ ድሪም፡ ወሰዱ።

፲፤ የፊተኞችም፡ በመጡ፡ ጊዜ፡ እጅግ፡ የሚወስዱ፡ መሰላቸው። እርሳቸውም፡ ደግሞ፡ አንድ፡ ድሪም፡ ኢየራሳቸው፡ ወሰዱ።

፲፩፤ ከወሰዱም፡ በኋላ፡ በባለ፡ ቤቱ፡ አንጐረጐሩበት። ሉቃ፡ ፲፭፡ ፳፱፡፡

፲፪፤ እንደህ፡ሲሉ። እለዚህ፡ የኋለኞቹ፡ አንዲት፡ ሰዓት፡ ሰሩ፡ ከኛ፡ ጋራም፡ አስተካከልሃቸው፡ እኛ፡ የቀኑን፡ ድካም፡ የትኩሳቱንም፡ ጽናት፡ የተሸከምነ። ዘፍጥ፡ ፴፩፡ ፵፡፡

፲፫፤ እርሱ፡ ግን፡ መለሰ፡ ከርሳቸውም፡አንዱን፡ አለ። ወዳጄ፡ ሆይ፡ አልበደልሁህም። ባንድ፡ ድሪም፡ አልተሰማማህኝምን።

፲፬፤ ገንዘብህን፡ ይዘህ፡ ሒድ። እኔ፡ለዚያም፡ ለኋለኛው፡ እንዳንተ፡ እሰጠው፡ ዘንድ፡ እወዳለሁ።

፲፭፤*ወይስ፡አይገባኝምን፡የወደድሁትን፡አደርግ፡ ዘንድ፡ በከብቴ። ወይስ፡ ዓይንህም፡ ምቀኛ፡ ናት፡ እኔ፡ ቸር፡ ሰለ፡ ሆንሁ። *ሮሜ፡ ፱፡ ፲፮፡—፳፩፡፡

፲፮፤ እንደሁ፡*የኋለኞች፡የፊተኞች፡ይሆናሉ፡የፊተኞችም፡ የኋለኞች። የተጸሩ፡ እጅግ፡ ናቸውና፡ የተመረጡ፡ ግን፡ ጥቂት። *ም፡ ፲፱፡ ፴፡፡

፲፯፤ የሱስም፡ ወደ፡ የሩሳሌም፡ ሲወጣ፡ አሥራ፡ ሁለቱን፡ ደቀ፡ መዛሙርቱን፡ በመንገድ፡ለብቻቸው፡ ወሰደ፡ አላቸውም። ማር፡ ፲፡ ፴፪፡—፴፬፡፡ ሉቃ፡ ፲፰፡ ፴፩፡—፴፫፡፡

፲፰፤ እነሆ፡እኛ፡ ወደ፡ የሩሳሌም፡ እንወጣለን፡ የሰው፡ ልጅም፡ ለካህናት፡ አለቆች፡ ለጻፎችም፡ ይሰጣል። የሞት፡ ፍርድም፡ ይፈርዱበታል። ሉቃ፡ ፲፮፡ ፳፩፡፡ ፲፯፡ ፳፪፡፡

፲፱፤ ለአሕዛብም፡ አሳልፎ፡ ይሰጡታል፡ ሊያፈዙበት፡ይገርፉትማል፡ይሰቅሉትማል።በሶስተኛውም፡ ቀን፡ ይነሣል።

፳፤ በዚያን፡ ጊዜ፡ *የዘብዴዎስ፡ የልጆቹ፡ እናት፡ ወደርሱ፡ መጠች፡ ከልጆቿዋ፡ ጋራ፡ ስትሰግድለት፡ ከርሱም፡ አንዳች፡ ስትሻ። ማር፡ ፲፡ ፴፭፡—፵፭፡፡ *ም፡ ፲፡ ፪፡፡

፳፩፤ እርሱም፡ አላት፡ምን፡ ትሻለሽ። እርስዋም፡ አለችው። በል፡ እንዲቀመጡ፡ እሌህ፡ ልጆቼ፡ አንደኛው፡ በቀኝህ፡ ሁለተኛውም፡ በግራህ፡ በመንግሥትህ። ም፡ ፲፱፡ ፳፰፡፡

፳፪፤ የሱስም፡መለሰ፡ አለም። የምትለምኑትን፡ አታውቁም። ትችላላችሁን፡እኔ፡ የምጠጣውን፡ *ጽዋውን፡ ትጠጡ፡ ዘንድ፡ ትጠመቁስ፡ አላችሁን፡ ተጥምቀቱን፡እኔ፡ የምጠመቀውን። አሉትም፡ እንችላለን። *ም፡ ፳፮፡ ፴፱፡፡ ዮሐ፡ ፲፰፡ ፲፩፡፡ ተሉቃ፡ ፲፪፡ ፶፡፡

፳፫፤ አላቸውም፡ ጽዋዬን፡ ትጠጣላችሁ፡ ጥምቀ

ቴንም፡ እኔ፡ የምጠመቀውን፡ ተጠመቃላችሁ። በቀ
ኜና፡ በግራዬ፡ መቀመጥ፡ግን፡ የምሰጠው፡የለኝም።
ለተዘጋጀላቸው፡ እንጂ፡ ካባቴ፡ ዘንድ።
ሮሜ፡ ፯፡ ፫።

፳፬፡ አሥሩም፡ ሰምተው፡ ሁለቱን፡ ወንድማማ
ች፡ ተቈጥዋቸው። ሉቃ፡ ፳፪፡ ፳፬፡—፳፯።

፳፭፡ የሱስም፡ ጸራቸው፡አለም። አወቃችሁ፡የአ
ሕዛብ፡ አለቆች፡እንዲገዝዋቸው፡ ታላቆቻቸውም፡
በላያቸው፡ እንዲሠለጠኑ። ሉቃ፡ ፳፪፡ ፳፭።

፳፮፡ ለላንተስ፡ እንደሁ፡አይሆንም። ነገር፡ግን፡ በ
ላያችሁ፡ታላቅ፡መሆን፡ የሚወድ፡ ሎሌ፡ ይሁናችሁ።

፳፯፡ በላንት፡ በፊት፡ ይሆን፡ ዘንድ፡ የወደደም፡
ስላንት፡ባርያ፡ ይሁናችሁ።

፳፰፡ የሰው፡ ልጅ፡ እንደልመጣ፡ ሊያገለግሉት፡
*ሊያገለግል፡እንጂ፡ነፍሱንም፡ሊሰጥ፡ለብዙ፡ †ቤዛ።
*ዮሐ፡ ፲፫፡ ፬፡—፲። ፊል፡ ፪፡ ፯። †፩፡ ጢሞ፡ ፪፡ ፮።

፳፱፡ ከዩሪኮም፡ በወጡ፡ ጊዜ፡ ብዙ፡ አሕዛብ፡ ተ
ከተሉት። ማር፡ ፲፡ ፵፮፡—፶፪።
ሉቃ፡ ፲፰፡ ፴፭፡—፵፫።

፴፡ ሁለት፡ ዕውሮችም፡ እነሆ፡ በመንገድ፡ ላይ፡ ተ
ቀምጠው፡ነበሩ። የሱስም፡ እንዲያርፍ፡ በሰሙ፡ ጊ
ዜ፡ ጮሁ፡ እንደሁ፡ ሲሉ። ማረን፡ አቤቱ፡ የዳዊት፡
ልጅ።

፴፩፡ የተሰበሰቡትም፡ገሠፅዋቸው፡ዝም፡ይሉ፡ዘ
ንድ። እርሳቸው፡ ግን፡ አብዝተው፡ ጮሁ፡ እንደሁ፡
ሲሉ። ማረን፡ አቤቱ፡ የዳዊት፡ ልጅ።

፴፪፡ የሱስም፡ ቆመ፡ ጸራቸውም፡ አለም። ምን፡
ትሻላችሁ፡ አደርግላችሁ፡ ዘንድ።

፴፫፡ አሉት፡ አቤቱ፡ዓይኖቻችን፡ ይከፈቱ፡ዘንድ።

፴፬፡ የሱስም፡ ራራላቸው፡ ዓይኖቻቸውንም፡ ዳ
ሰሰ። የዚያን፡ ጊዜውም፡ ዓይኖቻቸውንም፡ ዳሰሰ።
የዚያን፡ጊዜውም፡ዓይኖቻቸው፡አዩ፡ተከተሉትም።

## ምዕራፍ፡ ፳፩።

፩፡ ወደ፡ የሩሳሌምም፡ ቀርበው፡ ወደ፡ ቤትፋጌ፡
በመጡ፡ጊዜ፡ ወደ፡ ደብረ፡ዘይት፡ አጠገብ። የዚያን፡
ጊዜ፡ የሱስ፡ ሁለት፡ ከደቀ፡ መዛሙርቱ፡ ላከ።
ማር፡ ፲፩፡ ፲፡—፴፫። ሉቃ፡ ፲፱፡ ፳፱፡—፵፰።
ዮሐ፡ ፲፪፡ ፲፪፡—፲፯።

፪፡ እንደሁ፡ሲላቸው። በፊታችሁ፡ወደላቸው፡ አ
ገር፡ ሒዱ፡ የዚያን፡ ጊዜም፡ የታሠረች፡ አህያ፡ ታገኛ
ላችሁ፡ ውርንጫም፡ ከርስዋ፡ ጋራ። ፈትዋቸው፡ እር
ሳቸውንም፡ አምጡልኝ።

፫፡ ማንም፡ አንዳች፡ ቢላችሁ፡ በሉ፡ ጌታ፡ ይሻቸዋ
ል። እርሱም፡ አሁን፡ ይሰዳቸዋል። ም፡ ፳፯፡ ፲፭።

፬፡ ይህም፡ ሁሉ፡ የሆነ፡ ይፈጸም፡ዘንድ፡ ነው፡ በነ
ቢይ፡ የተባለው፡ እንደሁ፡ ሲል።

፭፡ ለፅዮን፡ *ልጅ፡ በልዋት። እነሆ፡ ንጉሥሽ፡ ወደ
ንቺ፡ ይመጣል፡ ተዋርዶ። ባህያ፡ ላይ፡ ተቀምጦ፡ በ
ውርንጫም፡ በጫነት፡ ከብት፡ ልጅ፡ላይ።
*ዘካ፡ ፱፡ ፱፡—፲፪።

፮፡ ደቀ፡ መዛሙርቱም፡ሒደው፡የሱስ፡ እንደዘዛ
ቸው፡ አደረጉ።

፯፡ አህያዪቱንና፡ ውርንጫዋንም፡ አመጡ። ልብ
ሳቸውንም፡ በላያቸው፡ ጫኑ፡ አስቀመጡትም።

፰፡ እጅግ፡ ብዙ፡ ሰዎችም፡ *ልብሳቸውን፡በመንገ
ድ፡ አነጸፉ። ሌሎችም፡ ከዛፍ፡ ጫፍ፡ ጫፉን፡ ቈርጠ
ው፡ አነጸፉ። *፪፡ ነገሥ፡ ፱፡ ፲፫።

፱፡ በፊቱም፡ የሚሔዱ፡ ሰዎች፡ የተከተሉትም፡
ጮሁ፡ እንደሁ፡ሲሉ። *ሆሳዕና፡ ለዳዊት፡ልጅ። በእግ
ዚአብሔር፡ ስም፡ የሚመጣ፡የተባረከ፡ነው። ሆሳዕ
ና፡ ከላይ። *መዝ፡ ፻፲፰፡ ፳፭፡ ፳፮።

፲፡ የሱስም፡ ወደ፡ የሩሳሌም፡ በገባ፡ ጊዜ፡ አገሪቱ፡
ሁሉዋ፡ ታወከች፡ ስትል፡ ማነው። ዮሐ፡ ፲፪፡ ፲፱።

፲፩፡ ሕዝብም፡አሉ። ይህ፡ነቢዩ፡የሱስ፡ነው፡የናዝሬ
ቱ፡ ከገሊላ፡ ወገን፡ የምትሆን።

፲፪፡ የሱስም፡ ወደ፡እግዚአብሔር፡ መቅደስ፡ ገባ፡
በቤተ፡ መቅደስም፡ የሚሸጡን፡የሚገዙንም፡ሁሉ፡
አወጣ። የሰራፎችንም፡ማዕድ፡የርግብ፡ሻጮችንም፡
ወንበር፡ ገለበጠ። ዮሐ፡ ፪፡ ፲፬።

፲፫፡ አላቸውም፡ የተጸፈ፡ ነው፡ *ቤቴ፡ የጸሎት፡ ቤ
ት፡ እንዲባል። እላንተ፡ ግን፡ †የሌቦች፡ ዋሻ፡ አደረጋ
ችሁት። *ኢሳ፡ ፶፮፡ ፯። †ኤር፡ ፯፡ ፲፩።

፲፬፡ ዕውሮች፡ አንካሶችም፡ ወደርሱ፡ መጡ፡ በመ
ቅደስ፡ ፈወሳቸውም።

፲፭፡ የካህናት፡ አለቆችና፡ ጻፎችም፡ የሰራውን፡
ተአምራት፡ ባዩ፡ ጊዜ፡ ሕፃናትም፡ በቤተ፡ መቅደስ፡
ሲጮሁ፡ ሲሉም። ሆሳዕና፡ ለዳዊት፡ልጅ፡ተቈጡ፡ አ
ሉትም።

፲፮፡ አትሰማምን፡ እሌህ፡ የሚሉትን። የሱስም፡
አላቸው፡ አዎን። ከቶ፡ አላነበባችሁምን፡ *ከልጆች፡
ከሕፃናትመ፡አፍ፡መስጋና፡አዘጋጀህ። *መዝ፡ ፰፡ ፫።

፲፯፡ ተዋቸውም፡ ከከተማም፡ ወደ፡ ሚያ፡ ወደ፡
ቢታንያ፡ ወጣ፡ ከዚያ፡ አደረ።

፲፰፡ በነጋውም፡ ወደ፡ ከተማ፡ ሲመለስ፡ ተራበ።

፲፱፡ በለስም፡ አየ፡ በመንገድ፡ ላይ፡ ወደርስዋም፡
መጣ፡ አንዳችም፡ አላገኘባትም፡ ከቅጠል፡ በቀር።
አላትም። ፍሬ፡ አይሁንብሽ፡ለዘላለም። የዚያን፡ ጊ
ዜውም፡ በለሲቱ፡ ደረቀች። ኢዮ፡ ፩፡ ፯።
ሕዝ፡ ፲፯፡ ፳፬። ዕብ፡ ፯፡ ፳።

፳፡ ደቀ፡ መዛሙርቱም፡ አይተው፡ተደነቁ፡እንደ
ሁ፡ ሲሉ። እንዴት፡ ደረቀች፡ በለሲቱ፡ አሁን፡ላሁን።

፳፩፡ የሱስም፡ መለሰ፡ አላቸውም። እውነት፡እላ
ችኋለሁ። ሃይማኖትስ፡ ቢኖራችሁ፡ ባትጠራጠሩም፡
እንደ፡ በለሲቱ፡ብቻ፡ አትሰሩም። ነገር፡ ግን፡ ይህን፡
ተራራ፡ብትሉት፡ ተነቅለህ፡ ወደ፡ ባሕር፡ ውደቅ፡ ይ
ሆናል። ምዕ፡ ፲፯፡ ፳።

፳፪፤ በጸሎትም፡የምትለምኑትን፡ሁሉ፡ በማመ
ናት፡ ትወስዳላችሁ።

፳፫፤ ወደ፡ቤተ፡ መቅደስም፡በመጣ፡ጊዜ፡ የካህና
ት፡አለቆች፡ የሕዝብም፡ ሽማግሌዎች፡ ወደርሱ፡ መ
ጡ፡እርሱም፡ሲያስተምር፡እንዲህ፡አሉት። በምን፡
ሥልጣን፡ይህን፡ታደርጋለህ።ይህንስ፡ሥልጣን፡የሰጠ
ህ፡ማነው። ዮሐ፡ ፪፡ ፲፰።

፳፬፤ የሱስም፡ መለሰ፡ አላቸውም። እኔም፡ ደግ
ሞ፡ አንዲት፡ ነገር፡ እጠይቃችኋለሁ። እላንትም፡ ብ
ትነግሩኝ፡ እኔ፡ ደግሞ፡ እነግራችኋለሁ፡ በምን፡ ሥል
ጣን፡ ይህነን፡ እንደደርግ።

፳፭፤ የዮሐንስ፡ ጥምቀት፡ ከወዴት፡ ነበረች። ከሰ
ማይን፡ ወይስ፡ ከሰው። እርሳቸው፡ ግን፡ በልባቸው፡
አሰቡ፡እንዲህ፡ ሲሉ። ከሰማይ፡ ብንለው፡ ይለናል።
እንኪያ፡ ምነው፡ አላመናችሁትም።

፳፮፤ ከሰውም፡ ብንል፡ ሕዝቡን፡ እንፈራለን። ሁ
ሉ፡ዮሐንስን፡እንደ፡*ነቢይ፡ያዩት፡ነበርና።*ም፡፲፬፡፭፡

፳፯፤ ለየሱስም፡መለሱለት፡አሉም።አናውቅም፡
እርሱም፡አላቸው። እኔም፡ አልነግራችሁም፡በምን፡
ሥልጣን፡ ይህነን፡ እንደደርግ።

፳፰፤ ምንስ፡ ይመስላችኋል። ሁለት፡ ልጆች፡ የነበ
ሩት፡ ሰው፡ ነበረ። ወደ፡ ፊተኛውም፡ መጣ፡ አለም።
ልጄ፡ ሆይ፡ ዛሬ፡ ወደ፡ ወይኔ፡ ሒድና፡ ስራ።

፳፱፤ እርሱም፡መለሰ፡አለም፡አልሔድም። ከዚ
ያ፡ ወዲያ፡ ግን፡ ተጠጠተና፡ ሔደ።

፴፤ ወደ፡ ሁለተኛውም፡ መጣ፡ እንዲሁም፡ አለ
ው። እርሱም፡ መለሰ፡ አለም፡ እኔ፡ እሔዳለሁ። አ
ልሔደም። ም፡ ፯፡ ፳፪።

፴፩፤ ማናቸው፡ ከሁለቱ፡ያባቱን፡ፈቃድ፡አደረገ።
አሉት፡ የፊተኛው። የሱስም፡ አላቸው። እውነት፡
እላችኋለሁ። *አጣርችና፡ ጋለሞቶች፡ ይቀድምዋች
ኋል፡ ወደ፡ እግዚአብሔር፡ መንግሥት፡ መግባት።
*ሉቃ፡ ፲፰፡ ፲፬።

፴፪፤ ዮሐንስ፡ መጥቶላችሁ፡ ነበርና፡ በጽድቅ፡ ት
ምህርት፡ አላመናችሁትምም። አጣሮች፡ግን፡ጋለሞ
ቶችም፡አመኑበት። እላንት፡ግን፡ይህነን፡ አይታችሁ፡
አልተጠጠታችሁም፡ ኋላ፡ ታምኑት፡ ዘንድ።
ሉቃ፡ ፯፡ ፳፱።

፴፫፤ ሌላ፡ ምሳሌ፡ ስሙ። ባለ፡ቤት፡ ሰው፡ ነበረ፡ የ
ወይን፡ ስፍራ፡ የተከለ። አጥርም፡ አዞረበት፡ መርገ
ጫም፡ ማሰለት፡ ግምብም፡ሰራ። ለጠባቆችም፡ሰጣ
ቸውና፡ ወደ፡ ሩቅ፡ *አገር፡ ሔደ።
*ማር፡ ፲፪፡ ፩፡—፲፪። ሉቃ፡ ፳፡ ፱፡—፲፱።

፴፬፤ የፍሬውም፡ ዘመን፡ በደረስ፡ ጊዜ፡ ባሮቹን፡
ወደ፡ ጠባቆች፡ ላከ፡ ፍሬውን፡ ይወስዱ፡ ዘንድ።
ኢሳ፡ ፭፡ ፩፡—፲።

፴፭፤ ጠባቆችም፡ባሮቹን፡ያዝዋቸው፡አንዱንም፡
መቱት፡ ሌላውንም፡ ገደሉት፡ ሌላውንም፡ወገሩት።
ም፡ ፳፫፡ ፴፬፡ ፴፯።

፴፮፤ ደግሞ፡ ሌሎች፡ ባሮችን፡ ላከ፡ ከፊተኞች፡ የ
ሚበዙ። እንዲሁም፡አደረጉባቸው። ም፡ ፳፪፡ ፮።

፴፯፤ በመጨረሻም፡ ልጁን፡ ላከባቸው፡ እንዲህ፡
ሲል፡ እስኪ፡ ልጄን፡ ያፍሩት፡ እንደሆን።

፴፰፤ ጠባቆችም፡ ልጁን፡ ባዩት፡ ጊዜ፡ እርሱ፡በርሳ
ቸው፡ አሉ። የሚወርሰው፡ ይህ፡ ነው። *ኑ፡እንግደለ
ውና፡ ርስትንም፡ እጁ፡ እናድርግ። *ም፡ ፳፯፡ ፲፰።

፴፱፤ ያዙትም፡ከወይኑም፡ወደ፡ ሜዳ፡ አወጡና፡
ገደሉት። ዕብ፡ ፲፫፡ ፲፪።

፵፤ የወይኑም፡ ባለ፡ ቤት፡ በመጣ፡ጊዜ፡እለዚያን፡
ጠባቆች፡ ምን፡ ያደርጋቸዋል። ኢሳ፡ ፭፡ ፫፡ ፮።

፵፩፤ አሉት። ክፎችን፡ በክፉ፡ ያጠፋቸዋል፡ወይኑ
ንም፡ ለሌላ፡ ጠባቆች፡ አሳልፎ፡ ይሰጣል፡ ፍሬውን፡
ለሚሰጡ፡በየጊዜው።

፵፪፤ የሱስ፡አላቸው። *በመጽሐፍ፡ከቶ፡ አላነበባ
ችሁምን። አናጾች፡ የናቁት፡ ደንጊያ፡ እርሱ፡ የማዝ
ን፡ ራስ፡ ሆነ። ከእግዚአብሔር፡ ዘንድ፡ ይህች፡ ሆነች፡
ባይናችንም፡ ድንቅ፡ ናት። መዝ፡ ፻፲፰፡ ፳፪።
የሐዋ፡ ፬፡ ፲፩። ሮሜ፡ ፱፡ ፴፫። ፩፡ ጴጥ፡ ፪፡ ፯።

፵፫፤ ስለዚህ፡ እላችኋለሁ። የእግዚአብሔር፡ መ
ንግሥት፡ከላንት፡ እንድትወጣ፡ ለሕዝብም፡ ፍሬዋ
ን፡ ለሚያደርግ፡ ትሰጣለች።

፵፬፤ በዚህ፡ ደንጊያ፡ ላይም፡ የወደቀ፡ይቀጠቀጣ
ል። ደንጊያ፡ የወደቀበት፡ ግን፡ ይፈጨዋል።
ዳን፡ ፪፡ ፴፬፡ ፴፭፡ ፵፬።

፵፭፤ የካህናትም፡ አለቆች፡ ፈሪሳውያንም፡ ምሳ
ሌውን፡ በሰሙ፡ ጊዜ፡ ስለርሳቸው፡ እንዲናገር፡ አ
ወቁ።

፵፮፤ ሊዙትም፡ አሰቡ፡ ከሕዝቡ፡ ግን፡ ፈሩ። በርሳ
ቸው፡ ዘንድ፡ እንደ፡ ነቢይ፡ ነበርና።

## ምዕራፍ፡ ፳፪፡

፩፤ የሱስም፡ መለሰ፡ ደግሞም፡ በምሳሌ፡ ነገራቸ
ው፡ እንዲህ፡ሲል። ሉቃ፡ ፲፬፡ ፲፮፡—፳፬።

፪፤ መንግሥተ፡ሰማያት፡ ንጉሥ፡ ሰው፡ ትመስላለ
ች፡ ዘርግ፡ ለልጁ፡ ያደረገ። ዮሐ፡ ፫፡ ፳፱።

፫፤ ባሮቹንም፡ ላከ፡ወደ፡ ሰርጉ፡የታደሙትን፡ ይጠ
ሩ፡ ዘንድ፡ እምቢም፡ አሉ።

፬፤ ደግሞ፡ ሌሎችን፡ ባሮቹን፡ ላከ፡ እንዲህ፡ ሲል።
የታደሙትን፡ በልዋቸው። እነሆ፡ መብሌን፡ አዘጋጀ
ሁ፡ ላሞቼ፡ ግቾቼም፡ ታርደዋል። ሁሉም፡ ተዘጋጀት
ዋል። ኑ፡ ወደ፡ ሰርጉ። ም፡ ፳፩፡ ፴፮።

፭፤ እርሳቸውም፡ቸል፡አሉ።አንዱም፡ወደርሻው፡
ሔደ፡ ሌላውም፡ ወደ፡ መሸጥና፡ መለወጡ።

፮፤ የቀሩትም፡ ባሮቹን፡ያዝዋቸው፡ ሰደብዋቸው
ም፡ ገደልዋቸውም።

፯፤ ንጉሡም፡ በሰማ፡ጊዜ፡ ተቈጣ፡ጭፍሮቹንም፡
ላከ፡ እሊያንም፡ ገዳዮች፡ አጠፋ፡ አገራቸውንም፡ አ
ቃጠለ። ም፡ ፳፬፡ ፪። ኢሳ፡ ፳፬፡ ፳፩። ዳን፡ ፱፡ ፳፯።

፰፡ ከዚያ፡ ወደ፡ ባሮቹን፡ አለ። ሰርጉስ፡ ተዘጋጅቶዋል፡ የተጸሩት፡ ግን፡ አይገባቸውም።

የሐዋ፡ ፲፫፡ ፵፮፡፡

፱፡ እንግዴህ፡ ወደ፡ መንገዱ፡ መተላለፊያ፡ ሒዱ፡ ያገኛችሁትንም፡ ሁሉ፡ ወደ፡ ሰርጉ፡ ጥሩት።

ሉቃ፡ ፲፬፡ ፳፫፡፡ ፳፩፡ ፵፫፡፡

፲፡ እሊያም፡ ባሮች፡ ወደ፡ መንገድ፡ ወጥተው፡ ያገኙትን፡ ሁሉ፡በሰበሰቡ፡ ክፎችንም፡ በጎችንም። ሰርጉንም፡ ተቀማጮች፡ መሉት። ም፡ ፲፫፡ ፵፯፡ ፵፰፡፡

፲፩፡ ንጉሡም፡የተቀመጡትን፡ለማየት፡በገባ፡ጊዜ፡ ከዚያ፡ አንድ፡ ሰው፡ አየ፡ የሰርግ፡ ልብስ፡ ያለበሰ።

፲፪፡ አለውም፡ ወዳጄ፡ ሆይ። እንዴት፡ ወደዚህ፡ ገባህ፡ የሰርግ፡ ልብስ፡ ያለበስህ። እርሱ፡ ግን፡ ዝም፡ አለ። ኢሳ፡ ፷፩፡ ፲፡፡ ፪፡ ቆሮ፡ ፭፡ ፫፡፡

፲፫፡ የዚያን፡ ጊዜ፡ ንጉሡ፡ ሎሌልቱን፡ አለ። እጁንና፡ እግሩን፡ አጽንታችሁ፡ እሠሩ፡ አውጡትም፡ ሚደም፡ ወደ፡ ጨለማ፡ ጣሉት። ልቅሶ፡ ወደሚሆንበት፡ ጥርስ፡ ማፋጨትም። ም፡ ፲፫፡ ፵፪፡፡ ፳፬፡ ፶፩፡፡

፲፬፡ የሚጸሩ፡ *እጅግ፡ናቸውና፡የሚመረጡ፡ግን፡ ጥቂት፡ ናቸው። *ም፡ ፳፡ ፲፮፡፡

፲፭፡ የዚያን፡ ጊዜ፡ ፈሪሳውያን፡ ሔዱ፡ ተማከሩም፡ በነገር፡ ያስቱት፡ ዘንድ። ማር፡ ፲፪፡ ፲፫፡—፴፩፡፡

ሉቀ፡ ፳፡ ፳፡—፵፡፡

፲፮፡ ደቀ፡ መዛሙርታቸውንም፡ ላኩበት፡ *ከሄሮድስ፡ ሰዎች፡ጋራ፡ እንዲህ፡ ሲሉ። መምህር፡ ሆይ። እናውቃለን፡ እውነተኛ፡ እንደ፡ ሆንህ፡ የእግዚአብሔርንም፡መንገድ፡በውነት፡ታስተምራለህ። ለማንም፡ አታደላም።የሰውን፡ፊት፡አታይምና። *ማር፡ ፫፡ ፮፡፡

፲፯፡ ንገረንም፡ ምን፡ ይመስልሃል። ይገባልን፡ ለቄሣር፡ ግብር፡ መስጠት፡ ወይስ፡ አይገባምን።

፲፰፡ የሱስም፡ክፋታቸውን፡ አወቀ፡አለም። ለምን፡ ትፈታተኑኛላችሁ፡ እላንት፡ ግብዞች።

፲፱፡ የግብሩን፡ ወርቅ፡አሳዩኝ። እርሳቸውም፡ ወርቁን፡ አመጡ።

፳፡ አላቸውም። የማናት፡ ይህች፡ መልክ፡ ጽፈቲቱስ።

፳፩፡ አሉትም፡የቄሣርን።የዚያን፡ጊዜ፡አላቸው። እንኪያስ፡የቄሣርን፡ለቄሣር፡ስጡ፡የእግዚአብሔርንም፡ ለእግዚአብሔር። *ሮሜ፡ ፲፫፡ ፯፡፡

፳፪፡ ሰምተውም፡ ተደነቁ፡ ትተውትም፡ ሔዱ።

፳፫፡ በዚያን፡ቀን፡ሰዱቃውያን፡ትንሣኤ፡የለም፡ የሚሉ፡ ወደርሱ፡ መጡ። የሐ፡ ፳፫፡ ፯፡ ፰፡፡

፳፬፡ እንዲህም፡ ሲሉ፡ ጠየቁት። መምህር፡ሆይ። *ሙሴ፡ አለ፡ አንድ፡ ሰው፡ ቢሞት፡ ልጅም፡ ባይኖረው፡ ወንድሙ፡ ምሽቱን፡ ያግባ፡ ዘርም፡ ለወንድሙ፡ ያድርግ። *ዘዳግ፡ ፳፭፡ ፭፡፡

፳፭፡ ከኛም፡ ዘንድ፡ ሰባት፡ ወንድማማች፡ ነበሩ። ታላቃቸው፡ምሽት፡አገባና፡ሞተ፡ልጅም፡ ባይኖረው፡ ምሽቱን፡ ተወ፡ ለወንድሙ።

፳፮፡ እንዲሁም፡ደግሞ፡ ሁለተኛው፡ ሦስተኛው፡ እስከ፡ ሰባተኛው።

፳፯፡ ከሁሉም፡ በኋላ፡ ሴቲቱ፡ ደግሞ፡ ሞተች።

፳፰፡ በትንሣኤ፡ ቀንስ፡ ለማን፡ ከሰባቱ፡ ምሽት፡ ትሆነዋለች። ሁሉ፡ አግብተዋታልና።

፳፱፡ የሱስም፡መለሰ፡ አላቸውም። ሳታችሁ፡ መጽሐፍ፡ ባለ፡ ማወቅ፡ የእግዚአብሔርንም፡ ኃይል።

፴፡ በትንሣኤ፡ አያገቡምና፡አይገቡምምና። እንደ፡ እግዚአብሔር፡ መልክተኞች፡ በሰማይ፡ ይሆናሉ፡ እንጂ። ራእይ፡ ፳፩፡ ፲፯፡፡

፴፩፡ ስለ፡ ትንሣኤ፡ ሙታን፡ ግን፡ አላነበባችሁምን፡ ከእግዚአብሔር፡ ዘንድ፡ የተባለውን፡ ባለ፡ ጊዜ።

፴፪፡ እኔ፡ *የአብርሃም፡ አምላክ፡ ነኝ። የይስሐቅም፡ አምላክ። የያዕቆብም፡ አምላክ። እግዚአብሔር፡ የሙታን፡ አምላክ፡ አይደለውም፤ የሕያዋን፡ እንጂ። *ዘፀአ፡ ፫፡ ፮፡ ፲፮፡፡ ዕብ፡ ፲፩፡ ፲፮፡፡

፴፫፡ አሕዛብም፡ሰምተው፡ከትምህርቱ፡አደነቁ።

፴፬፡ ፈሪሳውያንም፡ በሰሙ፡ ጊዜ፡ የሰዱቃውያንን፡ አፍ፡ እንደ፡ዘጋ፡ ሁሉ፡ወደርሱ፡ ባንድ፡ ተሰበሰቡ።

፴፭፡ ከርሳቸውም፡ ወገን፡አንድ፡ ኦሪታዊ፡ ጠየቀው፡ ሲፈትነው፡ እንዲህም፡ ሲለው።

ማር፡ ፲፪፡ ፳፰፡—፴፩፡፡

፴፮፡ መምህር፡ ሆይ። ከኦሪት፡ ማናቸይቱ፡ ትእዛዝ፡ ትበልጣለች። ሉቃ፡ ፲፡ ፳፭፡፡

፴፯፡ የሱስም፡አለው። እግዚአብሔርን፡አምላክህን፡ ትወድ፡ ዘንድ፡ ከፍጹም፡ ልብህ፡ ከፍጹምም፡ ነፍስህ፡ ከፍጹምም፡ አሳብህ።

ዘዳግ፡ ፮፡ ፭፡፡ ፲፡ ፲፪፡፡

፴፰፡ ይህች፡ መጀመሪያይቱ፡ ትእዛዝ፡ የምትበልጠው፡ናት።

፴፱፡ ሁለተኛይቱም፡ የምትመስላት። ባልንጀራህን፡ ትወድ፡ ዘንድ፡ እንደ፡ ነፍስህ። ዘሌዋ፡ ፲፱፡ ፲፰፡፡

፵፡ በለዚህ፡በሁለቱ፡ትእዛዛት፡ ኦሪት፡ሁሉ፡ነቢያትም፡ ተሰቅለዋል። ሮሜ፡ ፲፫፡ ፲፡፡ ገላት፡ ፭፡ ፲፬፡፡

፵፩፡ ፈሪሳውያንም፡ ተከማችተው፡ ሳሉ፡ የሱስ፡ ጠየቃቸው፡ እንዲህ፡ ሲል። ማር፡ ፲፪፡ ፴፭፡ ፴፯፡፡

ሉቃ፡ ፳፡ ፵፩፡—፵፬፡፡

፵፪፡ ስለ፡ክርስቶስ፡ምን፡ ይመስላችኋል። የማን፡ ልጅ፡ ነው። አሉት፡ የዳዊት፡ ልጅ።

፵፫፡ እርሱም፡ አላቸው፡ እንኪያ፡ እንዴት፡ ዳዊት፡ በመንፈስ፡ ቅዱስ፡ ጌታ፡ ይጸራዋል።

፵፬፡ እንዲህ፡ ሲል። *ጌታ፡ ጌታዬን፡ አለው። በቀኜ፡ ተቀመጥ፡ ጸላቶችህን፡ ከእግርህ፡ ጫማ፡ በታች፡ እስክጥል፡ ድረስ። *መዝ፡ ፻፲፡ ፩፡፡

፵፭፡ ዳዊት፡ጌታ፡ብሎ፡ከጸራው። እንዴት፡ልጁ፡ ይሆናል። ፩፡ ዜና፡ ፲፯፡ ፲፫፡፡

፵፮፡ ማንም፡ በነገር፡ ይመልስለት፡ዘንድ፡ አልቻለም። ማንም፡ ከቶ፡ ከዚያ፡ ቀን፡ጀምሮ፡ይጠይቀው፡ ዘንድ፡ አልደፈረም።

ምዕራፍ፡ ፳፫፤

፩፤ ከዚያ፡ ወዲያም፡ የሱስ፡ ለሕዝብና፡ ለደቀ፡ መዛሙርቱ፡ እንዲህ፡ ሲል፡ ነገራቸው።

ማር፡ ፲፪፡ ፴፰፡—፵፡፡

፪፤ ጻፎች፡ ፈሪሳውያንም፡ በሙሴ፡ ወንበር፡ ተቀመጡ። ሉቃ፡ ፳፡ ፵፭፡—፵፯፡፡ ዘፀአ፡ ፲፰፡ ፲፫፡፡

፫፤ ስለዚህም፡ ያልዋችሁን፡ሁሉ፡ ትጠብቁት፡ ዘንድ፡ ጠብቁት፡ አድርጉትም፡ እንደ፡ ስራቸው፡ ግን፡ አትስሩ። ኢያስተማሩት፡ አያደርጉትምና።

መልክ፡ ፪፡ ፯፡፡

፬፤ ታላቅ፡ ሸክም፡ የከበደም፡ አሥረው፡ በሰው፡ ጫንቃ፡ ይጭኑታልና፡ እርሳቸውስ፡ በፃታቸው፡ ስንኂ፡ አይነኩትም። ሉቃ፡ ፲፩፡ ፵፮፡፡

፭፤ ስራቸውንም፡ ሁሉ፡ ይሰራሉ፡ለሰው፡ *ሊታዩ። የቀሚሳቸውንም፡ እጅጌ፡ ያሰፋሉ፡ የልብሳቸውንም፡ ዘርፍ፡ †ያስረዝማሉ። *ም፡ ፮፡ ፩፡፡

†ዘፀአ፡ ፲፫፡ ፱፡፡ ዘኍል፡ ፲፭፡ ፴፰፡፡

፮፤ በምሳም፡ በላይ፡ መቀመጥ፡ ይወዳሉ፡ በሸንጎም፡ የፊተኛ፡ ወንበር። ሉቃ፡ ፲፬፡ ፯፡፡ ፲፩፡ ፵፫፡፡

፯፤ ገቢያ፡ ለገቢያም፡ መሳለም። ሰውም፡መምህራን፡ ይላቸው፡ ዘንድ።

፰፤ እላንተ፡ግን፡መምህራን፡ተብላችሁ፡አትጸሩ። መምህራችሁ፡ አንድ፡ ነውና፡ እርሱም፡ ክርስቶስ። እላንትም፡ ሁላችሁ፡ ወንድማማች፡ ናችሁ።

፱፤ በምድር፡ ላይም፡ ማንም፡ አባታችሁን፡ አትጽሩ። አባታችሁ፡ አንድ፡ ነውና፡ በሰማይ፡ ያለ።

መል፡ ፩፡ ፮፡ ፪፡ ፲፡፡ ኤፌ፡ ፫፡ ፲፬፡ ፲፭፡፡

፲፤ ጌቶችም፡ አትጸሩ። ጌታችሁ፡ አንድ፡ ነውና፡ እርሱም፡ ክርስቶስ።

፲፩፤ ከላንትም፡ የሚበልጥ፡ ሎሌ፡ ይሁናችሁ።

ም፡ ፳፡ ፳፮፡ ፳፯፡፡

፲፪፤ ነፍሱን፡ ከፍ፡ ከፍ፡ ያደረገ፡ ዝቅ፡ ይላልና፡ ነፍሱንም፡ ዝቅ፡ ዝቅ፡ ያደረገ፡ ከፍ፡ ከፍ፡ ይላልና።

ምሳ፡ ፳፱፡ ፳፫፡፡ ሕዝ፡ ፳፩፡ ፳፮፡፡ ፩፡ ጴጥ፡ ፭፡ ፭፡፡

፲፫፤ ወዮላችሁ፡ እላንተ፡ ጻፎች፡ ፈሪሳውያንም፡ ግብዞች። መንግሥተ፡ ሰማያትን፡ በሰው፡ ፊት፡ ትዘጋላችሁና። እላንተ፡ አትገቡምና። የሚገቡትንም፡ ይገቡ፡ ዘንድ፡ አተውም። ሉቃ፡ ፲፩፡ ፶፪፡፡

፲፬፤ ወዮላችሁ፡ እላንተ፡ ጻፎች፡ ፈሪሳውያንም፡ ግብዞች። የመበለቶችን፡ ቤት፡ ትበላላችሁና፡ በጸሎታችሁ፡ርዝመት፡ምክንያት። ስለዚህ፡ታላቅ፡ፍርድ፡ ትቀበላላችሁ። ሕዝ፡ ፳፪፡ ፳፭፡፡ ሚክ፡ ፪፡ ፱፡፡

፲፭፤ ወዮላችሁ፡ እላንት፡ ጻፎች፡ ፈሪሳውያንም፡ ግብዞች። ባሕሩን፡ በሩንም፡ ትዞራላችሁና፡ አንድ፡ መጻተኛ፡ ልታጠምቁ። በሆነም፡ ጊዜ፡ የገሃነም፡ልጅ፡ ታደርጉታላችሁ፡ የላንት፡ዕጽፍ።

፲፮፤ ወዮላችሁ፡ እላንት፡ *ዕውር፡ መሮች። የምትሉ፡ በቤተ፡ መቅደስ፡ የማለ፡ ኃጢአት፡ የለበትም። በቤተ፡ መቅደስ፡ ወርቅ፡ ግን፡ የማለ፡ እርሱ፡ኃጢአተኛ፡ ነው። *ም፡ ፲፭፡ ፲፬፡፡

፲፯፤ እላንት፡ ሰነፎች፡ዕውሮችም። ማናቸው፡ ይበልጣል። ወርቁን፡ ወይስ፡ ቤተ፡ መቅደስ፡ ወርቁን፡ የሚቀድሰው።

፲፰፤ ደግማችሁም፡ትላላችሁ፡በመሠዊያው፡የማለ፡ኃጢአት፡የለበትም። በላዩ፡ ባለው፡ ቍርባን፡ ግን፡ የማለ፡ ኃጢአተኛ፡ ነው።

፲፱፤ እላንት፡ሰነፎች፡ዕውሮችም። ማናቸው፡ ይበልጣል። ቍርባኑን፡ ወይስ፡ መሠዊያው፡ ቍርባኑን፡ የሚቀድሰው። ዘፀአ፡ ፳፱፡ ፴፯፡፡

፳፤ እንኪያስ፡ በመሠዊያው፡ የማለ፡ ፈጽሞ፡ በርሱ፡ ማለበት፡ በላዩም፡ ባለው፡ ሁሉ።

፳፩፤ በቤተ፡ መቅደስም፡ የማለ፡ እርሱ፡ ይምልበታል፡ በሚያድርበትም።

፳፪፤ በሰማይም፡ የማለ፡እርሱ፡በእግዚአብሔር፡ ዙፋን፡ ይምላል፡ በላዩ፡ በተቀመጠውም።

ም፡ ፭፡ ፴፬፡፡

፳፫፤ ወዮላችሁ፡እላንት፡ ጻፎች፡ ፈሪሳውያንም፡ ግብዞች። *ከሥር፡ አንድ፡ታወጣላችሁና፡ ጎመን፡ ዘርን፡ ጧናያምንም፡ አንሰላልንም። ታላቁንም፡ የኦሪትን፡ ተትአዛዝ፡ ተዋችሁ፡ ፍርድን፡ ምሕረትንም፡ ሃይማኖትንም። ይህችን፡ ታደርጉ፡ ዘንድ፡ ይገባችሁ፡ ነበር፡ያችንም፡ባትተው። *ሉቃ፡ ፲፩፡ ፵፪፡፡

ዘሌዋ፡ ፳፯፡ ፴፡፡ †ሚክ፡ ፮፡ ፰፡፡

፳፬፤ እላንት፡ዕውር፡ መሮች። ትንኝ፡ የምታጠሩ፡ ግመልንም፡ የምትውጡ።

፳፭፤ ወዮላችሁ፡ እላንት፡ ጻፎች፡ ፈሪሳውያንም፡ ግብዞች። የጽዋውንና፡ የወጭቱን፡ ላይ፡ ላዩን፡ ታጸራላችሁና። ውስጣቸው፡ግን፡ቅሚያ፡ ስስትም፡ መልቶዋል። ሉቃ፡ ፲፩፡ ፴፱፡፡ ማር፡ ፯፡ ፬፡፡

፳፮፤ አንተ፡ ፈሪሳዊ፡ ዕውር፡ አስቀድመህ፡ የጽዋውንና፡ የወጭቱን፡ውስጥ፡ አጽራ። ደግሞ፡ ላያቸው፡ ንጹሕ፡ ይሆን፡ ዘንድ። ቲጦ፡ ፩፡ ፲፭፡፡

፳፯፤ ወዮላችሁ፡ እላንት፡ ጻፎች፡ ፈሪሳውያንም፡ ግብዞች። የተለዘነ፡መቃብር፡ትመስላላችሁና። በሜዳ፡ መልካም፡ሁና፡ የሚታይ፡ በውስጡ፡ ግን፡ የሙታን፡ አፅንት፡ ርኩስም፡ ሁሉ፡ መልቶበታል።

ሉቃ፡ ፲፩፡ ፵፬፡፡ የሐዋ፡ ፳፫፡ ፫፡፡

፳፰፤ እንዲሁ፡ደግሞ፡እላንትም፡በሜዳ፡ለሰው፡ ትታያላችሁ፡ ጻድቃን፡ መስላችሁ። በውስጣችሁ፡ ግን፡ ማድላት፡ ኃጢአትም፡ መልቶባችኋል።

፳፱፤ ወዮላችሁ፡ እላንት፡ ጻፎች፡ ፈሪሳውያንም፡ ግብዞች። የነቢያትን፡ መቃብር፡ ትሰራላችሁና፡የጻድቃንን፡ መቃብርም፡ ታስጌጻላችሁ።

ሉቃ፡ ፲፩፡ ፵፯፡—፶፩፡፡

፴፤ ትላላችሁም፡ባባቶቻችን፡ ዘመንስ፡ ኑረን፡ አንድ፡ ሆነ፡ በነቢያት፡ ደም፡ ባልተባባርናቸውም፡ ነበርነ።

፴፩፤ እነሆ፡ በነፍሳችሁ፡ ትመሰክራላችሁ፡ የነቢያ
ት፡ ገደዮች፡ልጆች፡ እንደ፡ ሆናችሁ። የሐዋ፡ ፯፥ ፶፪።
፴፪፤ እላንትም፡ ያባቶቻችሁን፡ መስፈርያ፡ ፈጽ
ሙ።
፴፫፤ እላንተ፡ *እባቦች፡ የጉበና፡ ልጆች፡ እንዴት፡
ከገሃነም፡ ፍርድ፡ ታመልጣላችሁ። *ም፡ ፫፥ ፯።
፴፬፤ ስለዚህ፡ እነሆ፡ ነቢያትን፡ እልክባችኋለሁ፡
*ጠቢባንንም፡ጻፎችንም። ከርሳቸውም፡ትገድላላች
ሁ፡ትሰቅሉማላችሁ። ከርሳቸውም፡በመስጊዳችሁ፡
ትገርፏላችሁ፡ ካገር፡ወደገርም፡ ታሳድዋቸዋላችሁ።
*ም፡ ፲፫፥ ፶፪።
፴፭፤ በምድር፡ ላይ፡ የፈሰሰው፡የጻድቅ፡ ደም፡ ሁ
ሉ፡ ይደርስባችሁ፡ ዘንድ። ከጻድቁ፡ *ከአቤል፡ ደም፡
ጀምሮ፡እስከ፡በራክያ፡ልጅ፡እስከ፡ †ዘካርያስ፡ደም፡
ድረስ፡ በቤተ፡ መቅደስና፡ በመሠዊያው፡ መካከል፡
የገደላችሁት። *ኤር፡ ፳፮፥ ፲፭፥ ፩፥ ዮሐ፡ ፫፥ ፲፪።
†፪፥ ዜና፡ ፳፬፥ ፳፩—፳፪።
፴፮፤ እውነት፡ እላችኋለሁ። ይህ፡ ሁሉ፡በዚህ፡ ት
ውልድ፡ ላይ፡ እንዲደርስ።
፴፯፤ የሩሳሌም፡የሩሳሌም፡ሆይ። ነቢያትን፡የም
ትገድዪ፡ወደንች፡የተላኩትንም፡የምትወግሪ።ስንት
ግዜ፡ ልጆችሽን፡ እሰበስብ፡ ዘንድ፡ ወደድሁ፡ ዶሮ፡ ጫ
ጩቶችዋን፡ በክንፏዋ፡ ታች፡ እንድትሰበስብ። እንቢ
ንም፡ አላችሁ። *ሉቃ፡ ፲፫፥ ፴፬። የሐዋ፡ ፯፥ ፶፪።
፴፰፤ እነሆ፡ቤታችሁ፡የተፈታ፡ሁና፡ይቀርላችኋል።
፩፥ ነገሥ፡ ፱፥ ፯። ኤር፡ ፳፪፥ ፭—፲።
፴፱፤ እላችኋለሁና፡ እንደታዩኝ፡ እስክትሉ፡ ድረ
ስ። በእግዚአብሔር፡ ስም፡ የሚመጣ፡ የተባረከ፡
ነው። ም፡ ፳፩፥ ፱።

## ምዕራፍ፡ ፳፬፥

፩፤ የሱስም፡ ከቤተ፡መቅደስ፡ወጥቶ፡ ሔደ። ደቀ፡
መዛሙርቱም፡ የቤተ፡ መቅደስን፡ ስራ፡ ሊያሳዩት፡
ወደርሱ፡ መጡ። ማር፡ ፲፫። ሉቃ፡ ፳፩።
፪፤ የሱስም፡አላቸው፡ ይህነን፡ሁሉ፡ ታያላችሁን።
እውነት፡ እላችኋለሁ። ደንጊያ፡ በደንጊያ፡ ላይ፡ ከዚ
ህ፡እንዲደቀር፡ ይፈርሳል፡ እንጂ። ሉቃ፡ ፲፱፥ ፵፬።
፫፤ እርሱም፡ በደብረ፡ዘይት፡ተቀምጦ፡ሳለ፡ ደቀ፡
መዛሙርቱ፡ ወደርሱ፡ መጡ፡ ለብቻቸው፡ እንደህ፡
ሲሉ። ንገረነ፡ ይህ፡መቸ፡ ይሆናል፡ምንድርስ፡የመም
ጣትህ፡ ምልክት፡ ነው፡ የዓለሙስ፡ ፍጻሜ።
፬፤ የሱስም፡መልሶ፡ አላቸውም። ተጠንቀቁ፡ ማ
ንም፡ አያስታችሁ።
፭፤ ብዙ፡ ሰዎች፡ በስሜ፡ *ይመጣሉና፡ እንደህ፡
ሲሉ፡ ክርስቶስ፡ እኔ፡ ነኝ። እጅግም፡ ሰዎች፡ያስታሉ።
*ቍ፡ ፳፬። የሐዋ፡ ፭፥ ፴፮። ፩፥ ዮሐ፡ ፪፥ ፲፰።
፮፤ ፀብ፡ ትሰማላችሁና፡የፀብንም፡ወሬ። አወቁ፡
አትደንግጡ። ይህ፡ ሁሉ፡ ይሆን፡ዘንድ፡አለውና። ነገ
ር፡ ግን፡ ፍጻሜ፡ ገና፡ አይመጣም።
፯፤ ሕዝብ፡ በሕዝብ፡ ላይ፡ ይነሣሉና፡ መንግሥት
ም፡ በመንግሥት፡ላይ። ራብም፡ ይሆናል፡ ቸነፈርም፡
መናወጥም፡ በያገሩ።
፰፤ ይህም፡ ሁሉ፡ የምጥ፡ ጣር፡ መጀመርያ፡ ነው።
፱፤ የዚያን፡ጊዜ፡ ለመከራ፡ አሳልፎ፡ ይሰጥዋችኋ
ል፡ ይገልዋችኋልም። በአሕዛብም፡ ሁሉ፡ የተጸላች
ሁ፡ ትሆናላችሁ፡ ሰለ፡ ስሜ። ም፡ ፲፥ ፲፯።
ዮሐ፡ ፲፮፥ ፪።
፲፤ በዚያ፡ ጊዜም፡ ብዙ፡ ሰዎች፡ ይሰናከላሉ። እር
ሱ፡ በርሳቸውም፡ ይሰጣጣሉ። እርሱ፡ በርሳቸውም፡
ይላሉ።
፲፩፤ ካስተኞች፡ ነቢያትም፡ ብዙ፡ይነሣሉ፡ ብዞችን
ም፡ያስታሉ። ም፡ ፯፥ ፲፭። ፩፥ ዮሐ፡ ፬፥ ፩።
፲፪፤ ከዓመፃም፡ ብዛት፡ የተነሣ፡ ፍቅር፡ ከብዞች፡
ትበርዳለች። ፪፥ ተሰ፡ ፪፥ ፲። ፩፥ ጢሞ፡ ፫፥ ፩።
፲፫፤ እስከ፡ ፍጻሜ፡ ግን፡ የሚታገሥ፡ እርሱ፡ ይድ
ናል። ራእ፡ ፲፫፥ ፲።
፲፬፤ በዚህም፡ በመንግሥት፡ *ወንጌል፡ በዓለም፡
ሁሉ፡ ይሰበካል፡ †ምስክር፡ ሊሆንባቸው፡በአሕዛብ፡
ሁሉ። በዚያ፡ጊዜም፡ፍጻሜ፡ይመጣል።
*ም፡ ፳፰፥ ፲፱። †ም፡ ፲፥ ፲፰።
፲፭፤ የመፍረሱንም፡ መርከስ፡ በነቢዩ፡ በዳንኤል፡
የተባለችውን፡ በተቀደሰው፡ ስፍራ፡ ቁማ፡ ባያችሁ፡
ጊዜ። አንባቢም፡ ያስተውል። ዳን፡ ፱፥ ፳፮፥ ፳፯።
፲፪፥ ፲፩።
፲፮፤የዚያን፡ጊዜ፡በይሁዳ፡ያሉ፡ወደ፡ተራራ፡ይሽሹ።
፲፯፤ በሰገነት፡ ያለ፡አይውረድ፡ ከቤቱ፡ አንዳች፡ ይ
ወስድ፡ ዘንድ። ሉቃ፡ ፲፯፥ ፴፩።
፲፰፤ በምድረ፡ በደም፡ ያለ፡ወደ፡ኋላው፡ አይመለ
ስ፡ ልብሱን፡ ይወስድ፡ ዘንድ።
፲፱፤ ወዮላቸውም፡ለርጉዞች፡ለሚያጠቡም፡በዚ
ያን፡ ወራት።
፳፤ ጸልዩም፡ መሸሻችሁ፡ በክረምት፡ እንዳይሆ
ን፡ *በሰንበትም። *የሐዋ፡ ፩፥ ፲፪።
፳፩፤ በዚያን፡ጊዜ፡ ታላቅ፡ መከራ፡ይሆናልና። እን
ደርሱ፡ ያልሆነ፡ ዓለም፡ ከተፈጠረ፡ ጀምሮ፡ እስከ፡ ዛ
ሬ፡ ድረስ፡ እንጊደህም፡ አይሆንም። ዳን፡ ፲፪፥ ፩።
፳፪፤ ያች፡ ወራትስ፡ ባታጥር፡ሥጋ፡የለበሰ፡ ሁሉ፡ ባ
ልዳነም። ነገር፡ ግን፡ ስለ፡ ተመረጹት፡ ታጥራለች፡ ያ
ች፡ ወራት።
፳፫፤ የዚያን፡ ጊዜ፡ ማንም፡ ቢላችሁ፡ እነሆ፡ ክርስ
ቶስ፡ ከዚህ፡ ነው፡ ወይም፡ ከዚያ፡ አትመኑ።
፳፬፤ አስተኞች፡ ክርስቶስ፡ ተብለው፡ ይነሣሉና፡
አስተኞችም፡ ነቢያት። ምልክትም፡ ታምራትም፡ ታ
ላላቆች፡ ያደርጋሉ፡ የተመረጡትን፡ ስንኳ፡ ሊያስቱ፡
ቢቻላቸው። ቍ፡ ፭፥ ፲፩። ፪፥ ተሰ፡ ፪፥ ፰፥ ፱።
፳፭፤ እነሆ፡ አስቀድሜ፡ ነገርኋችሁ።
፳፮፤ቢልዋችሁም፡እነሆ፡በሜዳ፡ነው፡አትውጡ።
እነሆ፡ በቤት፡ ነው፡ አትመኑ።

፳፯፤ መብረቅ፡ ከምሥራቅ፡ እንዲወጣ፡ እስከ፡
ምዕራብም፡ እንዲታይ፡ እንደሁ፡ ደግሞ፡ የሰው፡ ል
ጅ፡ መታየቱ፡ ይሆናልና። ሉቃ፡ ፲፯፤ ፳፬።
፳፰፤ ጥምብም፡ ወደለበት፡ከዚያ፡አሞሮች፡ ይሰ
በሰባሉ። ኢዮብ፡ ፴፱፤ ፴። አንባ፡ ፩፤ ፰።
ሉቃ፡ ፲፯፤ ፴፯።
፳፱፤ በዚያን፡ ጊዜም፡ ከዚያ፡ *ዘመን፡ መከራ፡ በ
ኋላ፡ ጸሐይ፡ ጨለማ፡ ትሆናለች፡ ጨረቃውም፡ ብርሃ
ኑን፡ አይሰጥም። ከዋክብቱም፡ ከሰማይ፡ ይወድቃ
ሉ፡ የሰማይም፡ ኃይል፡ ትናወጣለች። *ኢሳ፡ ፲፫፤ ፲።
፪፤ ጴጥ፡ ፫፤ ፲።
፴፤ የዚያን፡ ጊዜም፡ የሰው፡ ልጅ፡ ምልክት፡ በሰ
ማይ፡ይገለጻል። የዚያን፡ ጊዜም፡ *ያለቅሳሉ፡የምድ
ር፡ አሕዛብ፡ ሁሉ። የሰው፡ልጅም፡በሰማይ፡ ደመና፡
ላይ፡ ሲመጣ፡ ያዩታል፡ ከኃይልና፡ ከብዙ፡ ምስጋና፡
ጋራ። *ራእ፡ ፩፤ ፯።
፴፩፤ መልክተኞቹንም፡ ይልካል፡ *ከምስር፡ ቃና፡
ታላላቅ፡ ድምፅ፡ ጋራ። ለርሱ፡ የተመረጡትንም፡ ካ
ራቱ፡ ነፋሳት፡ ያከማቻሉ፡ ከሰማይ፡ ዳር፡ጀምሮ፡እስ
ከ፡ ዳርቻዋ፡ ድረስ። *፩፤ ቆሮ፡ ፲፭፤ ፶፪።
፩፤ ተሰ፡ ፬፤ ፲፯። ራእ፡ ፳፤ ፪—፲።
፴፪፤ ከበለስም፡ ምሳሌውን፡ እወቁ። ጫፏዋ፡ የ
ለመለመ፡ እንደ፡ሆነ፡ቅጠልዋም፡የወጣ፡እንደ፡ሆነ፡
አወቃችሁ፡ በጋ፡ እንደ፡ ቀረበ።
፴፫፤ እንደሁ፡ ደግሞ፡ እላንትም፡ ይህነን፡ ሁሉ፡
ባያችሁ፡ ጊዜ፡ እወቁ፡ በደጅ፡ ላይ፡ እንደ፡ ቀረበ።
፴፬፤ እውነት፡ እላችኋለሁ፡ይህ፡ ትውልድ፡ እንዳ
ያልፍ፡ ይህ፡ ሁሉ፡ እስኪሆን፡ ድረስ።
፴፭፤ ሰማይና፡ምድር፡ያልፋል፡ ነገሬ፡ግን፡አያልፍ
ም። ም፡ ፭፤ ፲፰።
፴፮፤ ያነን፡ ቀን፡ ግን፡ ያቺንም፡ ሰዓት፡ ማንም፡ አ
ያውቃትም።የሰማይ፡መልክተኞች፡ስንኳ። ካንደ፡
ካባቴ፡ በቀር። ፩፤ ተሰ፡ ፭፤ ፩—፲፪።
፴፯፤ የኖህ፡ዘመንም፡እንደ፡ሆነ፡እንዴሁ፡ደግሞ፡
ይሆናል፡ የሰው፡ ልጅ፡ መምጣት።
ዘፍ፡ ፯፤ ፲፩—፳፪። ሉቃ፡ ፲፯፤ ፳፯፤ ፳፰።
፴፰፤ ከጥፋት፡ ውኃ፡ በፊት፡ ዘመን፡ እንደ፡ ነበሩ፡
ሲበሉ፡ ሲጠጡም። ሲጋቡ፡ ሲያገቡም። ኖህ፡ ወደ፡
መርከብ፡ እስከሚገባበት፡ቀን። ፪፤ ጴጥ፡ ፫፤ ፭፤ ፯።
፴፱፤ አላወቁምም፡ የጥፋት፡ ውኃ፡ መጥቶ፡ ሁሉ
ን፡እስኪያጠፋ፡ድረስ።እንዴሁ፡ደግሞ፡ይሆናል፡የሰ
ው፡ ልጅ፡ መምጣት።
፵፤ የዚያን፡ጊዜ፡ሁለት፡በርሻ፡ይሆናሉ። አንዱን፡
ይወስዲታል፡ ሁለተኛውንም፡ ይተውታል።
ሉቃ፡ ፲፯፤ ፴፭፤ ፴፯።
፵፩፤ ሁለት፡ሴቶች፡በወፍጮ፡ይፈጫሉ። አንዲቱ
ን፡ ይወስድዋታል፡ ሁለተኛዪቱንም፡ ይተውዋታል።
፵፪፤ እንግዴህ፡ትጉ። አታውቁምና፡ በምንም፡ ጊ
ዜ፡ ጌታችሁ፡ እንዲመጣ። ም፡ ፳፭፤ ፲፫።

፵፫፤ ይህነን፡ ግን፡ እውቁ። *ባለ፡ ቤት፡ ቢያውቅ፡
በምን፡ ትጋት፡ ሌባ፡ እንዲመጣ፡ በተጋ፡ ቤቱም፡ ሊ
ቈፈር፡ ባልተወም። *ሉቃ፡ ፲፪፤ ፴፱—፵።
፵፬፤ ስለዚህ፡እላንት፡ደግሞ፡ተዘጋጅታችሁ፡ተቀ
መጡ። ባላሰባችሁት፡ጊዜ፡የሰው፡ ልጅ፡ይመጣልና።
፵፭፤ እስኪ፡ ማነው፡ያ፡ የታመነው፡ብልሐተኛው
ም፡ ባርያ፡ ጌታው፡ በቤቱ፡ ሰዎች፡ላይ፡ የሚሾመው፡
ምግባቸውን፡ ሊሰጣቸው፡ በጊዜው።
፵፮፤ ያ፡ ባርያ፡ የተመሰገነ፡ ነው፡ ጌታው፡ መጥቶ፡
እንዴህ፡ ሲያደርግ፡ የሚያገኘው።
፵፯፤ እውነት፡ እላችኋለሁ፡ በከብቱ፡ ሁሉ፡ ላይ፡
እንዲሾመው። ም፡ ፳፭፤ ፳፩፤ ፳፫።
፵፰፤ በልቡ፡ ቢል፡ ግን፡ ያ፡ ክፉ፡ ባርያ። ጌታዬ፡ እስ
ኪመጣ፡ ይዘገያል። መክ፡ ፰፤ ፲፩።
፵፱፤ ባልንጀሮቹንም፡ ባሮች፡ ይመታ፡ ይጀምራል፡
ከሰካሮችም፡ ጋራ፡ ይበላል፡ ይጠጣልም።
፶፤ የዚያ፡ ባርያ፡ ጌታ፡ ይመጣል፡ ባላሰበው፡ ቀን፡
በማያውቃትም፡ ጊዜ።
፶፩፤ በመካከሉም፡ ይሰነጥቀዋል፡ እድሉንም፡ ከ
ግብዞች፡ ጋራ፡ ያደርግለታል። *ልቅሶ፡ ወደለበት፡ ጥር
ስ፡ ማፋጨትም። *ም፡ ፰፤ ፲፪።

## ምዕራፍ፡ ፳፭፤

፩፤ የዚያን፡ ጊዜ፡ መንግሥተ፡ሰማያት፡ አሥር፡ ቈ
ነጃጅት፡ ትመስላለች፡ መብራታቸውን፡ ይዘው፡ የወ
ጡ፡ሙሽራውን፡ ለመቀበል። ሉቃ፡ ፲፪፤ ፴፯።
ራእ፡ ፲፱፤ ፯።
፪፤ አምስቱ፡ ግን፡ ከርሳቸው፡ ብልሐተኞች፡ ነበሩ፡
አምስቱም፡ ሰነፎች።
፫፤ ሰነፎችም፡ መብራታቸውን፡ ወስደው፡ቅባኑግ፡
ከርሳቸው፡ ጋራ፡ አልወሰዱም።
፬፤ ብልሐተኞች፡ ግን፡ ቅባኑግ፡ወሰዱ፡በማሰሮዋቸ
ው፡ ከመብራታቸው፡ ጋራ።
፭፤ ሙሽራውም፡ በዘገየ፡ ጊዜ፡ ሁሉ፡ አንቀላፉ፡
ተኙም።
፮፤ እኩል፡ሌትም፡በሆነ፡ጊዜ፡ጩኸት፡ሆነ። እነሆ፡
ሙሽራ፡ ደረሰ። ውጡ፡ ትቀበሉት፡ ዘንድ።
፩፤ ተሰ፡ ፬፤ ፲፯።
፯፤ የዚያን፡ጊዜ፡እለዚያ፡ቈነጃጅት፡ሁሉ፡ተነሡ፡
መብራታቸውንም፡ አበጁ።
፰፤ ሰነፎችም፡ ብልሐተኞችን፡ አልዋቸው። ከቅባ
ኑጋችሁ፡ ስጡነ፡ መብራታችን፡ ይጠፋልና።
ምሳ፡ ፴፩፤ ፲፰።
፱፤ ብልሐተኞችም፡ መለሱ፡እንዴህ፡ሲሉ። ባይበ
ቃነሳ፡ ለኛም፡ ለላንትም። ነገር፡ ግን፡ ወደ፡ ሻያጮች፡
ሒዱ፡ ለላንትም፡ ግዙ።
፲፤ ሊገዙም፡ በሔዱ፡ጊዜ፡ ሙሽራው፡ መጣ። የተ
ዘጋጁትም፡ ከርሱ፡ ጋራ፡ ወደ፡ ሰርግ፡ ገቡ፡ ደጁም፡ ተ
ዘጋ። ሉቃ፡ ፲፫፤ ፳፭።

፲፩፡ ከዚያ፡ በኋላም፡ የቀሩቱ፡ ቈነጃጅት፡ መጡ፡ እንዲህ፡ ሲሉ። አቤቱ፡ አቤቱ፡ ክፈትልነ።

ሉቃ፡ ፲፫፡ ፳፭።

፲፪፡ እርሱ፡ግን፡ መለሰ፡ አለም። እውነት፡እላችኋለሁ፡እንደላውቃችሁ። ማ፡ ፯፡ ፳፫።

፲፫፡ እንግዲህ፡ትጉ። ቀኒቱን፡አታውቁምና፡ሰዓቲቱንም፡የሰው፡ ልጅ፡ የሚመጣባትን።

ማ፡ ፳፬፡ ፵፪።

፲፬፡ መንገድ፡እንደ፡ *ወደ፡ ሰው፡ነውና። ባሮቹንም፡ ጸራ፡ከብቱንም፡ሰጣቸው።

*ሉቃ፡ ፲፱፡ ፲፪—፳፯።

፲፭፡ ላንዱም፡ አምስት፡ መክሊት፡ ሰጠው። ለሁለተኛውም፡ ሁለት፡ መክሊት። ለሶስተኛውም፡ አንድ፡ መክሊት። ለሁሉ፡እንደ፡ ችሎቱ። ከዚያ፡ወዲያም፡ ሔደ። ሮሜ፡ ፲፪፡ ፮። ፩፡ ቆሮ፡ ፲፪፡ ፬።

፲፮፡ አምስት፡ መክሊት፡የወሰደውም፡ሔደ፡ ነገደባትም፡ ሌላ፡ አምስት፡ መክሊትም፡ ጨመረባት።

፲፯፡ እንደሁም፡ ደግሞ፡ ሁለት፡ መክሊት፡ የወሰደው። እርሱ፡ ደግሞ፡ ሁለት፡ መክሊት፡ ሌላ፡ ጨመረባት።

፲፰፡ አንድ፡ መክሊት፡ ግን፡የወሰደው፡ሔደ፡ ምድርም፡ ቈፈረና፡ የጌታውን፡ ወርቅ፡ ቀበረ።

፲፱፡ ከብዙ፡ ዘመንም፡በኋላ፡የለዚያ፡ ባሮች፡ ጌታ፡ መጣ፡ ተቋጠራቸውም። ማ፡ ፲፰፡ ፳፫።

፳፡ አምስት፡መክሊት፡የወሰደውም፡መጣ፡አምስት፡ መክሊትም፡ ሌላ፡ ሰጠ፡እንዲህ፡ ሲል። አቤቱ፡ አምስት፡ መክሊት፡ ሰጠኸኝ። እነሆ፡ አምስት፡ መክሊት፡ ሌላ፡ ጨመርሁባት።

፳፩፡ ጌታውም፡ አለው። *አዎን፡ አንተ፡ መልካም፡ ባርያ፡ የታመንህም። በጥቂት፡ የታመንህ፡ እኔ፡ በብዙ፡ እሾምሃለሁ። ግባ፡ ወደ፡ ጌታህ፡ ደስታ።

*ማ፡ ፳፬፡ ፵፭። ሉቃ፡ ፲፮፡ ፲። ዕብ፡ ፲፪፡ ፪።

፳፪፡ ሁለት፡ መክሊትም፡ የወሰደው፡ መጣ፡ አለም። ጌታ፡ሆይ። ሁለት፡መክሊት፡ጣልህብኝ። እነሆ፡ ሁለት፡ መክሊት፡ ሌላ፡ አተረፍሁ።

፳፫፡ ጌታውም፡አለው።*አዎን፡አንተ፡መልካም፡ ባርያ፡ የታመንኸም። በጥቂት፡ የታመንህ፡ እኔ፡ በብዙ፡ እሾምሃለሁ። ግባ፡ ወደ፡ ጌታህ፡ ደስታ።

*ቍ፡ ፳፩።

፳፬፡ አንድ፡ መክሊትም፡ የወሰደ፡ መጣና፡ አለ። ጌታ፡ ሆይ፡ አወቅሁህ፡ ጽኑ፡ ሰው፡ እንደ፡ ሆንህ። ያልዘራኸውን፡ ታጭዳለህ፡ያልበተንኸውንም፡ ትሰበስባለኽ።

፳፭፡ እኔም፡ ፈራሁና፡ ሔድሁ፡ ወርቅህንም፡በምድር፡ ቀበርሁ። እነሆ፡ ከብትህ፡ ላንተ።

ምሳ፡ ፳፪፡ ፲፫።

፳፮፡ ጌታውም፡ መለሰ፡ አለውም። አንተ፡ ክፉ፡ ባርያ፡ ተግባረ፡ ፈትም። አወቅህ፡ ያልዘራሁትን፡እንደጭድ፡ ያልበተንሁትንም፡ እንድሰበስብ።

፳፯፡ ወርቄን፡ ለሰራፊች፡ጥለኸው፡እንደ፡ሆንህ፡ ይገባህ፡ነበር። እኔም፡ መጥቼ፡ከብቴን፡ከትርፉ፡ጋራ፡ አወሰደው፡ ነበርሁ።

፳፰፡ ስለዚህም፡ ያን፡ አንድ፡ መክሊት፡ ውሰዱበት፡ አሥር፡ መክሊትም፡ ላለው፡ ስጡት።

፳፱፡ ያለው፡ሁሉ፡ይሰጠዋልና፡ይጨመርለታልምና። የሌለው፡ ግን፡ ያው፡ ቅሉ፡ ያለው፡ ይሔድበታል።

ማ፡ ፲፫፡ ፲፪። ኤር፡ ፰፡ ፲፫።

፴፡ ታካቹንም፡ ባርያ፡ ወደ፡ ሚያ፡ *ጣሉት፡ ጨለማ፡ ወደሚሆንበት። ከዚያ፡ ልቅሶ፡ ይሆናል፡ ጥርስ፡ ማፋጨትም። *ማ፡ ፳፬፡ ፶፩።

፴፩፡ የሰው፡ ልጅ፡በምስጋናው፡በመጣ፡ ጊዜ፡ቅዱሳን፡ መላእክትም፡ ሁሉ፡ ከርሱ፡ ጋራ። የዚያን፡ ጊዜ፡ በምስጋናው፡ ዙፋን፡ ይቀመጣል። ፩፡ ተሰ፡ ፬፡ ፲፮።

፪፡ ተሰ፡ ፩፡ ፯።

፴፪፡ አሕዛብም፡ ሁሉ፡ *በፊቱ፡ ይሰበሰባሉ። እርሱ፡ በርሳቸውም፡ ይለያቸዋል፡ ጠባቂ፡ ተበጎችን፡ከፍየሎች፡እንዲለይ። *ሮሜ፡ ፲፬፡ ፲። ራእ፡ ፳፡ ፲፫።

ትሕዝ፡ ፴፬፡ ፲፯።

፴፫፡ በጎችንም፡ በቀኙ፡ ያቆማል፡ ፍየሎችንም፡ በግራው።

፴፬፡ የዚያን፡ ጊዜ፡ ንጉሡ፡በቀኙ፡ ያሉትን፡ ይላቸዋል። ኑ፡ ያባቴ፡ ቡሩካን። መንግሥትን፡ውረሱ፡ ዓለም፡ ሳይፈጠር፡ የተዘጋጀላችሁን። ኢሳ፡ ፷፭፡ ፳፫።

ዮሐ፡ ፲፯፡ ፳፬።

፴፭፡ ተርቤ፡ ነበርሁ፡ አበላችሁኝ። ተጠምቼ፡ ነበርሁ፡ አጠጣችሁኝም። ስደተኛ፡ ነበርሁ፡ተቀበላችሁኝ። ኢሳ፡ ፶፰፡ ፯።

፴፮፡ ታረዝሁ፡ አለበሳችሁኝ። ታመምሁ፡ ጎበኛችሁኝ። ታሥሬ፡ ነበርሁ፡ ወደኔ፡ መጣችሁ።

፴፯፡ የዚያን፡ ጊዜ፡ ጻድቃን፡ ይመልሱለታል፡እንዲህ፡ ሲሉ። አቤቱ፡መቼ፡ተርበህ፡አየነህ፡ አበላነህስ፡ ወይስ፡ ተጸምተህ፡አጠጣነህ። ም፡ ፮፡ ፫።

፴፰፡ መቼስ፡ እንግዳ፡ ሆነህ፡ አየነህ፡ ተቀበልነህም። ወይስ፡ታርዘህ፡ አለበስነህ።

፴፱፡ ወይስ፡ መቼ፡ ታመህ፡ ታሥረህስ፡ አየነህ፡ ወደንተም፡ መጣነ።

፵፡ ንጉሥም፡ መልሶ፡ ይላቸዋል። እውነት፡ እላችኋለሁ። ከለዚህ፡ ከታናሾች፡ ከወንድሞቼ፡ ላንዱ፡ ያደረጋችሁት፡ ለኔ፡ አደረጋችሁ። ም፡ ፲፡ ፵።

፩፡ ጴጥ፡ ፬፡ ፰። ያዕ፡ ፪፡ ፲፫።

፵፩፡ ከዚያ፡ ወዲያ፡ ደግሞ፡ በግራው፡ያሉን፡ ይላል። ከኔ፡ ሒዱ፡ እላንት፡ ርጉማን፡ ወደ፡ *ዘላለም፡ እሳት፡ ለሰይጣን፡ የተዘጋጀት፡ ለመልክተኞቹም።

*ኢሳ፡ ፴፡ ፴፫። ራእ፡ ፳፡ ፲፡ ፲፭።

፵፪፡ ተርቤ፡ ነበርሁ፡ አላበላችሁኝምና። ተጠማሁ፡ አላጠጣችሁኝም። ኢዮብ፡ ፳፪፡ ፮፡ ፯።

ያዕ፡ ፬፡ ፲፯።

፵፫፡ እንግዳ፡ሁኜ፡መጣሁ፡አልተቀበላችሁኝም።

ራቁቴን፡ ሆንሁ፡አላለበሳችሁኝም። ታመምሁ፡ታሠ
ርሁም፡አላያችሁኝም።
፵፬፡ የዚያን፡ ጊዜ፡ እርሳቸው፡ ደግሞ፡ ይመልሱ
ለታል፡ እንዲህ፡ ሲሉ። አቤቱ፡መቸ፡ ተርበህ፡አየነህ፡
ወይስ፡ ተጸምተህ። ወይስ፡ እንግዳ፡ ሁነህ። ወይስ፡
ታሥረህ፡ ያላገለገልነህ።
፵፭፡ የዚያን፡ ጊዜ፡ ይመልስላቸዋል፡ እንዲህ፡ ሲ
ል። እውነት፡ እላችኋለሁ። ከለዚህ፡ ከወንድሞቼ፡
ላንዱ፡ ያላደረጋችሁት፡ ለኔ፡ አላደረጋችሁም።
፵፮፡እለዚያም፡ወደ፡ዘላለም፡ሥቃይ፡ይሔዳሉ።
ጻድቃን፡ ግን፡ ወደ፡ ዘላለም፡ ሕይወት።
ዮሐ፡ ፭፡ ፴፱።

ምዕራፍ፡ ፳፮፡

፩፡ የሱስም፡ ይህነን፡ ነገር፡ ሁሉ፡ በፈጸመ፡ ጊዜ፡ ለ
ደቀ፡ መዛሙርቱ፡ አለ። ማር፡ ፲፬፡ ሉቃ፡ ፳፪።
፪፡ አወቃችሁ፡ ፋሲካ፡ ከሁለት፡ ቀን፡ በኋላ፡ እን
ዲሆን። የሰው፡ ልጅም፡ ይሰጣል፡ ሊሰቀል።
ም፡ ፳፡ ፲፰።
፫፡ የዚያን፡ ጊዜ፡ ተከማቹ፡ የካህናት፡ አለቆች፡ ጻ
ፎችም፡ የሕዝቡም፡ ሽማግሎች፡ በሊቀ፡ ካህናቱ፡ ቤ
ት፡ ቀያፋ፡ የሚሉት።
፬፡ ባንድም፡ ተማከሩ፡ የሱስን፡ በተንኰል፡ ይዙ
ትና፡ ይገድሉት፡ ዘንድ።
፭፡ አሉም፡በበዓል፡አይሆንም። ሁከት፡በሕዝብ፡
እንዳይሆን።
፮፡ የሱስም፡ በቢታንያ፡ ሳለ፡ በሲሞን፡ በለምጻ
ሙ፡ ቤት። ዮሐ፡ ፲፪፡ ፩።
፯፡ ሴት፡ ወደርሱ፡መጣች፡ ከርስዋ፡ጋራም፡የሽቱ፡
ቢረሌ፡ነበረ፡ ዋጋው፡ የበዛ። በራሱም፡ ላይ፡ አፈሰሰ
ችው። እርሱም፡ ለመብል፡ ተቀምጦ፡ ነበር።
ሉቃ፡ ፯፡ ፴፯።
፰፡ ደቀ፡ መዛሙርቱም፡ ያነን፡ባዩ፡ ጊዜ፡ ተቈጡ፡
እንዲህ፡ ሲሉ፡ ለምን፡ ይህነን፡ ያህል፡ ጥፋት።
፱፡ ይህ፡ በብዙ፡ ዋጋ፡ ይሸጥ፡ ነበረና፡ ለድኆችም፡
ይሰጥ፡ነበረ።
፲፡ የሱስም፡ አስተውሎ፡ እንዲህ፡ አለ። ለምን፡
ይህችን፡ ሴት፡ ታታክትዋታላችሁ። መልካም፡ ማድ
ረግ፡ በኔ፡ አድርጋለችና።
፲፩፡ ድኆች፡ ሁለጊዜ፡ከላንት፡ጋራ፡ናቸውና። እኔ፡
ግን፡ ሁለግዜ፡ ከላንት፡ ጋራ፡ አልኖርም።
ዘዳግ፡ ፲፭፡ ፲፩።
፲፪፡ ይህችም፡ ይህነን፡ ሽቱ፡ በሥጋዬ፡ ላይ፡ ባፈሰሰ
ችው፡ ጊዜ፡ ለመቃብሬ፡ አደረገችው።
፲፫፡ እውነት፡ እላችኋለሁ። ይህች፡ ወንጌል፡ በተ
ሰበከችበት፡ ሰፍራ፡ሁሉ፡በዓለም፡ሁሉ፡ይህች፡ሴት፡
ያደረገችው፡ደግሞ፡ ለርስዋ፡ መታሰቢያ፡ ሁና፡ ይነገ
ራል።
፲፬፡ የዚያን፡ ጊዜ፡ ካሥራ፡ ሁለቱ፡ አንዱ፡ ስሙን፡
ይሁዳ፡ የሚሉት፡ የአስቆሮቱ፡ ወደ፡ ካህናት፡ አለቆ
ች፡ ሔደ።
፲፭፡ አለም። *ምን፡ትሰጡኛላችሁ፡እኔም፡አሲዛ
ችኋለሁ። እርሳቸውም፡ተሰማሙ፡ ከርሱ፡ ጋራ፡ †በ
ሠላሳ፡ ቅርሽ። *ዮሐ፡ ፲፩፡ ፴፯። †ዘካ፡ ፲፩፡ ፲፪።
፲፮፡ ከዚያችም፡ ጊዜ፡ ጀምሮ፡ ምቹ፡ ጊዜያት፡ ይ
ሻ፡ ነበረ፡ አሳልፎ፡ ሊሰጠው። ፩፡ ጢሞ፡ ፮፡ ፱፡ ፲።
፲፯፡ *ከፋሲካም፡ አስቀድሞ፡ በነበረው፡ ቀን፡ ደ
ቀ፡ መዛሙርቱ፡ ወደ፡ የሱስ፡ መጡ፡ እንዲህ፡ ሲሉ።
ወዴት፡ ትወዳለህ፡ እናዘጋጅልህ፡ ዘንድ፡ ፋሲካ፡ ል
ትበላ። *ዘፀአ፡ ፲፪፡ ፲፰፡—፳።
፲፰፡ እርሱም፡አለ፡ወደ፡ አገር፡ ሒዱ፡ወደ፡ እገሌ፡
እንዲህም፡ በሉት። መምህር፡ይላል፡ጊዜዬ፡ ደርስዋ
ል፡ ካንተ፡ ዘንድ፡ ፋሲካ፡ ላድርግ፡ ከደቀ፡ መዛሙር
ቴ፡ጋራ። ም፡ ፳፩፡ ፫።
፲፱፡ ደቀ፡ መዛሙርቱም፡ አደረጉ፡ የሱስ፡ እንዳዘ
ዛቸው፡ ፋሲካንም፡ አዘጋጁ።
፳፡ በመሸም፡ጊዜ፡ተቀመጠ፡ካሥራ፡ሁለቱ፡ጋራ።
፳፩፡ ሲበሉም፡ አለ። እውነት፡ እላችኋለሁ። ከላ
ንት፡ አንዱ፡ አሳልፎ፡ ይሰጠኛል።
ዮሐ፡ ፲፫፡ ፳፩—፳፮።
፳፪፡ እጅግም፡ አዘኑ፡ከርሳቸውም፡ኢያንዳንዱ፡
ይለው፡ ጀመረ። እንዳች፡ እኔ፡ እሆን፡ አቤቱ።
፳፫፡ እርሱም፡ መለሰ፡ አለም። እጁን፡ ወደ፡ ወ
ጭ፡ እቃ፡ ከኔ፡ ጋራ፡ የሚጠልቅ፡ እርሱ፡ አሳልፎ፡ ይሰ
ጠኛል። ዮሐ፡ ፲፫፡ ፲፰።
፳፬፡ የሰው፡ ልጅ፡ ግን፡ ይሔዳል፡ ስለርሱ፡ እንደ፡
ተጻፈ። ነገር፡ ግን፡ ወዮለት፡ ለዚያ፡ ሰው፡ በርሱ፡ምክ
ንያት፡ የሚሰጥ፡ የሰው፡ ልጅ። ያሰውስ፡ ባይወለድ፡
መልካም፡ ነበረለት።
፳፭፡ ይሁዳም፡አሳልፎ፡የሚሰጠው፡ መለሰ፡ አለ
ም። እንዳች፡እኔ፡እሆን፡መምህር፡ሆይ። አለውም፡
አንተ፡ አልህ።
፳፮፡ እርሳቸውም፡ ሲበሉ፡ የሱስ፡ እንጀራ፡ ያዘ፡
ባረከውም፡ ቈረሰውም፡ ለደቀ፡ መዛሙርቱም፡ ሰ
ጠ፡ አለም፡ ንሡ፡ ብሉ። ይህ፡ ሥጋዬ፡ ነው።
፩፡ ቆር፡ ፲፩፡ ፳፫—፳፱።
፳፯፡ ጽዋም፡ ተቀበለ፡ አመሰገነም፡እንዲህ፡ሲል
ም፡ ሰጣቸው። ከዚህ፡ ጠጡ፡ ሁላችሁ።
፳፰፡ ይህ፡ *ደሜ፡ ነውና፡ †ላዲስ፡ ሥርዓት፡ ስለ፡
ብዙ፡ ሰዎች፡ የሚፈስ፡ ኃጢአት፡ ለመስተስረይ።
*ዘፀአ፡ ፳፬፡ ፰። †ኤር፡ ፴፩፡ ፴፩። ዘካ፡ ፱፡ ፲፩።
፳፱፡ እላችሁማለሁ። ከዛሬ፡ ጀምሬ፡ ከዚህ፡ ከ
ወይን፡ ፍሬ፡ እንዳልጠጣ፡ እስከዚያ፡ቀን፡ ድረስ፡ አ
ዲሱን፡ እስከምጠጣበት፡ ከላንት፡ ጋራ፡ ባባቴ፡ መን
ግሥት።
፴፡ ባመሰገኑም፡ *ጊዜ፡ወደ፡ ደብረ፡ዘይት፡ወጡ።
*መዝ፡ ፻፲፫፡—፻፲፰።
፴፩፡ የዚያን፡ ጊዜ፡ የሱስ፡ አላቸው። ሁላችሁ፡ በ

ዚኽ፡ ሌሊት፡ ትክዱኛላችሁ። ተጽፏዋልና። *ጠባቂውን፡ እመታለሁ፡ የመንጋውም፡ በጎች፡ ይበተናሉ።
*ዘካ፡ ፲፫፡ ፯። ዮሐ፡ ፲፮፡ ፴፪።

፴፪፤ ነገር፡ ግን፡በተነሣሁ፡ ጊዜ፡ ወደ፡ገሊላ፡ እቀድማችኋለሁ። ም፡ ፳፰፡ ፯።

፴፫፤ ጴጥሮስም፡ መለሰ፡አለውም። ሁሉ፡ ቢክዱህ፡ እኔ፡ ከቶ፡ አልክድህም።

፴፬፤ የሱስም፡አለው። እውነት፡ እልሃለሁ። በዚኽ፡ ሌሊት፡ ዶሮ፡ ሳይጮህ፡ አስቀድመህ፡ሦስት፡ ጊዜ፡ እንድትክደኝ። ዮሐ፡ ፲፫፡ ፴፰።

፴፭፤ ጴጥሮስም፡ አለው። ካንተ፡ ጋራ፡ የምሞት፡ ብሆን፡ ከቶ፡ አልክድህም። እንዲህም፡ አሉ፡ *ደቀ፡ መዛሙርቱ፡ ሁሉ። *ቍ፡ ፶፮።

፴፮፤ ከዚያ፡ ወዲያ፡የሱስ፡ ከርሳቸው፡ ጋራ፡ወደ፡ ስፍራ፡ መጣ፡ ጌትሴማኔ፡ ወደምትባል። ደቀ፡ መዛሙርቱንም፡ አለ። ከዚህ፡ ተቀመጡ፡ ከዚያ፡ ሒጄ፡ እስክጸልይ፡ ድረስ።

፴፯፤ ከርሱ፡ጋራም፡ጴጥሮስንና፡ የዘብዴዎስን፡ ሁለት፡ ልጆች፡ ወስዶ፡ *ያዝንም፡ ይተክዝም፡ ጀመረ። *ዕብ፡ ፭፡ ፯።

፴፰፤ የዚያን፡ ጊዜ፡ አላቸው። ነፍሴ፡ አዘነች፡ እስከ፡ሞት፡ድረስ። ከዚህ፡ተቀመጡ፡ከኔም፡ጋራ፡ትጉ። ዮሐ፡ ፲፪፡ ፳፯።

፴፱፤ ጥቂትም፡ ፈቀቅ፡ አለ፡ በግምባሩም፡ ሰግዶ፡ ኢየጸለየ፡ እንዲህም፡ ኢያለ። አባቴ፡ ሆይ፡ ይቻል፡ እንደ፡ሆንስ፡ ይህች፡ *ጽዋ፡ከኔ፡ትለፍ፡ ነገር፡ ግን፡እኔ፡ እንደወድ፡ †አይደለም። አንተ፡ እንድትፈቅድ፡ እንጂ። *ዮሐ፡ ፲፰፡ ፲፩። †ዕብ፡ ፭፡ ፰።

፵፤ ወደ፡ደቀ፡መዛሙርቱም፡መጣ፡ተኝተውም፡ አገኛቸው። ጴጥሮስንም፡አለው። እንዲህም፡አልቻላችሁምን፡ ከኔ፡ ጋራ፡ አንዲት፡ ሰዓት፡ ትተጉ፡ዘንድ።

፵፩፤ ጸልዩ፡ትጉም፡ ወደ፡መከራ፡እንዳትገቡ። ነፍስስ፡ ተዘጋጅታለች፡ *ሥጋ፡ ግን፡ ደካማ፡ ነው። ም፡ ፬፡ ፲፭። *ዕብ፡ ፪፡ ፲፬።

፵፪፤ ደግሞ፡ ሁለተኛም፡ ሔዶ፡ ጸለየም፡ እንዲህ፡ ሲል። አባቴ፡ ሆይ፡ የማይቻል፡ እንደሆን፡ ይህች፡ ጽዋ፡ከኔ፡ታልፍ፡ ዘንድ፡ሳልጠጣት፡ፈቃድህ፡ትሁን።

፵፫፤ መጣም፡ ደግሞም፡ ተኝተው፡ አገኛቸው። ዓይኖቻቸው፡ በንቅልፍ፡ ከብደው፡ ነበሩና።

፵፬፤ ተዋቸውም፡ ደግሞም፡ ሔዶ፡ *ሦስተኛም፡ ጸለየ፡ የቀደመውን፡ነገሩንም፡ አለ። *፪፡ ቆሮ፡ ፲፪፡ ፰።

፵፭፤ ከዚያ፡ ወዲያ፡ ወደ፡ ደቀ፡ መዛሙርቱ፡ መጣ፡ አላቸውም። እንግዴህ፡ተኙ፡ዕረፉም። እነሆች፡ ደረሰች፡ ጊዜዪቱ፡ የሰው፡ ልጅም፡ በኃጢአተኞች፡ እጅ፡ ይሰጣል።

፵፮፤ ተነሡ፡እንሒድ። እነሆ፡ አሳልፎ፡ የሚሰጠኝ፡ አሁን፡ ደረሰ።

፵፯፤ እርሱም፡ ሲናገር፡ እነሆ፡ ይሁዳ፡ ካሥራ፡ ሁለቱ፡ አንዱ፡ መጣ፡ ከርሱ፡ ጋራም፡ ብዙ፡ ሰዎች፡ በሰይፍ፡ በጎመድም፡ ከካህናት፡ አለቆች፡ ዘንድ፡ከሕዝቡም፡ ሽማግሎች።

፵፰፤ አሳልፎ፡ የሰጠውም፡ መልክት፡ ሰጣቸው፡ እንዲህ፡ ሲል። የምስመው፡ እርሱ፡ ነው፡ ያዙት።

፵፱፤ የዚያን፡ ጊዜውም፡ ወደ፡ የሱስ፡ ቀረበ፡ አለም። ደኅና፡ ነህ፡ መምህር፡ ሆይ። እጅ፡ ነሣውም።

፶፤ የሱስም፡ አለው። ወዳጄ፡ ሆይ፡ ለምን፡ ነገር፡ መጣህ። የዚያን፡ ጊዜ፡ መጡ፡ እጃቸውንም፡ በየሱስ፡ ላይ፡ ጫኑ፡ያዙትም። መዝ፡ ፶፩፡ ፲፬።

፶፩፤ እነሆ፡ አንዱም፡ ከየሱስ፡ጋራ፡ከነበሩት፡እጁን፡ ዘረጋ፡ሰይፉንም፡ መዘዘ፡ የካህናቱንም፡ አለቃ፡ ባርያ፡ መታው፡ ጆሮውንም፡ ቈረጠው። ዘፍ፡ ፱፡ ፮። ራእ፡ ፲፫፡ ፲።

፶፪፤ የዚያን፡ጊዜ፡የሱስ፡ አለው፡ ሰይፍህን፡ መልስ፡ወደፊቱ። ሰይፍ፡ የሚያነሡ፡ ሁሉ፡ በሰይፍ፡ ይጠፋሉ።

፶፫፤ ወይስ፡ የማልችልን፡ ይመስልሃል፡ አሁን፡ ወደ አባቴ፡ እለምን፡ ዘንድ፡ ከመላእክትም፡ ካሥራ፡ ሁለት፡ ጭፍሮች፡ የሚበልጥ፡ ይሰድልኛል። ደን፡ ፯፡ ፲።

፶፬፤ ነገር፡ ግን፡ እንዴት፡ ይፈጸማሉ፡ መጻሕፍት፡ እንዲህ፡ ይሆን፡ ዘንድ፡ እንዲገባ።

፶፭፤ በዚያች፡ ጊዜ፡ የሱስ፡ ለሕዝቡ፡ አለ። እንደ፡ ሌባን፡ ልትዙኝ፡በሰይፍና፡ በጎመድ፡ ወጣችሁ። ሁሉ ግዜ፡ ከላንት፡ ጋራ፡እኖር፡ ነበርሁ፡ በቤተ፡ መቅድስ፡ ተቀምጬ፡ ሳስተምር፡ አልያዛችሁኝምም። ዮሐ፡ ፲፰፡ ፳።

፶፮፤ ነገር፡ግን፡ ይህ፡ ሁሉ፡ የሆነ፡ የነቢያት፡ መጻሕፍት፡ ይፈጸም፡ ዘንድ፡ ነው። *የዚያን፡ ጊዜ፡ ደቀ፡ መዛሙርቱ፡ ሁሉ፡ ጥለውት፡ሸሹ። *የሐዋ፡ ፲፫፡ ፳፯።

፶፯፤ የሱስን፡ ግን፡ የያዙት፡ ወደ፡ ቀያፋ፡ ወደ፡ *ካህናት፡ አለቃ፡ ወሰዱት። ጸፎች፡ ወደ፡ ተከማቹበት፡ ሽማግሎችም። *ዮሐ፡ ፲፰፡ ፲፫—፳፬።

፶፰፤ ጴጥሮስ፡ ግን፡ ከሩቅ፡ ተከተለው፡ እስከ፡ ካህናት፡አለቃ፡ቤት፡ ድረስ። ወደ፡ውሥጥም፡ገባ፡ከሎሌቱም፡ ጋራ፡ ተቀመጠ፡ ፍጻሜውን፡ ያይ፡ ዘንድ።

፶፱፤ የካህናት፡ አለቆች፡ ግን፡ ጸፎችም፡ ሸንጎው ም፡ ሁሉ፡ ያሰት፡ ምስክሮች፡ በየሱስ፡ ላይ፡ ይሹ፡ ነበሩ፡ ሊገሉት። አላገኙምም።

፷፤ምንስ፡ብዙ፡የሐሰት፡ምስክሮች፡በመጡ፡ጊዜ፡ አላገኙምም። ከዚያ፡ በኋላም፡ መጡ፡ ሁለት፡ ያሰት፡ ምስክሮች።

፷፩፤ አሉም። ይህ፡አለ፡ *የእግዚአብሔርን፡ቤት፡ አፈርሰው፡ ዘንድ፡ በሦስት፡ ቀንም፡ እሰራው፡ ዘንድ፡ እችላለሁ። ዮሐን፡ ፪፡ ፲፱—፳፬።

፷፪፤ የካህናቱ፡ አለቃም፡ ተነሣ፡እንዲህም፡አለ። ጥቂት፡ አትመልስምን። እሌህ፡ የሚመሰክሩብህ፡ ምንድር፡ ነው።

፷፫፤ የሱስም፡ *ዝም፡ብሎ፡ ነበረ። የካህናት፡ አለ

ቃም፡መለሰ፡አለም። በሕያው፡እግዚአብሔር፡አምልሃለሁ፡ እንድትነግረን፡ አንተ፡ክርስቶስ፡የእግዚአብሔር፡ ልጅ፡ እንደ፡ ሆንህ። ም፡ ፳፯፡ ፲፬።

፷፬፡ የሱስም፡ አለው። አንተ፡ አልህ። እኔ፡ ግን፡ እላችኋለሁ። ከዚህ፡ በኋላ፡ የሰው፡ልጅ፡ በኃይል፡ ቀኝ፡ *ሲቀመጥ፡ እንድታዩ፡ በሰማይም፡ ደመና፡ ሲመጣ። *ም፡ ፲፮፡ ፳፯፡ መዝ፡ ፻፲፡ ፩። ዳን፡ ፯፡ ፲፫፡ ፲፬።

፷፭፡ የዚያን፡ ጊዜ፡ የካህናት፡ አለቃ፡ ልብሱን፡ ቀደደ፡ እንደህ፡ሲል። እነሆ፡ሰደበ። ምን፡ አግደን፡ እንጊደህ፡ ወደ፡ ምስክር። እነሆ፡ አሁን፡ ስድቡን፡ ሰማችሁ። ዮሐ፡ ፲፡ ፴፫።

፷፮፡ እንጊደህ፡ ምን፡ትላላችሁ። እርሳቸው፡ግን፡ መለሱ፡ አሉም፡ *ደህ፡ ሞት፡ ይገባዋል።

*ዮሐ፡ ፲፱፡ ፯።

፷፯፡ የዚያን፡ ጊዜ፡ በፊቱ፡ ተፋበት፡ ጸፋትም፡ ሌሎችም፡ መቱት፡ እንደህ፡ ሲሉ። ኢሳ፡ ፶፡ ፮።

፷፰፡ ትንቢት፡ ንገረን፡ክርስቶስ፡ሆይ። ማነው፡ የጸፋህ።

፷፱፡ ጴጥሮስ፡ ግን፡ ካደራሽ፡ በሜዳ፡ ተቀምጦ፡ ነበረ። አንዲትም፡ ባርያ፡ወደርሱ፡ መጣች፡ እንደህ፡ ስትል። አንተም፡ደግሞ፡ ከገሊላው፡ ከየሱስ፡ ጋራ፡ ነበርህ። ዮሐ፡ ፲፰፡ ፲፭—፳፯።

፸፡ እርሱም፡ በሕዝብ፡ሁሉ፡ ፊት፡ ካደ፡ እንደህ፡ ሲል። የምትዪን፡ አላውቅም።

፸፩፡ ወደ፡ ደጅም፡በወጣ፡ጊዜ፡ሌላዪቱ፡አየችው፡ ከዚያም፡ ላሉት፡ አለች። ይህም፡ ከናዝሬቱ፡ ከየሱስ፡ ጋራ፡ ነበረ። ዮሐ፡ ፲፰፡ ፭።

፸፪፡ ደግሞም፡ በመሐላ፡ ካደ። ይህነን፡ሰው፡ አላውቀውም።

፸፫፡ ጥቂትም፡ ቈይተው፡ ቁመው፡ የነበሩት፡ መጡ፡ ጴጥሮስንም፡አሉት። በውነት፡ አንተም፡ከርሳቸው፡ ወገን፡ ነህ። ነገርህ፡ ደግሞ፡ ያስታውቅሃልና።

፸፬፡ በዚያን፡ጊዜ፡ ይረግም፡ ይምልም፡ ጀመረ፡ ይህነን፡ ሰው፡ አላውቀውም። በዚያን፡ ጊዜም፡ ዶሮ፡ ጮኸ።

፸፭፡ ጴጥሮስም፡ የየሱስን፡ ነገር፡ አሰበ፡ ያለውን። *ዶሮ፡ ሳይጮህ፡ ሶስት፡ ጊዜ፡ትክደኛለህ። ወደ፡ሜዳም፡ ወጣ፡ መራራ፡ ልቅሶም፡ አለቀሰ። *ቍ፡ ፴፬።

## ምዕራፍ፡ ፳፯፡

፩፡ *በጸባም፡ ጊዜ፡ የካህናት፡ አለቆች፡ ሁሉ፡ የሕዝቡም፡ ሽማግሌዎች፡ በየሱስ፡ ላይ፡ ተማከሩ፡ ይገድሉት፡ ዘንድ። *ማር፡ ፲፭፡ ፩። ሉቃ፡ ፳፪፡ ፷፮።

ዮሐ፡ ፲፰፡ ፲፰።

፪፡ አሠሩትም፡ይዘውትም፡ሔደ። ለጴንጤኑም፡ ለጲላጦስ፡ለሹሙ፡ አሳልፈው፡ሰጡት።

፫፡ የዚያን፡ጊዜ፡ አሳልፎ፡ የሰጠው፡ ይሁዳ፡ እንደ፡ ቀፈረደበት፡ ባየ፡ ጊዜ፡ ጠጠተው፡ ሠላሳውንም፡ ቅርሽ፡ ወደ፡ ካህናቱ፡ አለቆች፡ መለሰው፡ ወደ፡ ሽማግሌዎችም፡ እንደህ፡ ሲል። ም፡ ፳፮፡ ፲፭።

፬፡ ንጹሕ፡ ደም፡ አሳልፌ፡ በመስጠቴ፡ በደልሁ። እርሳቸውም፡ አሉ። እኛን፡ ምን፡ አግደነ። አንተ፡ እወቅ።

፭፡ ያነንም፡ ብር፡ በቤተ፡ መቅደስ፡ ጣለና፡ ሔደ፡ *ታንቆም፡ ሞተ። *የሐዋ፡ ፩፡ ፲፰።

፪፡ ሳሙ፡ ፲፯፡ ፳፫።

፮፡ የካህናትም፡ አለቆች፡ ብሩን፡ ወሰዱ፡ እንደህም፡ አሉ። ወደ፡ ቍርባን፡ ቤት፡ እንጨምረው፡ ዘንድ፡ አይገባንም። የደም፡ ዋጋ፡ ነውና። ማር፡ ፲፪፡ ፵፩።

፯፡ ተማከሩም፡ የሸቃ፡ ሰሪ፡ምድርም፡ *ገዙበት፡ ለንግዶች፡መቃብር። *የሐዋ፡ ፩፡ ፲፱።

፰፡ ስለዚህም፡ ያ፡ምድር፡የደም፡ ምድር፡ ተብሎ፡ ተጸራ፡ እስከ፡ ዛሬ።

፱፡ በዚያን፡ ጊዜ፡ ተፈጸመ፡ በነቢዩ፡ በኤርምያስ፡ የተባለው፡ እንደህ፡ ሲል። ሠላሳውንም፡ ቅርሽ፡ወሰዱ፡ የክቡሩን፡ ዋጋ፡ የእሥራኤል፡ልጆች፡የተሰማሙበትን። ዘካ፡ ፲፩፡ ፲፪፡ ፲፫። ኤር፡ ፴፫፡ ፯።

፲፡ ስለ፡ ሸቃ፡ ሰሪ፡ ምድርም፡ ሰጡት፡ እግዚአብሔር፡ እንደዘዘኝ።

፲፩፡ የሱስም፡ በሹሙ፡ ፊት፡ቆመ። ሹሙም፡ ጠየቀው፡ እንደህ፡ ሲል። አንተን፡ነህ፡የአይሁድ፡ንጉሥ። የሱስም፡ አለው። አንተ፡ አልህ። ማር፡ ፲፭፡ ፪።

ሉቃ፡ ፳፫። ዮሐ፡ ፲፰፡ ፳፰—፵።

፲፪፡ የካህናትም፡ አለቆች፡ ሽማግሌዎችም፡ ሲያሳጡት፡ በምንም፡ *አልመለሰላቸውም።

*ኢሳ፡ ፶፫፡ ፯።

፲፫፡ የዚያን፡ ጊዜ፡ አለው፡ ጲላጦስ። በስንት፡ነገር፡ እንዲመሰክሩብህ፡ አትሰማምን።

፲፬፡ አልመለሰለትምም፡ ባንዲት፡ቃል፡ ስንኳ፡ ሹሙ፡ እጅግ፡ እስኪያደንቅ፡ ድረስ።

፲፭፡ በየበዓሉም፡ ሁሉ፡ ለሹሙ፡ ልማድ፡ ነበረው፡ ለሕዝብ፡አንድ፡ የታሠረ፡ ይተውላቸው፡ ዘንድ፡ ከታሠሩት፡ የወደዱትን።

፲፮፡ የዚያን፡ ጊዜም፡ አንድ፡ የታሠረ፡ ነበረ፡ የታወቀ፡ በርባን፡ የሚባል።

፲፯፡ እርሳቸውም፡ ተከማችተው፡ ሳሉ፡ ጲላጦስ፡ አላቸው። ማነን፡ ትወዳላችሁ፡እተውላችሁ፡ዘንድ። በርባንን፡ ወይስ፡ የሱስን፡ ክርስቶስ፡ የሚባለውን።

፲፰፡ ያውቅ፡ ነበርና፡ በቅናት፡ አሳልፈው፡ እንደ፡ ሰጡት።

፲፱፡ እርሱም፡ በወንበር፡ ተቀምጦ፡ ሳለ፡ ምሽቱ፡ ላከችበት፡እንደህ፡ስትል። ተጠንቀቅ፡በዚያ፡ጻድቅ፡ ክፉ፡ አትስራ። ዛሬ፡ እጅግ፡ መከራ፡ በሕልም፡ ስለርሱ፡ተቀብያለሁና።

፳፡ የካህናት፡አለቆች፡ግን፡ሽማግሌዎችም፡ሕዝቡን፡ አባበሉ፡ በርባንን፡ ለማደን፡ ይለምኑ፡ ዘንድ፡ የሱስንም፡ ለመግደል።

፳፩፤ ኹሙም፡መለሰ፡እንደ ህም፡አላቸው። ከሁ
ለቱ፡ ማናቸውን፡ እተውላችሁ፡ ዘንድ፡ ትሻላችሁ።
እርሳቸውም፡ አሉ። በርባንን።
፳፪፤ጲላጦስም፡አላቸው።በየሱስም፡ክርስቶስ፡በ
ሚባለው፡ምን፡ ልስራበት። ሁሉም፡አሉ። ይሰቀል።
፳፫፤ ኹሙም፡ አለ። ምን፡ ክፉ፡ አደረገ። እርሳቸ
ው፡ግን፡ ጩኸት፡ አበዙ፡ እንደ ህ፡ ሲሉ። ይሰቀል።
፳፬፤ ጲላጦስም፡ አንዳች፡ እንዳይረባ፡ ባየ፡ ጊዜ፡
ነገር፡ ግን፡ ሁከት፡ እንደበዛ፡ እንጅ፡ ውኃ፡ አስመጣ፡
በሕዝቡም፡ፊት፡ *እጁን፡ ታጠበ፡ እንደ ህ፡ ሲል። እ
ኔ፡ ከዚ ህ፡ ጻድቅ፡ደም፡ንጹሕ፡ነኝ። እላንተ፡ እወቁ።
*ዘዳግ፡ ፳፩፡ ፮፡፡
፳፭፤ ሕዝቡ፡ ሁሉም፡ መለሱ፡ እንደ ህም፡ አሉ።
*ደሙ፡ በኛ፡ በልጆቻችንም፡ ላይ፡ ይሁን።
*የሐዋ፡ ፭፡ ፳፰፡፡ ዘዳግ፡ ፲፱፡ ፲፡፡
፳፮፤ የዚያን፡ ጊዜ፡ በርባንን፡ ተወላቸው፡ የሱስን
ም፡ ገረፈው፡ ሊሰቀልም፡ አሳልፎ፡ ሰጠው።
፳፯፤ ከዚያ፡ ወዲያም፡ የኹሙ፡ ጭፍሮች፡ የሱስ
ን፡ ወደ፡አደራሽ፡ወሰዱት፡ ጭፍራውንም፡ሁሉ፡አከ
ማቹበት። ዮሐ፡ ፲፱፡፡
፳፰፤ ልብሱንም፡ ገፈፉት፡ ቀይ፡ ቡርኑስም፡አለበ
ሱት።
፳፱፤ የሾህ፡ አክሊልም፡ ጉነጉኑ፡ በራሱ፡ ላይም፡
ጫኑ፡ ዘንግም፡ በቀኝ፡ እጁ፡ አስያዙት፡ በፊቱም፡ በ
ጉልበታቸው፡ ተምበረከኩ፡ ተሣለቅበትም፡ እንደ
ህ፡ ሲሉ። ይህንነት፡ላንተ፡ ይሁን፡የአይሁድ፡ ንጉሥ፡
ሆይ።
፴፤ በላዩም፡ *ይተፉበት፡ ነበረ፡ ዘንጉንም፡ነሡና፡
ራሱን፡ መቱበት። *ኢሳ፡ ፶፡ ፮፡፡
፴፩፤ ካፌዙበትም፡ ወዲያ፡ ያለበሱትን፡ ቡርኑስ፡
ገፈፉት፡ ልብሱንም፡ አለበሱት፡ ሊሰቅሉትም፡ ወሰ
ዱት።
፴፪፤ ሲወጡም፡ ያቂሬና፡ ሰው፡አገኙ፡ስሙን፡ ሲ
ሞን፡ የሚሉት። እርሱን፡ ጉተቱት፡ መስቀሉን፡ ይሸ
ከም፡ ዘንድ። ዕብ፡ ፲፫፡ ፲፪፡ ፲፫፡፡
፴፫፤ ጎልጎታም፡ ወደሚሉት፡ ስፍራ፡ በደረሱ፡ ጊ
ዜ፡ ትርጓሚውን፡ የራስ፡ ቦታ፡ ወደሚሉት።
፴፬፤ ባሞት፡ የተደባለቀ፡ *መጻጻ፡ ሰጡት። ቀመ
ሰም፡ ሊጠጣም፡ እምቢ፡ አለ። *መዝ፡ ፷፱፡ ፳፪፡፡
፴፭፤ በሰቀሉትም፡ ጊዜ፡ ልብሱን፡ ተካፈሉት፡ዕፃ
ም፡ ተጣጣሉበት፡ ይፈጸም፡ ዘንድ፡ በነቢዩ፡ የተባለ
ው። *ልብሶቼን፡ተካፈሉ፡እርሱ፡ በርሳቸው፡ በቀሚ
ሴም፡ ላይ፡ ዕፃ፡ ተጣጣሉ። *መዝ፡ ፳፪፡ ፲፱፡፡
፴፮፤ ከዚያም፡ ተቀምጠው፡ ይጠብቁት፡ ነበረ።
፴፯፤ በራሱ፡ በላይም፡ ኃጢአቱን፡ አኖሩ፡ ተጽፎ፡
እንደ ህ፡ስትል። ይህ፡የሱስ፡ነው፡የአይሁድ፡ንጉሥ።
፴፰፤ የዚያን፡ጊዜ፡ ሁለት፡ወንበዴች፡ ከርሱ፡ጋራ፡
ተሰቀሉ። አንዱ፡ በቀኙ፡ አንዱም፡ በግራው።
ኢሳ፡ ፶፫፡ ፲፪፡፡

፴፱፤ በርሱም፡ የሚያልፉ፡ይሰድቡት፡ነበረ፡ *ራሳ
ቸውን፡ ኢያነቃነቁ፡ ኢያሉም። *መዝ፡ ፳፪፡ ፯፡፡
፵፤ ቤተ፡ መቅደስን፡ *የምታፈርስ፡ ሆይ፡ በሶስት፡
ቀንም፡ የምትሰራው፡ ራስህን፡ አድን። የእግዚአብ
ሔር፡ ልጅስ፡ እንደ፡ ሆንህ፡ ከመስቀል፡ ውረድ።
*ዮሐ፡ ፪፡ ፲፱፡፡
፵፩፤ እንደ ሁም፡ ደግሞ፡ የካህናት፡አለቆች፡ ከጻ
ፎች፡ ከሽማግሎችም፡ ጋራ፡ ያፌዙበት፡ ይሉትም፡ ነ
በረ።
፵፪፤ ሌሎችን፡አዳነ። ራሱን፡ማዳን፡ አልቻለም።
እርሱ፡ የእሥራኤል፡ ንጉሥ፡ እንደ፡ ሆነ፡ አሁን፡ ከመ
ስቀል፡ ይውረድ፡ እኛም፡ እንመንበት።
፵፫፤ *በእግዚአብሔር፡ታምኖ፡ነበረ። አሁን፡ ያድ
ነው፡ ቢወደውስ። እኔ፡የእግዚአብሔር፡ ልጅ፡ ነኝ፡ ብ
ልዋልና። *መዝ፡ ፳፪፡ ፱፡፡
፵፬፤ እንደ ሁም፡ ደግሞ፡ ወንበዴች፡ ከርሱ፡ ጋራ፡
የተሰቀሉት፡ ይላገዱበት፡ ነበረ።
፵፭፤ ከስድስትም፡ ሰዓት፡ ጀምሮ፡ ጨለማ፡ ሆነ፡
በምድር፡ ሁሉ፡ ላይ፡ እስከ፡ ዘጠኝ፡ ሰዓት።
፵፮፤ በዘጠኝ፡ ሰዓት፡ጊዜም፡የሱስ፡በታላቅ፡ቃል፡
ጮኸ፡እንደ ህ፡ሲል። *ኤሎሄ፡ኤሎሄ፡ለማ፡ሰበቅታ
ኒ። እርሱ፡ የሚሆን። አምላኬ፡አምላኬ፡ ለምን፡ ተ
ውኸኝ። *መዝ፡ ፳፪፡ ፪፡፡
፵፯፤ ሕዝብም፡ከዚያ፡ ከቆሙት፡ወገን፡ በሰሙ፡
ጊዜ፡ አሉ። ይህስ፡ ኤልያስን፡ ይጸራል።
፵፰፤ አንድም፡ ከርሳቸው፡ የዚያን፡ ጊዜ፡ ፈጠነ፡
ስፍነግም፡ ወስዶ፡ መጻጻም፡ መላባት፡ *በዘንግ፡ ላይ
ም፡ አደረጋት፡ አጠጠውም። *ዮሐ፡ ፲፱፡ ፳፰፡፡
መዝ፡ ፷፱፡ ፳፪፡፡
፵፱፤ ሌሎች፡ ግን፡ አሉ። ተውት፡ እንደ፡ ኤልያስ፡
መጥቶ፡ ያድነው፡ እንደ፡ ሆነ።
፶፤ የሱስ፡ ግን፡ደግሞ፡በታላቅ፡ ቃል፡ጮኸ፡ ነፍሱን
ም፡ ሰጠ።
፶፩፤ እነሆም፡የቤተ፡ *መቅደስ፡መጋረጃ፡ለሁለት፡
ተቀደደ፡ ከላይ፡ እስከ፡ ታች። ምድርም፡ተናወጠች፡
ሕንጾችም፡ ተሰነጠቁ። *ዘፀአ፡ ፳፮፡ ፴፩፡፡
ዕብ፡ ፲፡ ፲፱፡ ፳፡፡
፶፪፤ መቃብሮችም፡ ተከፈቱ፡ የሚበዙም፡ ከቅዱ
ሳን፡ በድኖች፡ የተኙት፡ ተነሡ።
፶፫፤ ከትንሣኤውም፡ በኋላ፡ ከመቃብራቸው፡ ወ
ጡ፡ ወደ፡ ቅድስት፡ አገርም፡ ገቡ፡ ለብዞችም፡ ታዩ።
የሐዋ፡ ፳፫፡ ፳፮፡፡
፶፬፤ የመቶው፡ አለቃ፡ ግን፡ ከርሱ፡ ገራም፡ የነበሩ፡
የሱስም፡ሲጠብቁ።መናወጡን፡የሆነውንም፡ሁሉ፡
ባዩ፡ ጊዜ፡ እጅግ፡ ፈሩ፡ እንደ ህ፡ ሲሉ። በውነት፡ይህ፡
የእግዚአብሔር፡ ልጅ፡ ነበረ።
፶፭፤ ከዚያም፡ ነበሩ፡ ብዙ፡ ሴቶች፡ ከሩቅ፡ ያዩ።
እርሳቸውም፡ የሱስን፡ ከገሊላ፡ ይከተሉት፡ የነበሩ፡
የሚያገለግሉትም። ሉቃ፡ ፰፡ ፪፡ ፫፡፡

፶፮፤ ከርሳቸውም፡ ማርያም፡ መግደላዊት፡ ነበረች፡ ማርያምም፡ የያዕቆብና፡ የዮሴስ፡ እናት፡ የዘብደዊስም፡ የልጆቹ፡ እናት።

፶፯፤ *በመሸም፡ጊዜ፡ከአርማቴያ፡ ባለ፡ጸጋ፡ ሰው፡ መጣ፡ ስሙን፡ ዮሴፍ፡ የሚሉት። እርሱም፡ ደግሞ፡ ከየሱስ፡ ደቀ፡ መዛሙርት፡ ነበረ።

ዮሐ፡ ፲፱፡ ፴፰፡—፵፪፡፡ *ዘፀአ፡ ፴፱፡ ፳፩፡፡

፶፰፤ ይህ፡ ወደ፡ ጲላጦስ፡ ሔደ፡ የየሱስንም፡ሥጋ፡ ለመነው። የዚያን፡ ጊዜ፡ ጲላጦስ፡ አዘዘ፡ ሥጋውን፡ ይሰጡት፡ ዘንድ።

፶፱፤ ዮሴፍም፡ ሥጋውን፡ ወስዶ፡ በነጭ፡በፍታም፡ ከፈነው።

፷፤ ባዲስ፡መቃብርም፡ *አገባው፡ለርሱ፡በድንጊያ፡ በወቀረው፡ ታላቅ፡ ድንጊያም፡ በመቃብሩ፡ አፍ፡ገጠመና፡ ሔደ። *ኢሳ፡ ፶፫፡ ፱፡፡

፷፩፤ ከዚያም፡ ነበሩ፡ ማርያም፡መግደላዊት፡ሁለተኛይቱም፡ ማርያም፡ በመቃብሩ፡ ፊት፡ ተቀምጠው።

፷፪፤ በነገውም፡ ካርብ፡ በኋላ፡ በሚሆነው፡ የካህናት፡ አለቆች፡ፈሪሳውያንም፡ወደ፡ ጲላጦስ፡ ተሰበሰቡ፡ እንደህ፡ ሲሉ።

፷፫፤ ጌታ፡ ሆይ፡አስብነ፡፡ ያ፡ጥፉ፡ሕያው፡ ሳለ፡እንደ፡ተናገረ። *ከሶስት፡ቀን፡በኋላ፡እነሣለሁ። ቍ፡፵፡፡

፷፬፤ ስለዚህም፡ እዘዝ፡ መቃብሩ፡ እንዲጠበቅ፡ እስከ፡ ሶስት፡ ቀን፡ ድረስ። ደቀ፡መዛሙርቱ፡ በሌት፡ መጥተው፡ እንዳይሰርቁት፡ ለሕዝብም፡ ይላሉ፡ ከሙታን፡ እንደ፡ ተነሣ፡ የኋለኛዪቱም፡ ስሕተት፡ ከፊተኛዪቱ፡ ትከፋለች።

፷፭፤ ጲላጦስም፡ አላቸው፡ ጠባቆች፡ አልዋችሁ። ሒዱችሁ፡ መቃብሩን፡ አጽኑ፡ እንድታውቁ።

፷፮፤ እርሳቸውም፡ ሔደ፡መቃብሩንም፡ አጸኑ፡ ድንጊያውንም፡ *አተሙ፤ከጠባቆች፡ጋራ።

ዳን፡ ፮፡ ፲፯፡፡

ምዕራፍ፡ ፳፰፤

፩፤ ሰንበትም፡ካለፈ፡በኋላ፡በእሁድ፡ አጥቢያ፡ ማርያም፡ የመግደላዊቱ፡ ሁለተኛዪቱም፡ ማርያም፡ መቃብሩን፡ ሊያዩ፡ መጡ። ማር፡ ፲፮፡፡ ሉቃ፡ ፳፬፡፡

ዮሐ፡ ፳፡፡ ፩፤ ቆሮን፡ ፲፭፤ ፩፡—፯፡፡

፪፤ እነሆ፡ ታላቅ፡መናወጥም፡ሆነ። የእግዚአብሔር፡ መልክተኛ፡ ከሰማይ፡ ወርድዋልና። መጥቶም፡ ድንጊያውን፡ ከመቃብሩ፡ ደጃፍ፡ ፈነቀለው፡ በላዩም፡ ተቀመጠ።

፫፤ መልኩም፡ እንደ፡ መብረቅ፡ ነበረ። ልብሱም፡ ነጭ፡ እንደ፡ በረዶ። ም፡ ፲፯፤ ፪፡፡ የሐዋ፡ ፩፤ ፲፡፡

፬፤ ከግርማውም፡ የተነሣ፡ ጠባቆች፡ ደነገጡ፡ እንደ፡ ሞቱም፡ ሆኑ።

፭፤ መላኩ፡ ግን፡ መለሰ፡ ለሴቶቹም፡ አለ፡እላንተስ፡ አትፍሩ። የሱስን፡ የተሰቀለውን፡ እንድትሹ፡ አውቃለሁና።

፮፤ ከዚህ፡ የለም። ተነሥትዋልና፡ *እንደ፡ለ። ኑ፡ ስፍራውን፡ እዩ፡ †ጌታ፡ ተቀብሮበት፡ የነበረውን።

*ም፡ ፲፪፡ ፵፡፡ †የሐዋ፡ ፪፡ ፳፯፡፡

፯፤ ፈጥናችሁም፡ ሒዱ፡ ለደቀ፡ መዛሙርቱም፡ ንገርዋቸው፡ ከሙታን፡እንደ፡ ተነሣ። እነሆም፡ወደ፡ *ገሊላ፡ ይቀድማችኋል፡ከዚያ፡ ታዩታላችሁ። እነሆ፡ አልኋችሁ። ም፡ ፳፮፡ ፴፪፡፡

፰፤ ፈጥነውም፡ ከመቃብር፡ ወጡ፡ በፍርሃት፡ በደስታም፡ ሲቀዳደሙ፡ ለደቀ፡ መዛሙርቱ፡ሊነግሩ።

፱፤ በሔዱም፡ ጊዜ፡ ለደቀ፡ መዛሙርቱ፡ ሊነግሩ፡ እነሆ፡ የሱስ፡ ተገናኛቸው፡ እንደህ፡ ሲል። ደስ፡ ይበላችሁ። እርሳቸው፡ ግን፡ ቀረቡ፡ እግሩንም፡ ያዙና፡ ሰገዱለት።

፲፤ የዚያን፡ጊዜ፡የሱስ፡ አላቸው፡አትፍሩ። ሒዱ፡ *ለወንድሞቼ፡ ንገሩ፡ ወደ፡ ገሊላ፡ እንዲሔዱ። በዚያም፡ ያዩኛል። *ዕብ፡ ፪፡ ፲፩፡፡

፲፩፤ በሔዱም፡ ጊዜ፡ ከጠባቆች፡ ወገን፡ ሰዎች፡ ወደ፡ገር፡ መጡ፡ ለካህናት፡አለቆችም፡ የሆነውን፡ሁሉ፡ ነገሩ።

፲፪፤ እርሳቸውም፡ ከሽማግሎች፡ ጋራ፡ ተሰበሰቡ፡ ተማከሩም፡ለጭፍሮችም፡ ወርቅ፡ ሰጥዋቸው፡እሺ፡ ለማሰኘት፡ እንደህ፡ሲሉ።

፲፫፤ በሉ። ደቀ፡ መዛሙርቱ፡ በሌት፡ መጥተው፡ ሰረቁት፡ ተኝተን፡ ሳለነ። ም፡ ፳፯፡ ፷፬፡፡

፲፬፤ ይህም፡ ከሹሙ፡ዘንድ፡ቢሰማ፡እንዲያምን፡ እናደርገዋለን፡ እላንተም፡ ያላሳብ፡ እንድትሆኑ።

፲፭፤ እርሳቸውም፡ ወርቁን፡ ወስደ፡ እንደስተማርዋቸውም፡ አደረጉ። ይህም፡ ነገር፡ በአይሁድ፡ ዘንድ፡ ወጣ፡ እስከ፡ ዛሬ።

፲፮፤ አሥራ፡ አንዱ፡ ደቀ፡ መዛሙርት፡ ግን፡ ወደ፡ ገሊላ፡ ሔዱ፡ የሱስ፡ ወደዘዛቸው፡ ተራራ።

፲፯፤ ባዩትም፡ ጊዜ፡ ሰገዱለት። አኩሌቶች፡ ግን፡ ተጠራጠሩ።

፲፰፤ የሱስም፡መጣና፡ተናገራቸው፡እንደህ፡ሲል። ሥልጣን፡ ሁሉ፡ *ተሰጠኝ፡ በሰማይና፡ በምድር።

*ም፡ ፲፩፡ ፳፯፡፡ ኤፌ፡ ፩፡ ፳፡፡

፲፱፤ እንግዲህ፡ *ሒዱና፡ አሕዛብን፡ ሁሉ፡ አስተምሩ፡ አጥምቋቸውም፡ በአብና፡ በልጅ፡ በመንፈስ፡ ቅዱስም፡ ስም። *ማር፡ ፲፮፡ ፲፭፡ ፲፮፡፡

፳፤ በርሱም፡ ያዘዝኋችሁን፡ ሁሉ፡ መጠበቅ፡ አስተምርዋቸው። እኔም፡ እነሆ፡ *ከላንተ፡ ጋራ፡ ነኝ፡ በዘመኑ፡ ሁሉ፡ እስከ፡ ፍጻሜ፡ ዘመን። አሜን።

*ም፡ ፲፰፡ ፳፡፡ ዘሌዋ፡ ፲፡ ፲፩፡፡

ተፈጸመ ፡ የማቴዎስ ፡ ወንጌል።

# የማርቆስ ፡ ወንጌል ።

# የጌታችን ፡ የየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ቅዱስ ፡ ወንጌል ፡ እንደ ፡ ጻፈው፡ ቅዱስ ፡ ማርቆስ ፡፡

## ምዕራፍ፡ ፩፤

፩፤ የየሱስ፡ ክርስቶስ፡ የእግዚአብሔር፡ ልጅ፡ ወን
ጌል፡ መጀመርያ፡ ይህ፡ ነው። ማቴ፡ ፫። ሉቃ፡ ፫።
ዮሐ፡ ፩፤ ፲፱።
፪፤ በነቢያት፡ እንደ፡ ተጻፈ። *እነሆ፡ መልክተኛዬ
ን፡ እልካለሁ፡ ባንተ፡ ፊት፡ መንገድህንም፡ በፊትህ፡
ይጸርጋል። *መልክ፡ ፫፤ ፩—፬። ማቴ፡ ፲፩፤ ፲።
፫፤ ድምጽ፡ በምድረ፡ በደ፡ ይጮሃል። የእግዚአብ
ሔርን፡ መንገድ፡ ጽረጉ፡ ጎደናውንም፡ አስተካክሉ።
ኢሳ፡ ፵፤ ፫።
፬፤ ዮሐንስ፡ በምድረ፡ በደ፡ ያጠምቅ፡ ነበረ፡ የንስ
ሐ፡ ጥምቀትም፡ ያስተምር፡ ነበረ፡ ለኀጢአት፡ ማስ
ተስረያ።
፭፤ የይሁደም፡ አገር፡ ሁሉ፡ ወደርሱ፡ ይወጡ፡ ነበ
ሩ፡ የየሩሳሌምም፡ ሰዎች፡ ሁሉ። ከርሱም፡ በዮርደ
ኖስ፡ ወንዝ፡ ይጠመቁ፡ ነበሩ፡ በኀጢአታቸው፡ ኢየተ
ናዘዙ።
፮፤ የዮሐንስም፡ ልብስ፡ የግመል፡ ጸጕር፡ ነበረ። በ
ወገቡም፡ የቍርበት፡ መቀነት፡ ይታጠቅ፡ ነበረ። መብ
ሉም፡ አንበጣ፡ የምድረ፡ በደም፡ ማር።
፯፤ እንደህም፡ ሲል፡ ያስተምር፡ ነበረ። ከኔ፡ የሚ
በረታ፡ ከኔ፡ በኋላ፡ ይመጣል። እኔንም፡ አይገባኝም፡
ተጐንብሼ፡ የጫማውን፡ ጠፍር፡ እፈታ፡ ዘንድ።
፰፤ እኔ፡ በውኃ፡ አጠምቃችኋለሁ፡ እርሱ፡ ግን፡ በ
መንፈስ፡ ቅዱስ፡ ያጠምቃችኋል።
፱፤ ሆነም፡ በዚያ፡ ወራት፡ መጣ፡ የሱስ፡ *ከናዝሬ
ት፡ ከገሊላ፡ አገር፡ ከዮሐንስም፡ በዮርደኖስ፡ ተጠ
መቀ። ዮሐ፡ ፩፤ ፴፩—፴፬። *ሉቃ፡ ፪፤ ፶፩።
፲፤ በዚያን፡ ጊዜም፡ ከውኃ፡ ሲወጣ፡ ሰማዮች፡ ሲ
ቀደዱ፡ አየ፡ መንፈስ፡ ቅዱስም፡ እንደ፡ ርግብ፡ ሲወ
ርድበት።
፲፩፤ ድምጽም፡ ከሰማይ፡ መጣ፡ እንደህ፡ ሲል።
አንተ፡ ነህ፡ ልጄ፡ የምወድህ፡ ደስታዬንም፡ የማደ
ብህ። ም፡ ፱፤ ፯።
፲፪፤ በዚያን፡ ጊዜም፡ መንፈስ፡ ወደ፡ ምድረ፡ በደ፡
አወጣው። ሉቃ፡ ፬፤ ፩—፲፫።
፲፫፤ ከዚያም፡ በምድረ፡ በደ፡ አርባ፡ ቀን፡ ነበረ፡ ከ
ሰይጣን፡ ተፈትኖ። ከአራዊት፡ ጋራም፡ ነበረ፡ መላእ
ክትም፡ ያገለግሉት፡ ነበሩ።
፲፬፤ ዮሐንስም፡ ከታሠረ፡ በኋላ፡ የሱስ፡ ወደ፡ ገሊ
ላ፡ መጣ፡ የእግዚአብሔርን፡ መንግሥት፡ ወንጌል፡
ኢያስተማረ።
፲፭፤ እንደህም፡ሲል። *ዘመን፡ ተፈጸመ፡ የእግዚ
አብሔር፡ መንግሥትም፡ ቀረበች። ንስሐ፡ ግቡ፡ በወ
ንጌልም፤ እመኑ። *ገላት፡ ፬፤ ፬።
፲፮፤ በገሊላ፡ባሕርም፡አጠገብ፡ ሲሔድ፡ሲሞንን፡
አየ፡እንድርያስንም፡ ወንድሙን፡መርበብታቸውን፡
ወደ፡ ባሕር፡ ሲጥሉ። አጥማጆች፡ ነበሩና።
ማቴ፡ ፬፤ ፲፰፤ ፳፪። ሉቃ፡ ፭፤ ፩—፲፩።
፲፯፤ የሱስም፡ አላቸው። ኑ፡ በኋላዬ፡ ሰውም፡ እን
ድታጠምዱ፡ አደርጋችኋለሁ።
፲፰፤ የዚያን፡ ጊዜም፡ መርበብታቸውን፡ ትተው፡
ተከተሉት።
፲፱፤ ከዚያም፡ ጥቂት፡ ፈቀቅ፡ ብሎ፡ ያዕቆብን፡ አ
የ፡ የዘብደዎስን፡ልጅ፡ ዮሐንስም፡ወንድሙን። እር
ሳቸውም፡ በታንኳ፡ መርበብታቸውን፡ ሲያበጁ።
፳፤ የዚያን፡ ጊዜም፡ ጸራቸው። አባታቸውንም፡
ዘብደዎስን፡ በታንኳ፡ ላይ፡ ከሞያተኞች፡ ጋራ፡ ተው
ት፡ በኋላውም፡ ሔዱ።
፳፩፤ ወደ፡ ቅፍርናሆም፡ ገቡ። በዚያን፡ ጊዜም፡ ቅ
ደሚ፡ ቀን፡ ወደ፡ መስጊድ፡ ገባ፡ ያስተምርም፡ ነበር።
ሉቃ፡ ፬፤ ፴፩—፴፯።
፳፪፤ ከትምህርቱም፡ የተነሣ፡ *አደነቁ። ግዛት፡
እንደለው፡ ያስተምራቸው፡ ነበርና፡ እንደ፡ ጻፎችም፡
አይደለም። *ማቴ፡ ፯፤ ፳፰፤ ፳፱።
፳፫፤ በምስጊዳቸውም፡ ጋኔን፡ የነበረበት፡ ሰው፡
ነበረ፡ ጮኸም፡ እንደህ፡ ሲል።
፳፬፤ አየ፡ አንተ፡ንና፡ እኛን፡ምን፡ *አገኘተነ፡የሱስ፡
ሆይ፡ የናዝሬቱ። ልታጠፋን፡ መጣህን። ፈጽሚ፡ አ
ወቅሁ፡አንተ፡ማነህ፡የእግዚአብሔር፡ተቅዱስ፡ሆይ፡
*ም፡ ፭፤ ፯። ተመዝ፡ ፲፮፤ ፲። ዕ፯፤ ፲፮።
፳፭፤ የሱስም፡ ገሠጸው፡ እንደህ፡ ሲል። አፍህን፡
ዝጋና፡ ከርሱም፡ ውጣ።
፳፮፤ ርኩስ፡ መንፈስም፡ አንዘፈዘፈው፡ በታላቅ፡
ቃልም፡ ጮኸ፡ ከርሱም፡ ወጣ። ም፡ ፱፤ ፳፮።
፳፯፤ ሁላቸውም፡ አደነቁ፡ እርሱ፡ በርሳቸውም፡
ተጫወቱ፡እንደህ፡ ሲሉ። ምንድር፡ ነው፡ እንደህ፡ ያ
ለ፡ ነገር። ይህ፡ አዲስ፡ ትምህርትስ፡ ምንድር፡ ነው።
በትእዛዝ፡ ደግሞ፡ አጋንንት፡ ርኩሳን፡ያዛልና፡ ይታዘ
ዙትማል።
፳፰፤ የዚያን፡ ጊዜውም፡ ወሬው፡ በገሊላ፡ አጠገ
ብ፡ ባለው፡ አገር፡ ሁሉ፡ ወጣ።
፳፱፤ በዚያን፡ ጊዜም፡ ከመስጊድ፡ ወጡና፡ ወደ፡
ሲሞንና፡ ወደ፡ እንድርያስ፡ ቤት፡ መጡ፡ ከያዕቆብና፡
ከዮሐንስ፡ ጋራ። ማቴ፡ ፰፤ ፲፬—፲፮።
ሉቃ፡ ፬፤ ፴፰—፵፩።

፴፤ የሲሞንም፡የምሽቱ፡እናት፡በምንቸ፡ወድቃ፡ ነበረች። የዚያን፡ጊዜም፡ስለርሰዋ፡አሉት።

፴፩፤ እርሱም፡ ቀረበና፡ አስነሣት፡ እጅዋን፡ ይዞ። ደዌዋም፡ የዚያን፡ ጊዜውን፡ ተዋት፡ ታገለግላቸው ም፡ ነበረች።

፴፪፤ በመሸም፡ ጊዜ፡ ጸሐይ፡ ከገባች፡ ድውያንን፡ ሁሉ፡ አመጡለት፡ አብደችንም።

፴፫፤ አገሩም፡ ሁሉ፡ በደጁ፡ ተከማችቶ፡ ነበረ።

፴፬፤ እጅግም፡ ሰዎች፡ ፈወሰ፡ በሌላ፡በሌላ፡ደዌ፡ ከታመሙት፡ እጅግም፡ ሰይጣናት፡ አወጣ። *ሰይጣ ናትም፡ ይናገሩ፡ ዘንድ፡ አልተወም፡ እርሱን፡ ስለ፡ አ ወቁ። *ሉቃ፡ ፬፡ ፵፩፡፡ የሐዋ፡ ፲፮፡ ፲፯፡ ፲፰፡፡

፴፭፤ እጅግ፡ ማልደም፡ በሌት፡ ተነሣ፡ ወጣም፡ ወደ፡ ምድረ፡ በደም፡ ስፍራ፡ ሔደ፡ ከዚያም፡ ይጸል ይ፡ ነበር። ሉቃ፡ ፬፡ ፵፪፡—፵፬፡፡

፴፮፤ሲሞንም፡ተከተለው፡ከርሱም፡ጋራ፡የነበሩ።

፴፯፤ ባገኙትም፡ ጊዜ፡ አሉት፡ ሁሉ፡ ይሹሃል።

፴፰፤ እርሱም፡ አላቸው፡ወደ፡ ቀረበችው፡ መንደ ር፡ እንሒድ፡ ከዚያ፡ ደግሞ፡ አስተምር፡ ዘንድ። ስለ ዚህ፡ መጥቻለሁና። ዮሐ፡ ፲፰፡ ፴፯፡፡

፴፱፤ በየመስጊደቸውም፡ ያስተምር፡ ነበረ፡ በገሊ ላ፡ ሁሉ፡ ሰይጣናትንም፡ አወጣ።

፵፤ ለምጻምም፡ መጣበት፡ወደርሱ፡ ሲኽ። በጕል በቱም፡ ለርሱ፡ ወደቀ፡ እንዲህ፡ ሲለው። ብትፈቅድ ስ፡ ታነጻኝ፡ ዘንድ፡ ትችላለህ። ማቴ፡ ፰፡ ፪፡—፬፡፡ ሉቃ፡ ፭፡ ፲፪፡—፲፬፡፡

፵፩፤ የሱስም፡ ራራለት፡ እጁንም፡ ዘረጋና፡ ደሰሰ ው፡ እንዲህም፡ አለው። እፈቅዳለሁ፡ ንጻ።

፵፪፤በተናገረም፡ጊዜ፡ለምጹ፡ከርሱ፡ሔደ፡ነጻም።

፵፫፤ *ገሠጸውም፡ የዚያን፡ጊዜም፡ ሰደደው። *ም፡ ፫፡ ፲፪፡፡ ፯፡ ፴፮፡፡

፵፬፤ እንዲህም፡ አለው። ተጠንቀቅ፡ ለማንም፡ አንደች፡ አትናገር። ነገር፡ግን፡ሒድ፡ ራስህንም፡ ለካህ ን፡ አስፈትን። ስለ፡ነጻህም፡ *አቅርብ፡ ሙሴ፡ እንደ ዘዘ፡ ምስክር፡ ይሆንባቸው፡ ዘንድ። *ዘሌዋ፡ ፲፬፡፡

፵፭፤ እርሱ፡ ግን፡ በወጣ፡ጊዜ፡እጅግ፡ያወራ፡ያጨ ውትም፡ ጀመረ። የሱስ፡ ወደገር፡ ተገልጦ፡ መግባት፡ እስኪሳነው፡ ድረስ፡ ነገር፡ ግን፡ በሜዳ፡ በተፈታ፡ ስፍ ራ፡ ነበረ። ወደርሱም፡ ከቦታ፡ ሁሉ፡ ይመጡ፡ ነበሩ።

## ምዕራፍ፡ ፪፤

፩፤ ደግሞም፡ ከጥቂት፡ ቀን፡ በኋላ፡ ወደ፡ ቅፍርና ሆም፡ ገባ። በቤትም፡ እንደለ፡ ተሰማ። ማቴ፡ ፱፡ ፩፡—፲፰፡፡ ሉቃ፡ ፭፡ ፲፯፡—፳፮፡፡

፪፤ በዚያን፡ጊዜም፡ ብዙ፡ ሰዎች፡ ወደርሱ፡ ተሰበ ሰቡ። በደጁ፡ ፊት፡ የነበረው፡ ስፍራ፡ እስኪጨንቃቸ ው፡ ድረስ። ነገርም፡ ይነግራቸው፡ ነበረ።

፫፤ አራት፡ የተሸከሙትም፡ ድውይ፡አመጡለት።

፬፤ ከሕዝቡም፡ ብዛት፡ ወደርሱ፡ ለመቅረብ፡ ቢሳ ናቸው፡ የቤቱን፡ ማገር፡ ነድለው፡ ከፈቱ፡ ያለበቱን። በክፍቱም፡ድውዩ፡ተኝቶበት፡የነበረውን፡አልጋ፡ አወ ረዱት።

፭፤ የሱስም፡ ሃይማኖታቸውን፡ አይቶ፡ ድውዩን፡ አለው። ልጄ፡ ሆይ፡ ኃጢአትህ፡ ቀረልህ።

፮፤ ከዚያም፡ከጻፎች፡ ወገን፡ሰዎች፡ተቀምጠው፡ ነበሩ፡ በልባቸውም፡ አሰቡ።

፯፤ ለምን፡ ይህ፡ እንዲህ፡ ኢየተሳደበ፡ይናገራል። ማን፡ ይችላል፡ ኃጢአት፡ ማስተስረይ፡ ካንዱ፡ ከእግ ዚአብሔር፡ በቀር። ኢሳ፡ ፵፫፡ ፳፭፡፡ መዝ፡ ፻፴፡ ፬፡፡ ዘፀአ፡ ፴፬፡ ፯፡፡

፰፤ የዚያን፡ ጊዜም፡ የሱስ፡ በመንፈሱ፡ አወቀ፡ እ ንዲህ፡በልባቸው፡እንዲያስቡ፡ አላቸውም። ለምን፡ ይህነን፡በልባችሁ፡ታስባላችሁ። የሐዋ፡ ፪፡ ፳፬፡ ፳፭፡፡

፱፤ ማናቸው፡ ይበረታል፡ ለድውይ፡ ይገል፡ ዘንድ፡ ኃጢአትህ፡ተሰረየልህ። ወይስ፡ይገል፡ዘንድ። ተነሣ፡ አልጋህን፡ ተሸከምና፡ ሒድ።

፲፤ ነገር፡ ግን፡ ታውቁ፡ ዘንድ፡ ለሰው፡ ልጅ፡ ሥልጣ ን፡ እንደለው፡ኃጢአት፡ያስተሰርይ፡ዘንድ፡ በምድር፡ ላይ። ድውዩን፡ ይለዋል።

፲፩፤ አንተን፡ እልሃለሁ። ተነሣ፡ አልጋህንም፡ አን ሣ፡ ወደ፡ ቤትህም፡ ሒድ።

፲፪፤ የዚያን፡ ጊዜውም፡ ተነሣ፡ አልጋውንም፡ ተሸ ከመ፡ በሁሉም፡ ፊት፡ ወጣ። ሰው፡ ሁሉ፡ እስኪያደ ንቅ፡ ድረሰ። እግዚአብሔርንም፡ አመሰገኑ፡ እንዲህ፡ ኪሉ። እንዲህ፡ ያለ፡ ከቶ፡ አላየነም። ም፡ ፩፡ ፳፯፡፡

፲፫፤ ደግሞም፡ ወደ፡ ባሕር፡ ዳር፡ ወጣ። ሰውም፡ ሁሉ፡ ወደርሱ፡ ይመጣ፡ ነበር፡ ያስተምራቸውም፡ ነበረ።

፲፬፤ እርሱም፡ ሲያልፍ፡ሌዊን፡ አየ፡የእልፍዮስን፡ ልጅ፡ ተቀምጦ፡ ሲቀርጥ። አለውም፡ ተከተለኝ። እ ርሱም፡ ተነሥቶ፡ ተከተለው።

፲፭፤ በቤቱም፡ ለምሳ፡ ተቀምጦ፡ ሳለ፡ ብዙ፡ ቀራ ጮች፡ ኃጢአተኞችም፡ ተቀምጠው፡ ነበሩ፡ ከየሱስ፡ ጋራ፡ ከደቀ፡ መዛሙርቱም። እጅግ፡ ነበሩና፡ የተከተ ሉት። ሉቃ፡ ፯፡ ፲፯፡፡

፲፮፤ ጻፎችና፡ ፈሪሳውያንም፡ ባዩት፡ ጊዜ፡ ከቀራ ጮችና፡ ከኃጢአተኞች፡ ጋራ፡ ሲበላ። ለደቀ፡ መዛሙ ርቱ፡ አሉ። ምንሁንዋል፡ካጣርችና፡ከኃጢአተኞች፡ ጋራ፡ የሚበላ፡ የሚጠጣም።

፲፯፤ የሱስም፡ ሰማና፡ አላቸው። ጤና፡ ያላቸው፡ ባለ፡ መድኃኒትን፡ አይሹትም፡ የታመሙት፡ እንጂ። ጻድቃንን፡ ወደ፡ ንስሐ፡ልጸራ፡አልመጣሁም፡ ኃጢአ ተኞችን፡እንጂ። ም፡ ፩፡ ፲፭፡፡

፲፰፤ የዮሐንስም፡ ደቀ፡ መዛሙርት፡ የፈሪሳውያ ንም፡ ወገን፡ ይጾሙ፡ ነበሩ። መጡም፡ አሉትም። ለ ምን፡ የዮሐንስ፡ደቀ፡ መዛሙርት፡የፈሪሳውያንም፡ ይጾማሉ። ደቀ፡ መዛሙርትህ፡ ግን፡ አይጾሙም።

፲፱፡ የሱስም፡አላቸው። ሙሽራው፡ከርሳቸው፡ ጋ ራ፡ ሳለ፡ የሰርግ፡ ልጆች፡ ይጾሙ፡ ዘንድ፡ ይችላሉን። ሙሽራው፡ ከርሳቸው፡ ጋራ፡ ሳለ፡ ሊጾሙ፡ አይቻላቸ ውም።

፳፡ ነገር፡ ግን፡ ዘመን፡ ይመጣል፡ ሙሽራው፡ ከርሳ ቸው፡ በወጣ፡ ጊዜ፡ በዚያን፡ ጊዜ፡ ይጾማሉ።

፳፩፡ ማንም፡ አዲስ፡ ዉርቅ፡ አይጠቅምም፡ ባሮ ጌ፡ ልብስ፡ ላይ። ያለዚያ፡ ግን፡ አዲሱ፡ ቍራጭ፡ አሮ ጌውን፡ ይቀድዋል፡ መቀደዱም፡ ታላቅ፡ ይሆናል።

፳፪፡ አዲስ፡ጸጅም፡ባሮጌ፡ጋን፡የሚያኖር፡የለም። ያለዚያስ፡ አዲሱ፡ ፀጅ፡ አሮጌውን፡ ጋን፡ ይስነጥቀዋ ል፡ ፀጁም፡ ይፈሳል፡ ጋኑም፡ ይጠፋል። አዲሱ፡ ፀጅ፡ ባዲስ፡ ጋን፡ ይገለበጣል፡ እንጂ።

፳፫፡ ሆነም፡ በቅዳሚ፡ በርሻ፡ መካከል፡ ሲሔድ፡ ደቀ፡ መዛሙርቱ፡ በመንገድ፡ ሲያልፉ፡ እሸት፡ ይነቅ ሉ፡ ነበር። ሉቃ፡ ፮፡ ፩፡—፭፡፡ ማቴ፡ ፲፪፡ ፩፡—፰፡፡

፳፬፡ ፈሪሳውያንም፡ አሉት። የሚያደርጉትን፡ እ ይ፡ በቅዳሚ፡ የማይገባውን።

፳፭፡ እርሱም፡ አላቸው። ከቶ፡ አላነበባችሁምን፡ ዳዊት፡ ያደረገውን፡ በሻ፡ በተራበም፡ ጊዜ፡ እርሱ፡ ከ ርሱ፡ ጋራም፡ የነበሩት።

፳፮፡ እንዴት፡ ወደ፡ *እግዚአብሔር፡ቤት፡እንደገ ባ፡ አብያታር፡ የካህናት፡ አለቃ፡በነበረ፡ ወራት። የመ ሥዋዕትም፡ እንጀራ፡ እንደበላ። መብሉ፡ †የማይገ ባውን፡ ለካህናት፡ብቻ፡ እንጂ። ደግሞም፡ ከርሱ፡ጋ ራ፡ የነበሩት፡ እንደሰጠ። *፩፡ ሳሙኤ፡ ፳፩፡ ፮፡፡ ፳፪፡ ፰፡፡ †ዘሌዋ፡ ፳፬፡ ፱፡፡

፳፯፡ አላቸውም። ሰንበት፡ስለ፡ ሰው፡ ሆነ። ሰው፡ ስለ፡ሰንበት፡ አይደለም። ዘዳግ፡ ፭፡ ፲፬፡፡

፳፰፡ እንደሁም፡ የሰው፡ ልጅ፡ ደግሞ፡ የሰንበት፡ ጌታ፡ ነው።

ምዕራፍ፡ ፫፡

፩፡ ወደ፡ መሰጊድም፡ደግሞ፡ገባ። ከዚያም፡ሰው፡ ነበረ፡ እጁ፡ የሰለለ። ማቴ፡ ፲፪፡ ፱፡—፲፬፡፡ ሉቃ፡ ፮፡ ፮፡—፲፩፡፡

፪፡ ይጠብቁትም፡ ነበሩ፡ በሰንበት፡ያድነው፡ እንደ ሆን፡ ብለው፡ ሊያሳጡት።

፫፡ እጁ፡ የሰለለውንም፡ ሰው፡ አለው። ቁም፡ በ ማህል።

፬፡ አላቸውም። በሰንበት፡ መልካም፡ ማድረግ፡ ይገባልን፡ ወይስ፡ ክፉ፡ ነፍስ፡ ትድንን፡ ወይስ፡ ትሙ ት። እርሳቸው፡ ግን፡ ዝም፡ አሉ።

፭፡ ወደርሳቸውም፡ ዙሮ፡ አየ፡ *በቍጣ፡ ስለ፡ ልባ ቸው፡ ድንዛዜ፡ አዝኖ። ያነንም፡ሰው፡ አለው፡ እጅህ ን፡ ዘርጋ። ዘረጋትም፡ እጁም፡ ደኅና፡ ሁኖ፡ ቀረች፡ እን ደ፡ ሁለተኛዋ። *ዮሐ፡ ፲፩፡ ፶፫፡፡

፮፡ የዚያን፡ ጊዜም፡ ፈሪሳውያን፡ ወጡ፡ *ከሄሮድ ስ፡ ሰዎች፡ ጋራ፡ ተማከረውበት፡ ሊያጠፉት። *ማቴ፡ ፳፪፡ ፲፮፡፡

፯፡ የሱስ፡ ግን፡ ወደ፡ ባሕር፡ ሔደ፡ ከደቀ፡ መዛሙ ርቱ፡ ጋራ። እጅግም፡ ሰው፡ ተከተለው፡ ከገሊላ፡ ከይ ሁዳም።

፰፡ ከየሩሳሌም፡ ከኤዶምያስም፡ ከዮርዳኖስ፡ ማዶም፡ ከጢሮስና፡ ከሲዶናም፡ አጠገብ፡ እጅግ፡ ሰ ው፡ ያደረገውን፡ ሁሉ፡ በሰሙ፡ጊዜ፡ ወደርሱ፡መጡ።

፱፡ ደቀ፡መዛሙርቱንም፡አላቸው። ታናሽ፡ታንኳ፡ ያዘጋጁለት፡ ዘንድ፡ ስለ፡ ሰው፡ ብዛት፡ እንዳያጫን ቁት።

፲፡ ብዙ፡ ሰዎች፡ አድኖ፡ ነበርና። ደዌ፡ ያለበት፡ ሁ ሉ፡ እስኪወድቅበት፡ ሊደሰው።

፲፩፡ ርኩሳን፡ መናፍስትም፡ ባዩት፡ ጊዜ፡ በፊቱ፡ ወ ድቀው፡ ይጮሁ፡ ነበሩ፡ እንዲህ፡ ሲሉ። አንተ፡ *የእግ ዚአብሔር፡ ልጅ፡ ነህ። *ሉቃ፡ ፬፡ ፵፩፡

፲፪፡ እጅግም፡ ተቈጣቸው፡ እንዳይገልጡት። ምዕ፡ ፩፡ ፴፬፡፡

፲፫፡ ወደ፡ ተራራም፡ ወጣ፡ የወደዳቸውንም፡ ጸራ። ወደርሱም፡ መጡ። ማቴ፡ ፲፡ ፪፡—፬፡፡ ሉቃ፡ ፲፪፡ ፲፯፡፡

፲፬፡ አሥራ፡ ሁለትም፡ አደርጋቸው፡ ከርሱ፡ ጋራ፡ ይኖሩ፡ ዘንድ። ሊያስተምሩም፡ ይልካቸው፡ ዘንድ።

፲፭፡ ሥልጣንም፡ ይሆንላቸው፡ ዘንድ፡ ድውያንን፡ ለመፈወስ፡ ሰይጣናትም፡ ለማውጣት።

፲፮፡ ሲሞንንም፡ ስሙን፡ ጴጥሮስ፡ አለው።

፲፯፡ ያዕቆብንም፡ የዘብዴዎስን፡ ልጅ፡ ዮሐንስን ም፡ የያዕቆብን፡ ወንድም፡ ስማቸውን፡ ቦአኔርጌስ፡ አለ። ትርጓሚውም፡ የነጐድጓድ፡ ልጆች፡ነው። ሉቃ፡ ፱፡ ፶፬፡፡

፲፰፡ እንድርያስንም። ፊልጶስንም። ተማስንም። ያዕቆብንም፡ የእልፍዮስን፡ ልጅ። ታዴዎስንም። ሲ ሞንንም፡ የቀነናዊን።

፲፱፡ ይሁዳንም፡ ያስቀሮቱን። እርሱም፡ ደግሞ፡ አሳልፎ፡ የሰጠው።

፳፡ ወደ፡ ቤትም፡ መጡ። ደግሞም፡ ሰው፡ ተሰበ ሰበ፡ እንጀራ፡ ስንኳ፡ ለመብላት፡ እስኪሳናቸው፡ ድ ረስ።

፳፩፡ ወገኖቹም፡ ሰምተው፡ ሊይዙት፡ ወጡ፡ ምና ልባት፡ ልቡ፡ ዘነጋ፡ ብለው፡ ነበሩና።

፳፪፡ ጸፎችም፡ ከየሩሳሌም፡ የወረዱ፡ ብዔል፡ ዜ ቡል፡ አለበት፡ በሰይጣናትም፡ አለቃ፡ ሰይጣናትን፡ ያወጣል፡ አሉ። ማቴ፡ ፲፪፡ ፳፬፡—፴፪፡፡ ሉቃ፡ ፲፩፡ ፲፭፡—፳፪፡፡

፳፫፡ ጸራቸውም፡ በምሳሌም፡ አላቸው። እንዴ ት፡ ይችላል፡ ሰይጣን፡ ሰይጣንን፡ ያወጣው፡ ዘንድ።

፳፬፡ መንግሥትም፡ እርሱ፡ በርሱ፡ቢከፋፈል። ያ፡ መንግሥት፡ ይጸና፡ ዘንድ፡ አይቻለውም።

፳፭፡ ቤትም፡ እርሱ፡ በርሱ፡ ቢከፋፈል። ያቤት፡ ይጸና፡ ዘንድ፡ አይችልም።

፳፮፤ ሰይጣንም፡ ራሱን፡ ቢጻላ፡ ቢለይም፡ ሊጸና፡ አይችልም፡ ነገር፡ ግን፡ ፍጻሜ፡ አለበት።

፳፯፤ ማንም፡ ወደ፡ ብርቱ፡ ቤት፡ ይገባ፡ ዘንድ፡ አይችልም፡ ከብቱንም፡ ይበዘብዝ፡ ዘንድ፡ ብርቱውን፡ አስቀድሞ፡ ካላሠረ። ከዚያ፡ ወዲያም፡ ቤቱን፡ ይበዘብዛል።

፳፰፤ እውነት፡ እላችኋለሁ። ኃጢአት፡ ሁሉ፡ ለሰው፡ ልጆች፡ እንዲሰረይ፡ ስድብም፡ የሚሳደቡበት።

፳፱፤ በቅዱስ፡ መንፈስ፡ ግን፡ የሚሳደብ፡ ለዘላለም፡ ስርየት፡ የለውም፡ የወትር፡ ፍርድ፡ ይፈረድበታል፡ እንጂ።

፴፤ ርኩስ፡መንፈስ፡አለበት፡ይሉ፡ነበረና። ቍ፡ ፳፪።

፴፩፤ ወንድሞቹም፡ እናቱም፡ መጡ፡ በሜዳም፡ ቆመው፡ ላኩበትም፡ ሊጠሩት ማቴ፡ ፲፪፤ ፵፮፤—፶።
ሉቃ፡ ፰፤ ፲፱፤—፳፩።

፴፪፤ ሰዎችም፡ በዙርያው፡ ተቀምጠው፡ ነበሩ፡ አሉትም። እነሆ፡ እናትህ፡ ወንድሞችህም፡ በሜዳ፡ ይሹሃል።

፴፫፤ እርሱም፡ መለሰላቸው፡እንዲህ፡ ሲል። ማናት፡ እናቴ፡ ወንድሞቼስ።

፴፬፤ በዙርያውም፡ተቀምጠው፡ ወደ፡ ነበሩት፡ አይቶ፡ አለ። እነሆ፡ እናቴ፡ ወንድሞቼም።

፴፭፤ የእግዚአብሔርን፡ ፈቃድ፡ የሚያደርግ፡ እርሱ፡ ወንድሜ፡ ነውና፡ እናቴም።

## ምዕራፍ፡ ፬፤

፩፤ ደግሞም፡ በባሕር፡ ዳር፡ ያስተምር፡ ጀመረ፡ እጅግ፡ ሰውም፡ ወደርሱ፡ ተሰበሰበ። ወደ፡ መርከብ፡ ወጥቶ፡ በባሕር፡ እስኪቀመጥ፡ድረስ፡ ሰውም፡ ሁሉ፡ በባሕር፡ አጠገብ፡ በምድር፡ ላይ፡ ነበረ።
ማቴ፡ ፲፫፤ ፩፤—፳፫። ሉቃ፡ ፰፤ ፬፤—፲፭።

፪፤ እጅግም፡ ያስተምራቸው፡ ነበረ፡ በምሳሌ። በትምህርቱም፡ አላቸው።

፫፤ ስሙ፡ እነሆ፡ ወጣ፡ ዘሪ፡ ይዘራ፡ ዘንድ።

፬፤ እርሱም፡ ሲዘራ፡ ከዘሩ፡ አንዳንድ፡በመንገድ፡ ወደቀ፡ የሰማይም፡ ወፎች፡ መጡና፡ በሉት።

፭፤ አንዳንድም፡ በደንጊያ፡ ላይ፡ ወደቀ፡ እጅግ፡ ምድር፡ ባልነበረበት። የዚያን፡ጊዜውም፡ በቀለ፡የጠለቀ፡ ምድር፡ ባይኖርበት።

፮፤ ጸሐይም፡በወጣች፡ ጊዜ፡ ተቃጠለ፡ስርም፡ ባይኖረው፡ ደረቀ።

፯፤ ሌላም፡ በሾህ፡ ላይ፡ ወደቀ። እሾህም፡ ወጣና፡ አነቀው፡ አላፈራምም።

፰፤ ሌላም፡ በመልካም፡ምድር፡ ወደቀ፡ ያደገ፡የለማም፡ ፍሬም፡ የሰጠ። አንዱም፡ ሠላሳ፡ አመጣ፡ ሁለተኛውም፡ ስድሳ፡ ሦስተኛውም፡ መቶ።

፱፤ አላቸውም፡ የሚሰማ፡ ጆሮ፡ ያለው፡ ይስማ።

፲፤ ብቻውንም፡ በሆነ፡ ጊዜ፡ በዙርያው፡ የነበሩ፡ ካሥራ፡ ሁለቱ፡ ጋራ፡ ስለ፡ ምሳሌው፡ ጠየቁት።

፲፩፤ አላቸውም። እላንተ፡ ተሰጥቶዋችኋል፡የእግዚአብሔር፡ መንግሥቱን፡ ምስጢር፡እንድታውቁት፡ እለዚያ፡ ግን፡ *በሜዳ፡ ያሉ፡ በምሳሌ፡ነገር፡ ሁሉ፡ ይሆንላቸዋል። *፩፤ ቆሮ፡ ፭፤ ፲፪።

፲፪፤ ማየትንም፡እያዩ፡እንዳይመለከቱ፡ መስማትንም፡እየሰሙ፡ እንዳያስተውሉም፡ እንዳይመለሱ፡ ኃጢአታቸውም፡እንዳይሰረይላቸው።
ኢሳ፡ ፮፤ ፱፤ ፲።

፲፫፤ አላቸውም። ይህነን፡ ምሳሌ፡አላስተዋላችሁም፡እንዴትስ፡ምሳሌውን፡ሁሉ፡ታስተውላላችሁ።

፲፬፤ ዘሪው፡ ቃልን፡ የሚዘራው፡ ነው።

፲፭፤ በመንገድም፡ ያሉ፡ እርሳቸው፡ ናቸው፡ ቃል፡ ወደሚስራበት። በሰሙበት፡ ጊዜም፡ ሰይጣን፡ ይመጣል፡ በልባቸውም፡ የተዘራውን፡ቃል፡ ይወስዳል።

፲፮፤ እንዲሁም፡በደንጊያ፡ላይ፡የተዘሩት፡ እሌህ፡ ናቸው፡ ነገር፡ በሰሙ፡ ጊዜ፡ በዚያን፡ ጊዜ፡ በደስታ፡ የሚቀበልዋት።

፲፯፤ በውሥጣቸውም፡ ሥር፡ የላቸውም። እርሳቸው፡ የጊዜው፡ ናቸው፡ እንጂ። መከራም፡ በሆነ፡ ጊዜ፡ ወይም፡ ስደት፡ ስለ፡ ነገር፡ የዚያን፡ ጊዜውን፡ ያነቅፋሉ።

፲፰፤ በሾህም፡ የተዘሩ፡ እሌህ፡ ናቸው። ነገር፡ የሚሰሙ።

፲፱፤ የዚህ፡ ዓለም፡አሳብና፡ የባለጠግነትም፡ ማታለል፡ ሌላም፡ ሥጋዊ፡ ፈቃድ፡ ገብቶ፡ ነገርን፡ ያንቃል፡ ያለ፡ ፍሬም፡ ይሆናል። ም፡ ፲፤ ፳፫።

፳፤ በመልካም፡ ምድር፡ የተዘሩም፡ እሌህ፡ ናቸው። ነገር፡ የሚሰሙ፡የሚቀበሉትም፡ ፍሬም፡ ያደርጋሉ። አንዱ፡ ሠላሳ፡ሁለተኛውም፡ስድሳ፡ሦስተኛውም፡ መቶ።

፳፩፤ ይላቸውም፡ነበረ። በውኑ፡መብራት፡ያመጣሉን፡ ከንቅብ፡ በታች፡ ያኖሩት፡ ዘንድ፡ ወይስ፡ ካልጋ፡ በታች። በመቅረዙ፡ ላይ፡ ሊኖር፡ አይደለምን።
ማቴ፡ ፭፤ ፲፭። ሉቃ፡ ፰፤ ፲፮፤—፲፰።

፳፪፤ የተሠወረ፡የለምና፡የማይገለጥ። በሽሽግም፡ የሚደረግ፡ የለምና፡ ግን፡ ወደ፡ መብራት፡ እንዲመጣ፡ እንጂ። ማቴ፡ ፲፤ ፳፮። ሉቃ፡ ፲፪፤ ፪።

፳፫፤ የሚሰማ፡ ጆሮ፡ ያለው፡ ይስማ።

፳፬፤ አላቸውም። እዩ፡ ምን፡ ትሰማላችሁ። በምትሰፍሩት፡መስፈርያ፡ ይሰፈረላችኋል፡ ይጨመርላችኋልም፡ ለላንት፡ ለምትሰሙ። ማቴ፡ ፯፤ ፪።

፳፭፤ ያለው፡ይጨመርለታልና። የሌለው፡ያለው፡ ቅሉ፡ ይሔድበታል። ማቴ፡ ፲፫፤ ፲፪።

፳፮፤ እርሱም፡ አለ። እንዲህ፡ናት፡የእግዚአብሔር፡ መንግሥት፡ እንደ፡ ሰው፡ዘርን፡ በምድር፡ ላይ፡ በጣለ፡ ጊዜ።

፳፯፤ ይተኛልም፡ ይነሣልም፡ ሌትና፡ ቀን። ዘሩም፡ ይበቅላል፡ ያድጋልም፡ እርሱ፡ ሳያውቀው።
ያዕ፡ ፭፤ ፯።

፳፰፡ ምድሪቱ፡ ከርሷዋ፡ ፍሬ፡ታመጣለችና። በመጀመርያ፡ ሣር። ኋላም፡ ዛላ፡ ኋላም፡ በዛላው፡ ስንደ፡ ትመላለች።

፳፱፡ ፍሬ፡ ግን፡ በበሰለች፡ ጊዜ፡ ማጭድ፡ ይሰደል፡ መከር፡ ደርሶዋልና።

፴፡ አለም።እግዚአብሔር፡መንግሥት፡ ማንን፡ ትመስላለች። ወይስ፡ በምን፡ምሳሌ፡እንመስላታለን።

ማቴ፡ ፲፫፡ ፴፩፡—፴፪። ሉቃ፡ ፲፫፡ ፲፰፡ ፲፱።

፴፩፡ እንደ፡ ሰናፍጭ፡ ቅንጣት፡ ናት። እርስዋም፡ በምድር፡ ላይ፡ በተዘራች፡ ጊዜ፡በምድር፡ ካለ፡ ከዘር፡ ሁሉ፡ ታንሳለች።

፴፪፡ በተዘራችም፡ ጊዜ፡ ትወጣለች፡ ከለምለምም፡ ሁሉ፡ የምትበልጥ፡ ትሆናለች፡ ታላላቅ፡ጫፎም፡ ታደርጋለች፡የሰማይ፡ ወፎች፡ በጽላዋ፡ ታች፡ ይሰፍሩ፡ ዘንድ፡ እስኪሆን፡ ድረስ።

፴፫፡ እንደዚህም፡ባለ፡ብዙ፡ምሳሌ፡በነገር፡ይነግራቸው፡ነበረ፡ መስማቱን፡ በሚችሉበት፡ መጠን።

፴፬፡ ያለ፡ ምሳሌ፡ ግን፡ አልነገራቸውም። ለብቻውም፡ ሳለ፡ ነገሩን፡ ሁሉ፡ ለደቀ፡ መዛሙርቱ፡ ይፈታላቸው፡ ነበር።

፴፭፡ በዚያም፡ ቀን፡ በመሸ፡ ጊዜ፡ አላቸው። እንሒድ፡ ወደ፡ ማዶ። ማቴ፡ ፰፡ ፲፰፡ ፳፫፡—፳፯። ሉቃ፡ ፰፡ ፳፪፡—፳፭።

፴፮፡ ሰውንም፡ አሰናብተው፡ ከዚያው፡ በመርከብ፡ እንደ፡ ነበረ፡ ወሰዱት። ሌሎች፡ታናናሽም፡መርከቦች፡ ደግሞ፡ ከርሱ፡ ጋራ፡ ነበሩ።

፴፯፡ ዓውሎ፡ ነፋስም፡ ታላቅ፡ ነበረች። መውጁንም፡ ትገለብጥ፡ ነበረች፡ በመርከብ፡ እስክትመላ፡ ድረስ።

፴፰፡ እርሱም፡ ተኝቶ፡ ነበር፡ በኋላዋ፡ ክንዱን፡ ተንተርሶ። አነቁትም፡ እንደዚህም፡ አሉት። መምህር፡ ሆይ፡ አያገድህምን፡ ስናልቅ።

፴፱፡ ተነሣም፡ነፋሱንም፡ገሠጸ፡ ባሕሩንም፡አለ። ዝም፡ በል። ጸጥ፡ በል። ነፋሱም፡ ዝም፡ አለ፡ ታላቅ፡ ጸጥታም፡ ሆነ።

፵፡ አላቸውም። ለምን፡እላንተ፡ እንደዚህ፡ ትፈራላችሁ። እንዴት፡ ሃይማኖት፡ የላችሁም።

፵፩፡ ታላቅ፡ ፍርሃትም፡ ፈሩ፡ እርሱ፡ በርሳቸውም፡ አሉ፡ እንጃ፡ ይህ፡ ማነው። ባሕርም፡ ነፋስም፡ ይታዘዙታልና።

## ምዕራፍ፡ ፭፡

፩፡ ወደ፡ ባሕር፡ ማዶም፡ መጡ፡ ወደ፡ ገደሬኖች፡ አገር። ማቴ፡ ፰፡ ፳፰፡—፴፬። ሉቃ፡ ፰፡ ፳፮፡—፴፱።

፪፡ ከመርከብም፡ በወጣ፡ ጊዜ፡ አንድ፡ ሰው፡ ከመቃብር፡ አገኘው፡ ርኩስ፡መንፈስ፡የነበረበት።

፫፡ መኖርያውም፡ በመቃብር፡ነበረ። ማንም፡ በሰንሰለት፡ ስንኳ፡ ያጸናው፡ ዘንድ፡ አልቻለም።

፬፡ ብዙ፡ ጊዜ፡ በግር፡ ብረት፡ በሰንሰለትም፡ ይታሠር፡ ነበርና። ሰንሰለቱንም፡ ይቈርጥ፡ ነበር፡ እግር፡ በረቱንም፡ ይሰብር፡ ነበር። ማንም፡ ሊይዘው፡ አይችልም፡ ነበር።

፭፡ ሁልጊዜም፡ በሌት፡ በቀንም፡ በመቃብርና፡ በተራራ፡ ይጮኽ፡ነበር፡ ሰውነቱንም፡በበልጭት፡ ይቈርጥ፡ ነበረ።

፮፡ የሱስንም፡ ከሩቅ፡ ባየ፡ ጊዜ፡ ሮጦ፡ ሰገደለት።

፯፡ በታላቅ፡ ድምጽም፡ ጮኾ፡ አለም። ባንተና፡ በኔ፡ መካከል፡ምን፡ አለ፡ የሱስ፡ ሆይ፡ የልዑል፡የእግዚአብሔር፡ ልጅ። በእግዚአብሔር፡ አምልሃለሁ። እንዳትሣቅየኝ። ማቴ፡ ፰፡ ፳፱።

፰፡ አንተ፡ ርኩስ፡ መንፈስ፡ ከዚህ፡ ሰው፡ ውጣ፡ ይለው፡ ነበርና።

፱፡ ማነው፡ስምህ፡ብሎም፡ ጠየቀው። መለሰም፡ እንደዚህ፡ ሲል። ስሜ፡ ሌጌዎን፡ ነው። እጅግ፡ ነንና።

፲፡ እጅግም፡ ለመነው፡ ካገር፡ ወደ፡ ሜዳ፡ እንዳያሰደቸው።

፲፩፡ ከዚያም፡ በተራራ፡ አጠገብ፡ታላቅ፡የርያ፡ መንጋ፡ ይሰማራ፡ ነበር።

፲፪፡ ሰይጣናትም፡ለመኑት፡እንደዚህ፡ሲሉ።ተወን፡ ወደ፡ እርያች፡ እንገባባቸው፡ ዘንድ።

፲፫፡ የዚያን፡ ጊዜም፡ ፈቀደላቸው፡ የሱስ። ርኩሶች፡ መናፍስትም፡ ወጡና፡ ወደ፡ እርያው፡ ገቡ። መንጋውም፡ ሮጠ፡ ከገደል፡አፋፍም፡ወደ፡ባሕር፡ ወደቀ። ሁለት፡ ሺህም፡ ያህሉ፡ ነበር፡ በባሕርም፡ ሠጠሙ።

፲፬፡ እርያ፡ ጠባቆች፡ ግን፡ሸሹ፡ ባገርም፡ በሜዳም፡ አወሩ። የሆነውንም፡ ለማየት፡ወጡ።

፲፭፡ ወደ፡ የሱስም፡ ቀረቡ፡ እብዱንም፡ አዩ፡ተቀምጦ፡ ለብሶም፡ ጤምቶም፡ ሌጌዎን፡ የነበረበቱን። ፈሩም።

፲፮፡ ያዩትም፡ ነገሩዋቸው፡ የብዱ፡ ስራ፡ የርያውስ፡ እንዴት፡ ነበረ።

፲፯፡ ይለምኑትም፡ ጀመሩ፡ ካገራቸው፡ ይሔድ፡ ዘንድ።

፲፰፡ ወደ፡ መርከብም፡በወጣ፡ ጊዜ፡ እብድ፡ የነበረው፡ ከርሱ፡ ጋራ፡ ይሆን፡ ዘንድ፡ ለመነው።

፲፱፡ የሱስ፡ግን፡ አልተወውም፡ ነገር፡ ግን፡ አለው። ወደ፡ ቤትህ፡ ሒድ፡ ከሰዎችህ፡ ዘንድ፡ ንገራቸውም፡ እግዚአብሔር፡ በስራልህ፡ ሁሉ፡ አንተንም፡ በመማሩ።

፳፡ ሒደም፡ *ባሥሩ፡ አገርም፡ያስተምር፡ ጀመረ፡ የሱስ፡ ባደረገለት፡ ሁሉ። ሁሉም፡ ተደነቁ።

*ም፡ ፯፡ ፴፩።

፳፩፡ የሱስም፡ ደግሞ፡በመርከብ፡ወደ፡ ማዶ፡ ባለፈ፡ ጊዜ፡ እጅግ፡ ሰዎች፡ ወደርሱ፡ተሰበሰቡ፡ በባሕር፡ አጠገብም፡ ነበረ።

፳፪፡ እነሆ፡ ከመስጊድም፡ አለቆች፡ አንድ፡መጣ፡ ስሙን፡ ያይሮስ፡ የሚሉት። ባየውም፡ ጊዜ፡ በግሩ፡ ወደቀ። ማቴ፡ ፱፡ ፲፰፡—፳፮። ሉቃ፡ ፰፡ ፵፩፡—፶፮።

፳፫፡ እጅግም፡ ይለምነው፡ ነበር፡ እንደህ፡ ሲል። ታናሺቱ፡ ልጄ፡ ለሞት፡ቀርባለች፡ነገር፡ግን፡ና፡ *እጅህንም፡ ጫንባት፡ እንድትፈወስና፡ እንድትድን።
*ም፡ ፯፡ ፴፪፡

፳፬፡ ከርሱ፡ጋራም፡ ሔደ፡ እጅግ፡ ሰውም፡ ተከተለው። ያጫንቁትም፡ ነበሩ።

፳፭፡ ቤትም፡ ደም፡ የሚፈሳት፡ ካሥራ፡ ሁለት፡ አመት፡ጀምሮ።

፳፮፡ ከብዙም፡ ጠቢባን፡እጅግ፡ ደከመች፡ ከብትዋንም፡ሁሉ፡በተነች፡አንዳችም፡አልተጠቀመችም። ከፋባት፡(ባሰባት፡)እንጂ።

፳፯፡ የየሱስን፡ ነገር፡ በሰማች፡ ጊዜ፡ በሰዎች፡ መካከል፡ በኋላው፡ መጣች፡ ልብሱንም፡ ደሰሰች።

፳፰፡ ብላለችና። ልብሱን፡የደሰስሁ፡እንደሆን፡ ደንሁ።

፳፱፡ የዚያን፡ጊዜውም፡የደምዋ፡ምንጭ፡ደረቀ። በሰውነትዋም፡አወቀች፡ ከደዌዋ፡ እንደ፡ ደነች።
ዘሌዋ፡ ፳፡ ፲፰።

፴፡ የዚያን፡ጊዜም፡የሱስ፡ በራሱ፡ አውቆ፡ ከርሱ፡ ኃይል፡ እንደወጣ፡ ወደ፡ ሰዎች፡ ተመለሰ፡ አለም። ማን፡ ልብሴን፡ደሰሰ።
ሉቃ፡ ፮፡ ፲፱።

፴፩፡ ደቀ፡ መዛሙርቱም፡ አሉት። ታያለህ፡ሰው፡ ያጫንቅሃል፡ ማን፡ደሰሰኝም፡ ትላለህን።

፴፪፡ በዙርያውም፡ ያየ፡ ነበረ፡ደህችን፡ ያደረገችውን፡ ሊያይ።

፴፫፡ ሴቲቱ፡ግን፡ ፈራች፡ተንቀጠቀጠችም፡ የተደረገባትን፡ ስላወቀች። መጥታም፡ በገደችለት፡ እውነትንም፡ ሁሉ፡ ነገረችው።

፴፬፡ እርሱም፡ አላት። አንቺ፡ ልጄ፡ ሃይማኖትሽ፡ አደነሽ። በደህና፡ ሒጂ፡ ከደዌሽም፡ ተፈወሺ።

፴፭፡ እርሱም፡ሲናገር፡ሰዎች፡ ካለቃው፡ ቤት፡ መጡ፡ እንደህ፡ ሲሉ። ልጅህ፡ሞተች። ለምን፡እስካሁን፡ መምህርን፡ ታደክመዋለህ።

፴፮፡ የሱስ፡ ግን፡ የዚያን፡ ጊዜ፡ የተባለውን፡ ነገር፡ በሰማ፡ጊዜ፡ የመስጊዱን፡ አለቃ፡ አለው። አትፍራ። እመን፡ ብቻ።

፴፯፡ ማንም፡ ከርሱ፡ ጋራ፡ አላስከተለውም፡ ከጴጥሮስና፡ ከያዕቆብ፡ ከዮሐንስም፡ ከያዕቆብ፡ ወንድም፡ በቀር።

፴፰፡ ወደ፡ምስጊዱ፡አለቃ፡ ቤትም፡ መጣ፡ሁከትም፡ አየ፡ ሰዎችም፡ ሲያለቅሱ፡ ዋይም፡ ሲሉ።

፴፱፡ ገባም፡አላቸውም። ለምን፡ ትፈጀላችሁ፡ ታለቅሱማላችሁ። *ብላቴናይቱ፡ አልሞተችም፡ እርስዋ፡ ተኝታለች፡ እንጂ።
*ዮሐ፡ ፲፩፡ ፲፩።

፵፡ ከነገሩም፡ ሳቁ። እርሱ፡ ግን፡ ሁሉን፡ አወጣ፡ ከርሱ፡ ጋራም፡ የብላቴናይቱን፡ አባት፡ ወሰደ፡ እናትዋንም፡ ከርሱ፡ ጋራም፡የነበሩትን፡ብላቴናይቱ፡ ወደለችበትም፡ ስፍራ፡ ገባ።

፵፩፡ የብላቴናይቱንም፡ እጅ፡ ያዘ፡ አላትም። ጣሊታ፡ ቁሚ። ትርጓሜውም፡ አንቺ፡ብላቴና፡ እልሻለሁ፡ *ተነሺ።
*ሉቃ፡ ፯፡ ፲፬።

፵፪፡ በዚያን፡ ጊዜም፡ ብላቴናይቱ፡ ተነሣች፡ ሔደችም። ያሥራ፡ ሁለት፡ አመት፡ልጅ፡ ነበረችና። አደነቁም፡ እጅግ፡ ማድነቅ።

፵፫፡ እጅግም፡ አዘዛቸው፡ ደህነን፡ ለማንም፡ እንደያስታውቁ። አላቸውም፡ ስጥዋት፡ ትብላ።

## ምዕራፍ፡ ፮፡

፩፡ከዚያም፡ወጣ፡ወደገሩም፡መጣ።ደቀ፡መዛሙርቱም፡ ተከተሉት።
ማቴ፡ ፲፫፡ ፶፫—፶፰።
ሉቃ፡ ፬፡ ፲፮—፴።

፪፡ ቅደሚም፡ በሆነ፡ በመስጊድ፡ ያስተምር፡ ጀመረ። ብዙ፡ ሰዎችም፡ በሰሙ፡ ጊዜ፡ ያደንቁ፡ ነበሩ፡ እንደህ፡ ሲሉ። ደህች፡ *ከወደት፡ መጣችለት። ምንስ፡ ጥበብ፡ ደህች፡ናት፡ የተሰጠችው፡ ደህነን፡ ያህል፡ ኃይል፡ በጁ፡ እንዲደረግ።
*ዮሐ፡ ፯፡ ፲፭።

፫፡ ደህ፡ጸራቢው፡ አደደለምን፡የማርያም፡ ልጅ። የያዕቆብም፡ወንድም፡ የዮሳም፡የደሁደም፡ የሲሞንም። እኅቶቹስ፡ ከዚህ፡ ከኛ፡ ዘንድ፡አደደሉምን። ያነቅፈበትም፡ ነበሩ።

፬፡ የሱስም፡ አላቸው። ነቢይ፡ አደናቅም፡ ባገሩ፡ በወገኑም፡በቤቱም፡ በቀር።

፭፡ ከዚያም፡ አንድ፡ ኃይል፡ ማድረግ፡ አልቻለም፡ ከጥቂት፡ ድውያን፡ በቀር፡ እጁን፡ እናረገባቸው፡ ፈወሳቸውም።

፮፡ ሃይማኖት፡ ስለ፡ ጠፋባቸው፡ አደነቀ። መንደሩንም፡ ሁሉ፡ ኢየዞረ፡ ያስተምር፡ ነበር።

፯፡ አሥራ፡ሁለቱንም፡ ጸራ፡ *ሁለት፡ ሁለትም፡ አድርጎ፡ ላካቸው፡ ስልጣንም፡ሰጣቸው፡በርኩሳን፡ መናፍስት፡ ላይ።
*ሉቃ፡ ፲፡ ፩። ፱፡ ፩—፮።
ማቴ፡ ፲፡ ፩፡ ፱፡ ፲።

፰፡ አዘዛቸውም፡ ለመንገድ፡ አንዳች፡ እንዳደወስዱ፡ ከበትር፡ በቀር። ከረጢት፡ ስንኳ፡ እንጀራም፡ ናስም፡ በመቀነታቸው።

፱፡ ከጫማ፡በቀር፡በግራቸው። ሁለት፡ቀሚስም፡ እንደደለብሱ።

፲፡ አላቸውም። ወደ፡ ማናቸውም፡ ቤት፡ ጉብታችሁ፡ ከዚያ፡ እስክትወጡ፡ ድረሱ።

፲፩፡ የማደቀበልዋችሁም፡ ሁሉ፡ከላንትም፡ የማደሰሙ። ከዚያ፡ ወጥታችሁ፡ በግራችሁ፡ በታች፡ ያለውን፡ ትቢያ፡ አርግፉ፡ ለርሳቸው፡ ምስክር፡ እንዲሆን። እውነት፡ እላችኋለሁ፡ ሶደምና፡ ገሞራ፡ዕረፍት፡ እንዲሆንላት፡ በፍርድ፡ ቀን፡ ከዚያች፡ አገር፡ ይልቅ።
ማቴ፡ ፲፡ ፲፬—፵፪።

፲፪፡ በወጡም፡ ጊዜ፡ አስተማሩ፡ ንስሐ፡ ደገቡ፡ ዘንድ።

፲፫፡ እጅግም፡ሰይጣናት፡አወጡ። *በዘይትም፡ብዙ፡ ድውያንን፡ ቀቡ፡ አደንዋቸውም። *ያዕ፡ ፭፡ ፲፬።

፲፬፡ ሄሮድስ፡ ንጉሥም፡ ሰማ፡ (ስሙ፡ ተገልጥዋል
ና)፡ አለም። ዮሐንስ፡ መጥምቅ፡ ከሙታን፡ ተነሣ፡
ስለዚህም፡ ኃይል፡ ይደረግበታል።

ማቴ፡ ፲፬፡ ፩ —፲፪።

፲፭፡ ሌሎችም፡ አሉ፤ ኤልያስ፡ ነው። ደግሞም፡ሌ
ሎች፡ አሉ፡ ነቢይ፡ ነው፡ወይም፡ከነቢያት፡እንደ አንዱ።

ሉቃ፡ ፱፡ ፯፡—፱።

፲፮፡ ሄሮድስ፡ግን፡በሰማ፡ ጊዜ፡ አለ። ዮሐንስ፡እኔ፡
ራሱን፡ የቈረጥሁት፡ ይህ፡ ነው። እርሱ፡ ከሙታን፡
ተነሣ።

፲፯፡ እርሱ፡ ሄሮድስ፡ ልኮ፡ ዮሐንስን፡ወስደት፡ በግ
ዞትም፡ አኑሮት፡ ነበርና፡ ስለ፡ ሄሮድያዳ፡ የፊልጶስ፡
የወንድሙ፡ ምሽት። ምሽት፡ አድርጓት፡ ነበርና።

፲፰፡ ዮሐንስ፡ ሄሮድስን፡ ይለው፡ ነበርና፡ አይገባህ
ም፡ *የወንድምህን፡ ምሽት፡ ትወስድ፡ ዘንድ።

*ዘሌዋ፡ ፲፰፡ ፲፮።

፲፱፡ ሄሮድያዳ፡ ግን፡ ጸልታው፡ ነበረች፡ ልትገድለ
ውም፡ ትሻ፡ ነበረች፡ አልቻለችም።

፳፡ ሄሮድስ፡ ዮሐንስን፡ ይፈራ፡ ነበርና፡ ጻድቅ፡ ቅ
ዱስም፡ እንደ፡ ሆነ፡ ስላወቀው። ይጠብቀውም፡ ነበ
ረ። በሰማውም፡ ጊዜ፡ እጅግ፡ ነገር፡ ያደርግ፡ ነበረ፡ በ
ደስታም፡ ይሰማ፡ ነበረ።

፳፩፡ በምቹ፡ ጊዜ፡ ሄሮድስ፡ በተወለደበት፡ ቀን፡
ለመኳንንቱ፡ ለሻለቆችም፡ ለገሊላም፡ ሹማምት፡
ምሳ፡ ባደረገ፡ ጊዜ።

፳፪፡ የሄሮድያዳ፡ ልጅ፡ ገባችና፡ ዘፈነች። ያም፡ ሄ
ሮድስንና፡ ባንድ፡ የተቀመጡትን፡ ደስ፡ አሰኘ። ንጉ
ሡም፡ ብላቴናዪቱን፡ አላት። የወደድሽውን፡ ለም
ንኝ፡ እሰጥሽ፡ ዘንድ።

፳፫፡ ማለላትም፡ የለምንሽውን፡ እንድሰጥሽ፡ የ
መንግሥቴ፡ እኩል፡ ስንኳ፡ ቢሆን። አስቴ፡ ፭፡ ፫፡ ፮።

፳፬፡ እርስዋ፡ ግን፡ ወጣች፡ እናትዋንም፡ አለች።
ምን፡ ልለምነው። እርስዋም፡አለች። የመጥምቁን፡
የዮሐንስን፡ራስ።

፳፭፡ ብላቴናዪቱም፡ የዚያን፡ጊዜ፡ ፈጥና፡ ወደ፡ ን
ጉሡ፡ገባች፡ እንደህም፡ብትል፡ለመነችው። እሻለሁ፡
አሁን፡ ትሰጠኝ፡ ዘንድ፡ በሰፊድ፡ የመጥምቁን፡ የዮ
ሐንስ፡ ራስ።

፳፮፡ ንጉሡም፡ እጅግ፡ አዘነ። ነገር፡ ግን፡ ስለ፡ መ
ሐላው፡ ከርሱ፡ ጋራም፡ ስለ፡ ተቀመጡት፡ ሊነሣት፡
አልወደደም።

፳፯፡ የዚያን፡ ጊዜም፡ ንጉሡ፡ አንገት፡ ቈራጭ፡ ሰ
ደደ፡ራሱንም፡ለማምጣት፡አዘዘ።እርሱም፡ሔደና፡
ራሱን፡ በግዞት፡ቈረጠ።

፳፰፡ ራሱንም፡ በሰፊድ፡ ይዞ፡ መጣ፡ ለብላቴናዪ
ቱም፡ ሰጣት። ብላቴናዪቱም፡ ለናትዋ፡ ሰጠችው።

፳፱፡ ደቀ፡መዛሙርቱም፡በሰሙ፡ጊዜ፡መጡ፡በድ
ኑንም፡ አነሡና፡ በመቃብር፡ ጨመሩት።

፴፡ ሐዋርያትም፡ ወደ፡ የሱስ፡ ተሰበሰቡ፡ ሁሉን
ም፡ ነገሩት፡ ያደረጉትንም፡ ያስተማሩትንም።

ሉቃ፡ ፱፡ ፲።

፴፩፡ አላቸውም። እላንት፡ ለብቻችሁ፡ ኑ፡ ወደ፡
ምድረ፡ በዳ፡ ስፍራ፡ ጥቂትም፡ ዕረፉ። የሚመጡ፡
የሚሔዱም፡ እጅግ፡ ነበሩና፡ ለመብልም፡ ጊዜ፡ አላ
ገኙም።

፴፪፡ በመርከብም፡ወደ፡ምድረ፡ በዳ፡ ሔዱ፡ ብቻ
ቸውን። ማቴ፡ ፲፬፡ ፲፫፡—፳፩። ሉቃ፡ ፱፡ ፲፩፡—፲፯።

ዮሐ፡ ፮፡ ፩፡—፲፭።

፴፫፡ ሰዎችም፡ ሲሔዱ፡ አዩዋቸው፡ብዙ፡ ሰዎች
ም፡ አወቁበት። ካገር፡ ሁሉ፡ ወጥተው፡ ወደዚያ፡ ፈ
ጠኑ፡ ቀደምዋቸውም፡ ወደርሱም፡ ተሰበሰቡ።

፴፬፡ የሱስም፡ በወጣ፡ ጊዜ፡ እጅግ፡ ሰዎች፡ አየ፡
*አዘነላቸውም። እንደ፡ በጎች፡ ጠባቂ፡ እንደ፡ ሌላቸ
ው፡ነበሩና። እጅግም፡ ነገር፡ያስተምራቸው፡ጀመረ።

*ማቴ፡ ፱፡ ፴፮።

፴፭፡ በመሸም፡ ጊዜ፡ ደቀ፡ መዛሙርቱ፡ ወደርሱ
መጡ፡ አሉም። ስፍራው፡ ምድረ፡ በዳ፡ ነው፡ ጊዜው
ም፡ አለፈ። ም፡ ፳፰፡ ፩፡—፲።

፴፮፡ አሰናብታቸው፡ ወደገር፡ ይሒዱ፡ ወደ፡ መን
ደርም፡ ባጠገባችን፡ ወደላችው፡ እንጀራ፡ ይገዙ፡ ዘን
ድ። የሚበሉት፡ የላቸውምና።

፴፯፡ እርሱ፡ ግን፡መለሰ፡ አላቸውም። እላንት፡ ስ
ጥዋቸው፡ ይብሉ። አሉትም፡ እንሒድ፡ በሁለት፡ መ
ቶ፡ድሪም፡እንጀራ፡እንግዛ፡እንሰጣቸውም፡ ሊበሉ።

፴፰፡ እርሱ፡ግን፡ አላቸው። ስንት፡እንጀራ፡ አላች
ሁ። ሒዱችሁ፡ እዩ። ባወቁም፡ ጊዜ፡ አሉ። አምስት፡
ሁለትም፡ዓሣ።

፴፱፡ አዘዛቸውም፡ ሰዎችን፡ ለማስቀመጥ፡ ከፈ
ለው፡ በለመለመ፡ መስክ፡ ላይ።

፵፡ ተከፋለው፡ተከፋለውም፡ ተቀመጡ። መቶ፡
መቶ። አምሳም፡ አመሳ።

፵፩፡ አምስቱን፡ እንጀራና፡ሁለቱንም፡ ዓሣ፡ ወሰ
ደ፡ *ወደ፡ ሰማይም፡ አየ፡ ባረከም። እንጀራውንም፡
ቈረሰ፡ ለደቀ፡ መዛሙርቱም፡ ሰጠ፡ ሊያቀርቡላቸ
ው። ሁለቱንም፡ዓሣ፡ለሁሉ፡ከፈለ። *ም፡ ፯፡ ፴፬።

፵፪፡ ሁሉም፡ በሉ፡ ጸገቡም።

፵፫፡ ከቍራሹም፡ አነሡ፡ አሥራ፡ ሁለት፡ሞሰብ፡
የመላ፡ ካሣውም።

፵፬፡ እንጀራውንም፡ የበሉ፡ አምስት፡ ሺህ፡ ሰዎ
ች፡ የሚያህሉ፡ ነበሩ።

፵፭፡ በዚያን፡ ጊዜ፡ደቀ፡ መዛሙርቱን፡ ግድ፡ አላ
ቸው፡ ወደ፡ መርከብ፡ እንዲገቡ፡ ወደ፡ ማዶም፡ እን
ዲቀድሙት፡ ወደ፡ ቤተ፡ ሰይዳ፡ አጠገብ። እርሱ፡ ሰ
ዎችን፡ እስኪያሰናበት፡ ድረስ።

ማቴ፡ ፲፬፡ ፳፪፡—፴፮። ዮሐ፡ ፮፡ ፲፭፡—፳፩።

፵፮፡ ካሰናበታቸውም፡ወደ፡ያ፡ወደ፡ተራራ፡ሔደ፡
ይጸልይ፡ ዘንድ።

፵፯፡ በመሸም፡ ጊዜ፡ መርከቢቱ፡ በባሕር፡ መካከ
ል፡ ነበረች፡ እርሱም፡ ለብቻው፡ በምድር፡ ላይ።

፵፰፡ በመቅዘፍ፡ ሲጨነቁም፡አይቶ፡ ነፋስ፡ ከፊቶ
ቻቸው፡ ነበርና፡ ከሌቱ፡ ነራተኛው፡ሰዓት፡ በባሕር፡ ላ
ይ፡ሲሔድ፡መጣባቸው፡ ሊያልፋቸውም፡ይሻ፡ነበር።

፵፱፡ እርሳቸው፡ግን፡በባሕር፡ ላይ፡ሲሔድ፡ ባዩት፡
ጊዜ፡ ምትሐት፡ መሰላቸው፡ ጮሁም።

፶፡ ሁሉ፡አይተውታልና፡ ደነገጡም። የዚያን፡ጊዜ
ም፡ተናገራቸው፡አላቸውም።አይዞቋችሁ፡እኔ፡ነኝ።
አትፍሩ።

፶፩፡ ወደ፡ መርከቡም፡ ወጣ፡ ከርሳቸው፡ ዘንድ።
*ነፋሱም፡ ጸጥ፡ አለ። በልባቸውም፡ እጅግ፡ ያለ፡ ል
ክም፡ ተገረሙ። *ም፡ ፬፡ ፴፱፡፡

፶፪፡ የንጀራውን፡ ድንቅ፡ስራ፡አላስቡምና። ልባቸ
ው፡ ደንደና፡ ነበርና።

፶፫፡ በተሻገሩም፡ ጊዜ፡ ወደ፡ ጌንሴሬጥ፡ ምድር፡
መጡ፡ ተቀመጡም።

፶፬፡ ከመርከብም፡ ሲወጡ፡ በዚያን፡ ጊዜ፡ አወ
ቁት።

፶፭፡ ወደዚያች፡ አገርም፡ ዙርያ፡ሁሉ፡ አፈጠኑ፡ድ
ውያንንም፡ ባልጋ፡ ላይ፡ ይሸከሙ፡ ጀመረ፡ ወደሚሰ
ሙበት፡ ስፍራ፡ ሁሉ፡ ከዚያ፡ እንደለ።

፶፮፡ ወደ፡ ሔደበትም፡ ስፍራ፡ ሁሉ፡ ወደ፡ መንደ
ር፡ ወደ፡ ከተማም፡ ባገርም፡ቢሆን፡ ድውያንን፡ በገቢ
ያ፡ያኖሩ፡ነበር፡ ይለምኑትም፡ ነበረ፡ ደዌሱ፡ ዘንድ፡
የልብሱን፡ ጫፍ፡ ስንኳ፡ ቢሆን። የነካውም፡ ሁሉ፡
ደነ። ም፡ ፭፡ ፳፯፡ ፳፰፡፡

ምዕራፍ፡ ፯፡

፩፡ ፈሪሳውያንም፡ ወደርሱ፡ ተሰበሰቡ፡ ከጻፎች
ም፡ ሰዎች፡ ከየሩሳሌም፡ የመጡ።
ማቴ፡ ፲፭፡ ፩፡—፳፡፡

፪፡ ከደቀ፡ መዛሙርቱም፡ ሰዎች፡ ባዩ፡ ጊዜ፡ እንጀ
ራ፡ ሲበሉ፡ በርኩስ፡(ይህ፡ማለት፡) *ባልታጠበ፡ እጅ፡
ነቀፏቸው። *ሉቃ፡ ፲፩፡ ፴፰፡፡

፫፡ ፈሪሳውያን፡ አይሁድም፡ ሁሉ፡ እጃቸውን፡ ደ
ህና፡አድርገው፡ ሳይታጠቡ፡ አይበሉምና፡ የሽማግሌ
ችን፡ ወግ፡ ይዛሉና።

፬፡ ከገቢያም፡ መጥተው፡ካልታጠቡ፡አይበሉም።
እጅግ፡ ነገርም፡ አለች፡ የተያዙባት። ጽዋ፡ ማጠብ፡
ማድጋም፡ ገቦታም፡ አልጋም።

፭፡ ከዚያ፡ ወዲያም፡ ፈሪሳውያን፡ ጻፎችም፡ ጠየ
ቁት፡ እንደሆ፡ ሲሉ። ለምን፡ ደቀ፡ መዛሙርትህ፡ እ
ንደ፡ ሽማግሌች፡ ወግ፡አይሔዱም። እጃቸውን፡ሳይ
ታጠቡ፡ እንጀራ፡ ይበላሉ፡ እንጂ።

፮፡ እርሱ፡ ግን፡ መለሰ፡ አላቸውም። *ኢሳይያስ፡
ስለላንት፡ እውነት፡ ተናገረ፡አላንት፡ ግብዞች። እንደ፡
ተጻፈ። ይህ፡ ሕዝብ፡ በከንፈሩ፡ያከብረኛል፡ ልቡ፡ ግ
ን፡ ከኔ፡ የራቀ፡ ነው። *ኢሳ፡ ፳፱፡ ፲፫፡፡

፯፡ በከንቱ፡ ያመልኩኛል፡ በሰዎችም፡ ሥርዓት፡
በትምህርታቸውም፡ ኢያስተማሩ።

፰፡ የእግዚአብሔርን፡ ሥርዓት፡ ትታችሁ፡የሽማግ
ሎችን፡ ወግ፡ ትይዛላችሁና፡ እንደ፡ ጽዋን፡ ማጠብ፡
ማድጋንም፡እጅግም፡ ሌላ፡ ነገር፡ ይህነን፡የሚመስል፡
ታደርጋላችሁ።

፱፡ አላቸውም። በጣም፡ የእግዚአብሔርን፡ ሠር
ዓት፡ ተዋችሁ፡ ወጋችሁን፡ ትጠብቁ፡ ዘንድ።

፲፡ ሙሴ፡ ብልዋልና። *አባትህንና፡ እናትህን፡ አክ
ብር፡ አባቱንና፡ እናቱንም፡ የሰደበ፡ ፈጽሞ፡ ይሙት።
*ዘፀአ፡ ፳፡ ፲፪፡፡ ም፡ ፳፩፡ ፲፯፡፡

፲፩፡ እላንተ፡ ግን፡ ትላላችሁ። ሰው፡ ለአባቱ፡ ወይ
ም፡ ለእናቱ፡ ቁርባን፡ ነው፡ (እርሱም፡ ስጦታ፡) ከኔ፡
የምትረባበት፡ ቅርቶልሃል፡ ቢል።

፲፪፡ ሌላም፡ ነገር፡ ላባቱና፡ ለናቱ፡ ያደርግ፡ ዘንድ፡
አተውትም።

፲፫፡ የእግዚአብሔርን፡ ነገር፡ አንሳችሁ፡ በተሰጣች
ሁ፡ በወጋችሁ። እጅግም፡ እንደሁ፡ ያለ፡ ታደርጋላ
ችሁ።

፲፬፡ ሰዎችንም፡ ሁሉ፡ጸራ፡አላቸውም። ሁላችሁ፡
እኔን፡ አድመጹ፡ አስተውሉም።

፲፭፡ ከሰው፡ በሚደ፡ያለ፡ነገር፡ ሁሉ፡ ቢገባበት፡ *ሊ
ያረክሰው፡ አይችልም። ነገር፡ ግን፡ ከርሱ፡ የሚወጣ
ው፡ እርሱ፡ ነው፡ ሰውን፡ የሚያረክሰው።
*የሐ፡ ፲፡ ፲፬፡ ፲፭፡፡

፲፮፡ ማንም፡ የሚሰማ፡ ጆሮ፡ እንደለው፡ ይስማ።

፲፯፡ ከሰውም፡ ተለይቶ፡ ወደ፡ ቤት፡ በገባ፡ ጊዜ፡ ደ
ቀ፡ መዛሙርቱ፡ ስለ፡ ምሳሌው፡ ጠየቁት።

፲፰፡ አላቸውም። እንደህን፡ እላንትም፡ አታስተ
ውሉም። አታውቁምን፡ በሚደ፡ ያለ፡ ሁሉ፡ ወደ፡ ሰ
ው፡ ቢገባ፡ ሊያረክሰው፡ እንደይችል። ም፡ ፮፡ ፶፪፡፡

፲፱፡ ወደ፡ ልቡ፡ አይደርስምና፡ ወደ፡ ሆድ፡ እንጅ፡
ወደ፡ ዓይነ፡ ምድርም፡ ይወጣል፡ መብሉንም፡ ሁሉ፡
ያጠራዋል። ቲቶ፡ ፩፡ ፲፭፡፡

፳፡ አለም፡ ከሰው፡ የሚወጣ፡ እርሱ፡ ነው፡ ሰውን፡
የሚያረክሰው።

፳፩፡ ከውሥት፡ ከሰው፡ ልብ፡ ክፉ፡ አሳብ፡ ይወጣ
ልና፡ ምንዝር፡ ዝሙት፡ ነፍስን፡ መግደል።

፳፪፡ መስረቅ፡ ሥሥት፡ ክፋት፡ ተንኰል፡ ርኩስነ
ት፡ ምቀኝነት፡ ስድብ፡ ትዕቢት፡ ስንፍና።

፳፫፡ ይህ፡ ክፉ፡ ሁሉ፡ ከውሥጥ፡ ይወጣል፡ ሰውን
ም፡ ያረክሳል።

፳፬፡ ከዚያም፡ ተነሣ፡ ወደ፡ ጢሮስና፡ ወደ፡ሲደና፡
ደርቻም፡ ሔደ። ወደ፡ ቤትም፡ ገባ፡ ማንም፡ እንደያ
ውቅበት፡ ወደደ፡ ሊሰወርም፡ አልቻለም።
ማቴ፡ ፲፭፡ ፳፩፡—፳፰፡፡

፳፭፡ አንዲት፡ ሴት፡ ስለርሱ፡ ሰምታለችና፡ ታናሽ፡
ልጅም፡ ነበረቻት፡ ርኩስ፡ መንፈስ፡ የነበረባት። እርሰ
ዋም፡ መጣችና፡ በግሩ፡ ወደቀች።

፳፮፤ ሴቲቱም፡ የፅርዕ፡ ነበረች፡ ትውልድዋም፡ ከፊንቂ፡ ወገን፡ ከሶርያ። ትለምነውም፡ነበረች፡ ከልጅዋ፡ ሰይጣንን፡ ያወጣ፡ ዘንድ። ሮሜ፡ ፩፤ ፲፮፤—፲፯፤፤

፳፯፤ የሱስም፡ አላት። ተዪ፡ ልጆች፡ በፊት፡ ይጸገቡ። መልካም፡ አይደለምና፡ የልጆችን፡ እንጀራ፡ ነሥቶ፡ለቡችሎች፡መስጠት።

፳፰፤ እርስዋም፡ መለሰች፡ አለችውም። አዎን፡ አቤቱ፡ ቡችሎች፡ ደግመው፡ በማዕድ፡ ታች፡ ከሕፃናት፡ ፍርፋሪ፡ ይበላሉና።

፳፱፤ እርሱም፡ አላት። ስለዚህ፡ ነገር፡ ሒጂ። ሰይጣኑ፡ ከልጅሽ፡ ፈጽሞ፡ ወጣ።

፴፤ ወደ፡ ቤትም፡ ሔደች፡ሰይጣኑም፡ ወጥቶ፡ አገኘች፡ ልጅዋም፡ ባልጋ፡ ላይ፡ ተጋድማ።

፴፩፤ ደግሞም፡ ከጢሮስና፡ ከሲደና፡ ደርቻ፡ በወጣ፡ ጊዜ፡ ወደ፡ ገሊላ፡ ባሕር፡ መጣ፡ ባሥሩ፡ አገር፡ መካከል። ማቴ፡ ፲፭፤ ፳፱፤—፴፩፤፤

፴፪፤ ደንቆሮም፡ ድዳም፡ ይዘው፡ወደርሱ፡ መጡ፡ ለመኑትም፡ *እጁን፡ይጭንበት፡ዘንድ። *ም፡ ፭፤ ፳፫፤፤

፴፫፤ ከሰዎችም፡ለይቶ፡ ብቻውን፡ አወጣው፡ ጣቱንም፡ በጆሮው፡ ጨነበት። ምራቁንም፡ *ተፋበት፡ መላሱንም፡ ደሰሰ። *ም፡ ፰፤ ፳፫፤፤

፴፬፤ ወደ፡ሰማይም፡ *አየ፡ቍዘመም፡አለውም። ኤፋታ፡ እርሱም፡ ተከፈት፡ ማለት፡ነው። *ም፡ ፮፤ ፵፩፤፤

፴፭፤ የዚያን፡ጊዜም፡ ጆሮው፡ ተከፈተ፡ የመላሱም፡ እሥራት፡ ተፈታ፡ አጥርቶም፡ ተናገረ። ዮሐ፡ ፲፩፤ ፵፩፤፤

፴፮፤ አዘዛቸውም፡ ለማንም፡ እንዳይናገሩት፡ እርሳቸው፡ ግን፡ *ባዘዛቸው፡ መጠን፡ እጅግ፡ በብዙ፡ ያወሩት፡ነበሩ። *ም፡ ፩፤ ፵፫፤፤

፴፯፤ እጅግም፡ ያደንቁ፡ ነበሩ፡ እንዲህ፡ ኢያሉ። ነገሩን፡ ሁሉ፡ አሳመረ፡ ደናቁርት፡ እንዲሰሙ፡ አደረገ፡ ድዳችም፡ እንዲናገሩ።

## ምዕራፍ፡ ፰፤

፩፤ በዚያ፡ወራት፡ እጅግ፡ሰው፡ በሆነ፡ ጊዜ፡ የሚበሉትም፡ አልነበራቸውም፡የሱስ፡ ደቀ፡መዛሙርቱን፡ ወደርሱ፡ ጸራ፡ አላቸውም። ማቴ፡ ፲፭፤ ፴፪፤—፴፱፤፤

፪፤ እኔ፡ ለሌሁ፡ ሰዎች፡ አዝናለሁ። ከኔ፡ ጋራ፡ ተቀምጠው፡ ሶስት፡ ቀን፡ ሁንዋቸዋልና፡ የሚበሉትም፡ የላቸውም። ም፡ ፮፤ ፴፬፤፤

፫፤ ወደ፡ ቤታቸውም፡ ብሰዳቸው፡ ሳይበሉ፡ በመንገድ፡ ይደክማሉ። ከርሳቸው፡ አያሌ፡ ከሩቅ፡ መጡና።

፬፤ ደቀ፡ መዛሙርቱም፡ መለሱለት፡ እንዲህ፡ ሲሉ። ማንስ፡ ከወዴት፡ እሌህን፡እንጀራ፡ ያጸግብ፡ዘንድ፡ ይችላል፡ ከዚህ፡ በምድረ፡ በዳ።

፭፤ ጠየቃቸውም፡ ስንት፡ እንጀራ፡አላችሁ፡ብሎ። እርሳቸውም፡ አሉ፡ ሰባት።

፮፤ ሕዝቡንም፡ በምድር፡ላይ፡እንዲሰፍር፡አዘዘ። ሰባቱንም፡እንጀራ፡ወሰደ፡ ባረከውም፡ቈረሰውም፡ ለደቀ፡ መዛሙርቱም፡ ሰጠ፡ ያቀርቡላቸው፡ ዘንድ። ለሕዝቡም፡ አቀረቡ።

፯፤ ከርሳቸው፡ ጋራም፡ ጥቂት፡ ዓሣ፡ ነበር፡ እነዚህንም፡ ባረኮ፡ ደግሞ፡ ያቀርቡ፡ ዘንድ፡ አዘዘ።

፰፤ በሉም፡ ጸገቡም። የቍራሹንም፡ ትራፊ፡ አነሡ፡ ሰባት፡ ሞሰብ።

፱፤ የበሉትም፡ አራት፡ ሺህ፡ ይሆናሉ። አሰናበታቸውም።

፲፤ የዚያን፡ ጊዜም፡ ወደ፡ መርከብ፡ ገባ፡ከደቀ፡ መዛሙርቱ፡ ጋራ፡ ወደ፡ ደልማኑታ፡ አጠገብም፡ መጣ።

፲፩፤ ፈሪሳውያንም፡ ወጡ፡ ይከራከሩትም፡ ጀመሩ። ሲፈትኑትም፡ ከርሱ፡ ምልክት፡ ከሰማይ፡ ይሹ፡ ነበሩ። ማቴ፡ ፲፮፤ ፩፤—፲፪፤፤

፲፪፤ ቍዘመም፡ አለ። ለምን፡ ይህ፡ ትውልድ፡ ምልክት፡ ይሻል። እውነት፡ እላችኋለሁ። ለዚህ፡ ትውልድ፡ ምልክት፡ አይሰጠውም።

፲፫፤ ተዋቸውም። ደግሞም፡በመርከብ፡ገባ፡ወደ፡ማዶም፡ ሔደ።

፲፬፤ ደቀ፡መዛሙርቱም፡እንጀራ፡መውሰድ፡ረሱ። ለርሳቸውም፡ በመርከብ፡ አልነበራቸውም፡ ካንድ፡ እንጀራ፡ በቀር።

፲፭፤ እርሱም፡አዘዛቸው፡እንዲህ፡ሲል። እዩ፡ የፈሪሳውያንን፡ *የሄሮድስንም፡ †እርሾ፡ ተጠንቀቁ። *ም፡ ፫፤ ፮፤፤ †ሉቃ፡ ፲፪፤ ፩፤፤

፲፮፤ እርሱ፡ በርሳቸውም፡ ይተያዩ፡ ነበር፡ እንዲህ፡ ሲሉ። እንጀራ፡ ብለ፡ ሌለነ፡ ነው።

፲፯፤ የሱስም፡ ባወቀ፡ ጊዜ፡ አላቸው። ለምን፡ ታስባላችሁ፡ እንጀራ፡ የለነም፡ ብላችሁ። እስካሁንን፡ አታውቁም፡ *አታስተውሉም። እስከ፡ ዛሬስ፡ ልባችሁ፡ ገናን፡ ደንደና፡ ነው። *ም፡ ፮፤ ፶፪፤፤

፲፰፤ ዓይን፡ አላችሁን፡ አታዩምን፡ጆሮም፡ አላችሁን፡ አትሰሙምን፡ አታስቡምን።

፲፱፤ *አምስት፡ እንጀራ፡ላምስት፡ሺህ፡በቈረስሁ፡ ጊዜ፡ ስንት፡ ሞሰብ፡ ቍራሽ፡ የመላ፡ወሰዳችሁ። አሉት። አሥራ፡ ሁለት። *ም፡ ፮፤ ፵፩፤፤

፳፤ *በሰባቱስ፡ ጊዜ፡ ላራት፡ ሺህ። ስንት፡ ሞሰብ፡ ወሰዳችሁ፡ ቍራሽ፡ የመላ። እርሳቸውም፡ አሉ። ሰባት። *ቍ፡ ፭፤፤

፳፩፤ አላቸውም፡ እንዴት፡ አታስተውሉምን።

፳፪፤ ወደ፡ ቤተ፡ ሰይዳም፡ መጣ። ዕውርም፡ አመጡለት፡ *ይዳሰውም፡ ዘንድ፡ ለመኑት። *ም፡ ፮፤ ፶፮፤፤

፳፫፤ የውሩንም፡ እጅ፡ ያዘው፡ ካገርም፡ ወደ፡ ሜዳ፡ አወጣው፡ ባይኑም፡ ተፋበት፡እጁንም፡ ጨነበት፡ ጠየቀውም፡አንዳች፡ ያይ፡ እንደሆን። ም፡ ፯፤ ፴፪፤ ፴፫፤፤

፳፬፤ አሻቅቦም፡ ተመልክቶ፡ ሰዎችን፡እንደ፡ ዛፍ፡ ሲሔዱ፡ አያለሁ፡ አለ።

፳፭፡ ደግሞም፡ እጁን፡ ባይኑ፡ ላይ፡ ጫነበት፡ እን ደ፡ መለከትም፡ አደረገው። ደነም፡ ሁሉንም፡ ገልጦ፡ አየ።

፳፮፡ ወደ፡ቤቱም፡ሰደደው፡ እንዲህ፡ ሲል። ወደ፡ መንደር፡ አትግባ፡ በምንደርም፡ *ለማንም፡አንዳች፡ አትናገር። *ምዕ፡ ፯፡ ፴፮፡፡

፳፯፡ የሱስም፡ወጣ፡ደቀ፡መዛሙርቱም፡ ወደ፡ ፊ ልጶስ፡ ቂሣርያ፡ መንደሮች። በመንገድም፡ ደቀ፡ መ ዛሙርቱን፡ጠየቀ፡ እንዲህ፡ ሲላቸው። ምን፡ ይላሉ፡ ሰዎች፡ እኔ፡ እንደ፡ ሆንሁ። ማቴ፡ ፲፮፡ ፲፫፡ ፳፰፡፡ ሉቃ፡ ፱፡ ፲፰፡—፳፯፡፡

፳፰፡ እርሳቸውም፡ መለሱ። ሰዎች፡ ይላሉ፡ መጥ ምቁ፡ ዮሐንስ፡ ነው። ሌሎችም፡ ኤልያስ፡ ነው። ሌሎ ችም፡ ከነቢያት፡ አንዱ፡ ነው። ምዕ፡ ፮፡ ፲፭፡፡

፳፱፡ እርሱም፡አላቸው። እላንተስ፡ምን፡ ትላላች ሁ፡እኔ፡እንደ፡ሆንሁ። ጴጥሮስም፡መለሰ፡አለውም። አንተ፡ ክርስተስ፡ ነህ።

፴፡ ገሠጻቸውም፡ ለማንም፡ አንዳች፡ እንደይናገ ሩ፡ ስለርሱ። ምዕ፡ ፱፡ ፱፡፡

፴፩፡ ያስተምራቸውም፡ ጀመረ፡ የሰው፡ ልጅ፡ እ ጅግ፡ መከራ፡ ይቀበል፡ ዘንድ፡ እንዲገባው፡ ከሽማግ ሎችና፡ ከካህናትም፡አለቆች፡ከጻፎችም፡ይናቅ፡ ይገ ደልም፡ ዘንድ፡ ከሶስት፡ ቀንም፡ በኋላ፡ከሙታን፡ ይነ ሣ፡ ዘንድ።

፴፪፡ ይህነንም፡ ነገር፡ ገልጾ፡ ይናገር፡ ነበር። ጴጥሮስ ም፡ ያዘበት፡ ሊቈጣውም፡ ጀመረ።

፴፫፡ እርሱ፡ ግን፡ ዞረ፡ ወደ፡ ደቀ፡ መዛሙርቱም፡ አየ፡ ጴጥሮስንም፡ ተቈጣው፡ እንዲህ፡ ሲል። ከኋላ ዬ፡ ሒድ፡ አንተ፡ ሰይጣን። የእግዚአብሔርን፡ አታስ ብምና፡ የሰውን፡ እንጂ።

፴፬፡ ሕዝብንም፡ ከደቀ፡ መዛሙርቱ፡ ጋራ፡ ጸራ፡ አላቸውም። በኋላዬ፡መምጣት፡የሚወድ፡ ነፍሱን፡ ይካድ፡ መስቀሉንም፡ ይሸከም፡ ይከተለኝም።

፴፭፡ ነፍሱንም፡ማዳን፡ የሚወድ፡ይጥላታል። ነፍ ሱንም፡ የጣለ፡ ስለኔ፡ ስለ፡ ወንጌልም፡ እርሱ፡ ያድና ታል። ማቴ፡ ፲፡ ፴፱፡፡

፴፮፡ ለሰውም፡ ምን፡ ይረባዋል፡ ዓለምን፡ ሁሉ፡ ቢያተርፍ፡ ነፍሱንም፡ ቢያጐድል።

፴፯፡ ወይስ፡ ምን፡ ይሰጣል፡ ሰው፡ የነፍሱ፡ ቤዛ።

፴፰፡ በኔም፡ ያፈረ፡ ሁሉ፡ በነገሬም፡በዚህ፡ በዘማ ዊ፡ ትውልድ፡ በኃጢአተኛም። የሰው፡ ልጅ፡ ደግሞ፡ በርሱ፡ ያፍራል፡ባባቱ፡ ምስጋና፡ በመጣ፡ ጊዜ፡ ከመላ እክት፡ ቅዱሳኑ፡ ጋራ። ማቴ፡ ፲፡ ፴፫፡፡

## ምዕራፍ፡ ፱፡

፩፡ አላቸውም፡ እውነት፡ እላችኋለሁ፡ ከዚህ፡ ከ ቆሙት፡ ሰዎች፡ አሉ፡ ሞትን፡ የማይቀምሱት፡ የእግ ዚአብሔርን፡ መንግሥት፡እስኪያዩ፡ድረስ፡ በኃይል፡ ስትመጣ።

፪፡ ከስድስት፡ ቀንም፡ በኋላ፡ የሱስ፡ ጴጥሮስን፡ ያ ዕቆብንም፡ዮሐንስንም፡ ወሰደ፡ወደ፡ ረጅም፡ተራራ ም፡ አወጣቸው፡ ለብቻቸው፡ በፊታቸውም፡ ተለ ወጠ። ማቴ፡ ፲፯፡ ፩፡—፲፫፡፡ ሉቃ፡ ፱፡ ፳፰፡—፴፮፡፡

፫፡ ልብሱም፡ አበራ፡ እጅግም፡ እንደ፡ በረደ፡ ነጭ፡ ነበረ፡ አፃቢ፡ በምድር፡ ላይ፡ እንደርሱ፡ ነጭ፡ ያደርግ፡ ዘንድ፡ የማይችል።

፬፡ ኤልያስም፡ ተገለጠላቸው፡ ከሙሴ፡ ጋራ፡ ከየ ሱስ፡ ጋራም፡ ይናገሩ፡ ነበሩ።

፭፡ ጴጥሮስም፡ መለሰ፡ የሱስንም፡ አለ። መምህ ር፡ ሆይ፡ መልካም፡ ነው፡ ከዚህ፡ ብንቀመጥ። ሶስት ም፡ ድስ፡ እንስራ። ላንተ፡ አንድ፡ ለሙሴም፡ አንድ፡ ለኤልያስም፡ አንድ።

፮፡ የሚለውን፡ አላወቅምና፡ እጅግ፡ ስለ፡ ፈሩ።

፯፡ ደመናም፡ሰውርዋቸው፡ነበር። ከደመናም፡ ድ ምጽ፡ መጣ፡ እንዲህ፡ሲል። *ይህ፡ ነው፡የምወደው፡ ልጂ። እርሱን፡ ስሙት። *፪፡ ጴጥ፡ ፩፡ ፲፯፡፡

፰፡ ድንገትም፡ ዙረው፡ ተመለከቱ፡ ማንንም፡ አላ ዩም፡ ከየሱስ፡ ከብቻው፡ በቀር፡ ከርሳቸው፡ ጋራ።

፱፡ እርሳቸውም፡ከተራራ፡ሲወርዱ፡ከለከላቸው፡ ያዩትን፡ ለማንም፡ እንዳይናገሩ፡ የሰው፡ ልጅ፡ ከሙ ታን፡ እስኪነሣ፡ ድረስ። ምዕ፡ ፰፡ ፴፡፡

፲፡ ነገሬቱንም፡ ያዝዋት። ሲመራመሩ፡ ከሙታን፡ መነሣት፡ ምንድር፡ ነው።

፲፩፡ እንዲህም፡ ሲሉ፡ ጠየቁት። ለምን፡ ይላሉ፡ ጸ ፎች፡ ኤልያስ፡ አስቀድሞ፡ ይመጣ፡ ዘንድ፡ እንዲገ ባው።

፲፪፡ እርሱ፡ ግን፡ መለሰ፡ አላቸውም። ኤልያስ፡ በ ውነት፡ አስቀድሞ፡ ይመጣል፡ ሁሉንም፡ ያቀናናል። እንደ፡ *ተጻፈም፡ የሰው፡ ልጅ፡እጅግ፡ መከራ፡እንዲ ቀበል፡ እንዲናቅም። *ኢሳ፡ ፶፫፡ ፫፡፡

፲፫፡ ነገር፡ ግን፡እላችኋለሁ። *ኤልያስ፡ ፈጽሞ፡ መ ጣ። የወደዱትንም፡ ሁሉ፡ አደረጉበት፡ ስለርሱ፡ እን ደ፡ ተጻፈ። *ማቴ፡ ፲፩፡ ፲፬፡፡ ፩፡ ነገሥ፡ ፲፱፡ ፪፡ ፲፡፡

፲፬፡ ወደ፡ ደቀ፡ መዛሙርቱም፡ መጣ፡ እጅግም፡ ሰዎች፡ በዙርያቸው፡ አየ፡ ጻፎችም፡ ሲጠይቋቸው። ማቴ፡ ፲፯፡ ፲፬፡—፳፩፡፡ ሉቃ፡ ፱፡ ፴፯፡—፵፪፡፡

፲፭፡ የዚያን፡ ጊዜም፡ሰዎች፡ ሁሉ፡ ባዩት፡ ጊዜ፡ ደነ ገጡ፡ ወደርሱም፡ ፈጥነው፡ ሔደ፡ ተገናኙትም።

፲፮፡ ጻፎችንም፡ ጠየቀ። ምን፡ ትሻላችሁ፡ ከርሳ ቸው።

፲፯፡ ከሕዝቡም፡ አንዱ፡ መለሰ፡አለም። መምህ ር፡ ሆይ፡ ልጄን፡ ወዳንተ፡ አመጣሁት፡ በርሱም፡የማ ይናገር፡ መንፈስ፡ አለበት።

፲፰፡ ባገኘውም፡ ሁሉ፡ ስፍራ፡ ይጥለዋል፡ ያራግጠ ዋልም። ጥርሱንም፡ ያፋጫል፡ ይደርቅማል። ደቀ፡ መዛሙርትህንም፡ አልኋቸው፡ ያወጡት፡ ዘንድ፡ አ ልቻሉም።

፲፱፡ እርሱ፡ ግን፡ መለሰለት፡ አለም። እላንት፡ ያላ

መነ፡ ትውልድ። እስከ፡ መቼ፡ ከላንተ፡ ጋራ፡ እኖራለሁ፡ እስከ፡ መቼስ፡ እሽከማችኋለሁ። ወደኔ፡ አምጡት።

፳፤ ወደርሱም፡ አቀረቡት። ባየውም፡ ጊዜ፡ የዚያን፡ ጊዜውን፡ ጣለው፡ ኢያራገጠ፡ ጋኔኑ። በምድር፡ ላይም፡ ወደቀ፡ አረፋቱንም፡ ያደፈቅ፡ ጀመረ።

፳፩፤ አባቱንም፡ጠየቀው። ከስንት፡ አመት፡ጀምሮ፡ አገኘው፡ ይህ። እርሱ፡ ግን፡ መለሰ፡ አለም፡ ከሕፃንነት፡ ጀምሮ።

፳፪፤ ብዙ፡ ጊዜም፡ ወደ፡ እሳት፡ ጣለው፡ ወደ፡ ውኃም፡ ሊገለው። ነገር፡ ግን፡ ይቻልህ፡ እንደ፡ ሆን፡ ማረነ፡ እርደነም።

፳፫፤ የሱስም፡ አለው። ታምን፡ ዘንድ፡ ትችል፡ እንደ፡ ሆንህ፡ *ሁሉ፡ ለሚያምን፡ ይቻልዋል። *ም፡ ፲፩፡ ፳፫።

፳፬፤ የዚያን፡ ጊዜም፡ ሙኸ፡ የብላቴናው፡ አባት፡ ኢያለቀሰ፡ አለም። ጌታ፡ ሆይ፡ አምናለሁ። *አለማመኔን፡ እገዘው። *ሉቃ፡ ፲፯፡ ፭።

፳፭፤ የሱስም፡ የሰዎችን፡መራወጥ፡አይቶ፡ርኩሱን፡ መንፈስ፡ ገሠጸው፡እንደህ፡ ሲለው። አንተ፡ የማይናገር፡ መንፈስ፡ ደንቆርም፡ እኔ፡አዘዝሁህ፡ ከርሱ፡ ትወጣ፡ ዘንድ፡ ደግመህም፡ አትግባበት።

፳፮፤ መንፈሱም፡ ሙኸ፡ እጅግም፡ አራገጠው፡ ከርሱም፡ ወጣ። እንደ፡ ሞተም፡ ሆነ። እጅግ፡ ሰዎች፡ እስኪሉ፡ ድረስ፡ ፈጽሞ፡ሞተ። ም፡ ፩፡ ፳፮።

፳፯፤ የሱስ፡ ግን፡ እጁን፡ ያዘው፡ አስነሣውም፡ ተነሣም።

፳፰፤ ወደ፡ቤትም፡በገባ፡ጊዜ፡ደቀ፡ መዛሙርቱ፡ ለብቻው፡ ጠየቁት፡ ለምን፡ እኛ፡ አልቻልነም፡እናወጣው፡ ዘንድ።

፳፱፤ አላቸውም። እንደህ፡ ያለው፡ ዘመድ፡ ይወጣ፡ ዘንድ፡ አይቻልም፡ በጸሎትና፡ በጾም፡ በቀር።

፴፤ ከዚያም፡ ወጡ፡ በገሊላም፡ አለፉ። ማንም፡ ያውቅ፡ ዘንድ፡ አልወደደም። ማቴ፡ ፲፯፡ ፳፪፡ ፳፫። ሉቃ፡ ፱፡ ፵፫፡—፵፭።

፴፩፤ ደቀ፡ መዛሙርቱን፡ አስታውቀ፡ ብልዋቸው፡ ነበርና። የሰው፡ ልጅ፡ በሰዎች፡ እጅ፡ ይሰጣል፡ ይገሉትማል። በተገደለም፡ ጊዜ፡ ከሶስተኛው፡ ቀን፡ ይነሣል። ም፡ ፰፡ ፴፩። ፲፡ ፴፪።

፴፪፤ *እርሳቸው፡ ግን፡ ይህነን፡ ነገር፡ አላስተዋሉም፡ ይጠይቁትም፡ ዘንድ፡ ፈሩ። *ሉቃ፡ ፲፰፡ ፴፬።

፴፫፤ ወደ፡ ቅፍርናሆም፡መጣ። በቤትም፡ ሳለ፡ ጠየቃቸው። ምን፡ ታስቡ፡ ነበራችሁ፡በመንገድ፡ እርሱ፡ በርሳችሁ። ማቴ፡ ፲፰፡ ፩፡—፲፬። ሉቃ፡ ፱፡ ፵፮፡—፶።

፴፬፤ እርሳቸው፡ ግን፡ ዝማሉ። በመንገድ፡ እርሱ፡ በርሳቸው፡ ይናገሩ፡ ነበሩና፡ ከርሳቸው፡ ማን፡ ይበልጣል።

፴፭፤ ተቀመጠም፡ አሥራ፡ ሁለቱንም፡ ጸራቸው፡ አላቸውም። ማንም፡ በፊት፡ ይሆን፡ ዘንድ፡ ቢወድ፡ ከሁሉ፡ በኋላ፡ ይሁን፡ ለሁሉም፡ ሎሌ፡ ይሁን። ማቴ፡ ፳፡ ፳፮።

፴፮፤ ሕፃንም፡ ወሰደና፡ በመካከላቸው፡ አቀመው። በብብቱም፡ አደርጎ፡ አላቸው። ማር፡ ፲፡ ፴፬። ሉቃ፡ ፳፪፡ ፳፯።

፴፯፤ ከለዚህ፡ሕፃናት፡ አንዲን፡ በስሜ፡ የሚቀበል፡ እኔን፡ ደግሞ፡ ተቀበለኝ። የሚቀበለኝም፡ እኔን፡ አይቀበልም፡ የላከኝን፡ እንጂ። ም፡ ፲፡ ፲፮። ማቴ፡ ፲፡ ፵።

፴፰፤ ዮሐንስም፡ መለሰለት፡ እንደህ፡ ሲል። መምህር፡ ሆይ፡ አንድ፡ ሰው፡ አየነ፡ ሰይጣናትን፡ ሲያወጣ፡ በስምህ፡ የማይከተለነ። ከለከልነውም፡ አይከተለነምና። ዘኁል፡ ፲፩፡ ፳፯፡ ፳፰።

፴፱፤ የሱስ፡ ግን፡ አላቸው፡ አትከልክሉት። *ማንም፡በስሜ፡ ኃይል፡ ኢየሰራ፡ተሎ፡ በኔ፡ ላይ፡ ክፉ፡ ሊናገር፡አይችልምና። *፩፡ ቆር፡ ፲፪፡ ፫።

፵፤ በላያችሁ፡ የማይሆን፡ ሁሉ፡ ከላንት፡ ጋራ፡ ነውና። ማቴ፡ ፲፪፡ ፴።

፵፩፤ የውኃም፡ ጽዋ፡ ያጠጣችሁ፡ ሁሉ፡ በስሜ፡ ለክርስቶስ፡ ስለ፡ ሆናችሁ። እውነት፡ እላችኋለሁ፡ ዋጋው፡ እንደይጠፋ። ማቴ፡ ፲፡ ፵፪።

፵፪፤ ከለዚህም፡ከታናናሾች፡በኔ፡ከሚያምኑ፡አንዲን፡ያስካደ፡ ይሻለዋል፡የወፍጮ፡ ደንጊያ፡ ባንገቱ፡ ቢደረግ፡ ወደ፡ ባሕርም፡ ቢጣል።

፵፫፤ እጅህም፡ብታስትህ፡ ቍረጣት። አንካሳ፡ ሁነህ፡ወደ፡ሕይወት፡ብትገባ፡ይሻልሃልና። ሁለት፡እጅ፡ ኑሮህ፡ ወደ፡ገሃነም፡ከትሔድ፡እሳቱ፡ ወደማይጠፋ። ማቴ፡ ፭፡ ፴።

፵፬፤ ትላቸው፡ ወደማይሞት፡ እሳቱም፡ ወደማፈጠፋ።

፵፭፤ እግርህም፡ ብታስትህ፡ቍረጣት። ወደ፡ ሕይወት፡ ብትገባ፡ ይሻልሃልና፡ አንተ፡ አንካሳ፡ሁነህ፡ ሁለት፡ እግር፡ ኑሮህ፡ ወደ፡ ገሃነም፡ከትገባ፡ወደማይጠፋው፡ እሳት።

፵፮፤ ትላቸው፡ ወደማይሞት፡ እሳትም፡ የማይጠፋ። ቍ፡ ፵፬።

፵፯፤ ዓይንህም፡ ብታስትህ፡ አውጣት። ባንድ፡ ዓይን፡ ወደ፡ መንግሥተ፡ እግዚአብሔር፡ ብትገባ፡ ይሻልሃልና። ሁለት፡ አይን፡ ኑሮህ፡ ወደ፡ እሳት፡ ገሃነም፡ ከትጣል። ማቴ፡ ፭፡ ፳፱።

፵፰፤ ትሉ፡ የማይሞት፡ እሳቱም፡ የማይጠፋ። ቍ፡ ፵፬፡ ፵፮።

፵፱፤ ሁሉ፡ በሳት፡ ይጣፈጣልና። *መሥዋዕትም፡ ሁሉ፡ በጨው፡ ይሳላል። *ዘሌዋ፡ ፪፡ ፲፫።

፶፤ ጨው፡ መልካም፡ ነው። ጨው፡ ግን፡ አልጫ፡ ከሆነ፡ በምን፡ ይጣፈጣል። በሰውነታችሁ፡ ጨው፡ ይሁን፡ እርሱ፡ በርሳችሁም፡ በሰላም፡ ሁኑ። ማቴ፡ ፭፡ ፲፫። ሉቃ፡ ፲፬፡ ፴፬። ቆላ፡ ፬፡ ፮።

ምዕራፍ፡ ፲፤

፩፤ ከዚያም፡ ተነሥቶ፡ ወደ፡ *ይሁዳም፡አገር፡መጣ፡ በዮርዳኖስ፡ ማዶ፡ ደግሞም፡ ብዙ፡ ሰዎች፡ ወደርሱ፡ መጡ፡ እንደ፡ ልማዱም፡ ደግሞ፡ ያስተምራቸው፡ ነበረ። *ማቴ፡ ፲፱፡ ፩፡—፱። ምዕ፡ ፱፡ ፵፫።

፪፤ ፈሪሳውያንም፡ ወደርሱ፡ መጡ፡ ሊፈትኑት፡ጠየቁትም። ለሰው፡ ይገባልን፡ መሽቱን፡ይፈታ፡ ዘንድ።

፫፤ እርሱ፡ ግን፡ መለሰ፡ አላቸውም፡ ሙሴ፡ ምን፡ አዘዛችሁ።

፬፤ እርሳቸውም፡ አሉ። ሙሴ፡ አዘዘ፡ የፍቹ፡ ጽሕፈት፡ጽፎ፡እንዲፈታት። ዘዳግ፡ ፳፬፡ ፩። ማቴ፡ ፭፡፴፩።

፭፤ የሱስም፡ መለሰ፡ አላቸውም። ስለ፡ ልባችሁ፡ ክፋት፡ ይህነን፡ ትእዛዝ፡ ጻፈላችሁ።

፮፤ ከፍጥረት፡ መጀመርያ፡ ግን፡ ተባትና፡ እንስት፡ አደረጋቸው፡ እግዚአብሔር። ዘፍጥ፡ ፩፡ ፳፯።

፯፤ ስለዚህ፡ ሰው፡ አባቱንና፡ እናቱን፡ ይተዋል፡ ከምሽቱም፡ ጋራ፡ አንድ፡ ይሆናል። ዘፍጥ፡ ፪፡ ፳፬።

፰፤ ሁለቱም፡ አንድ፡ ሥጋ፡ ይሆናሉ። ገና፡ ሁለት፡ አይደሉምና፡ አንድ፡ ሥጋ፡ እንጂ።

፱፤እግዚአብሔር፡ያጋጠመውን፡ሰው፡አይለየው።

፲፤ በቤትም፡ ደግሞ፡ ደቀ፡ መዛሙርቱ፡ ስለዚህ፡ ጠየቁት።

፲፩፤ አላቸውም፡ ምሽቱን፡ ፈቶ፡ ሌላዪቱን፡ ያገባ፡ ፈጽሞ፡ አመነዘረባት።

፲፪፤ ሴትም፡ ባልዋን፡ ትታ፡ ሌላ፡ ብታገባ፡አመንዝራ፡ ሆነች።

፲፫፤ ሕፃናትንም፡ ወደርሱ፡ አመጡ፡ ሊደሳቸው፡ ደቀ፡ መዛሙርቱ፡ ግን፡ ያመጥዋቸውን፡ ተቈጥዋቸው። ማቴ፡ ፲፱፡ ፲፫፡—፲፭። ሉቃ፡ ፲፰፡ ፲፭፡—፲፯።

፲፬፤ የሱስም፡ ባያቸው፡ ጊዜ፡ አዘነ፡ አላቸውም። ተው፡ ሕፃናት፡ወደኔ፡ይምጡ፡አትከልክልዋቸው።የእግዚአብሔር፡ መንግሥት፡ እንደለዚህ፡ ላሉት፡ ናትና።

፲፭፤ እውነት፡አላችኋለሁ። የእግዚአብሔርን፡ መንግሥት፡ያልተቀበለ፡እንደ፡ ሕፃን፡ አይገባባትም። ማቴ፡ ፲፰፡ ፫፡ ፮።

፲፮፤ በብብቱም፡አኖራቸው፡እጁንም፡ጫነባቸው፡ ባረካቸውም። ምዕ፡ ፱፡ ፴፮።

፲፯፤ እርሱም፡በመንገድ፡ ወጥቶ፡ሳለ፡አንድ፡ሰው፡ ወደርሱ፡ አፈጠነ፡ በጕልበቱም፡ ሰገደለት፡ ጠየቀውም። አንተ፡ ቸር፡ መምህር። ምን፡ ልስራ፡ የዘላለም፡ ሕይወት፡ እወርስ፡ ዘንድ።

፲፰፤ የሱስ፡ ግን፡ አለው። ለምን፡ ቸር፡ ትለኛለህ። አንድም፡ ቸር፡ የለም፡ ካንዱ፡ በቀር፡ እርሱም፡ እግዚአብሔር።

፲፱፤ ትእዛዙን፡ታውቃለህ። *አታመንዝር። አትግደል። አትስረቅ። ባሰት፡ አትመስክር። አትጽላ። አባትህንና፡ እናትህን፡ አክብር። *ዘፀአ፡ ፳፡ ፲፪።

፳፤ እርሱም፡ መለሰ፡ አለውም። መምህር፡ ሆይ፡ ይህነን፡ ሁሉ፡ ጠበቅሁ፡ ከታናሽነቴ፡ ጀምሬ።

፳፩፤ የሱስም፡ ወደርሱ፡ ተመልክቶ፡ ወደደው፡ አለውም። አንዲት፡ነገር፡ታሸሃለች። ሒድ፡ያላህንም፡ ሁሉ፡ሽጥ፡ ለድኆችም፡ ስጥ። በሰማይም፡ ይከማች ልሃል። ናናም፡ ተከተለኝ፡ *መስቀልም፡ ተሸከም። *ማቴ፡ ፲፡ ፴፰።

፳፪፤ እርሱ፡ ግን፡ ስለዚህ፡ ነገር፡ አዘነ፡ ከፍቶትም፡ ሔደ። እጅግ፡ ባለ፡ ከብት፡ ነበርና።

፳፫፤ የሱስም፡ ወደ፡ ዙርያው፡ አየ፡ ደቀ፡ መዛሙርቱንም፡ አላቸው። እንዴት፡ *ይጨንቃል፡ ባለ፡ ከብት፡ ወደ፡ እግዚአብሔር፡ መንግሥት፡ መግባት።

፳፬፤ ደቀ፡መዛሙርቱም፡አደነቁ፡ከነገሩ፡የተነሣ። የሱስም፡ ደግሞ፡ መለሰ፡ አላቸውም። አላንት፡ ልጆች፡እንዴት፡ ጭንቅ፡ ነው፡ በከብት፡ *ለሚታመኑ፡ ወደ፡እግዚአብሔር፡ መንግሥት፡ ይገቡ፡ ዘንድ። *መዝ፡ ፷፪፡ ፲፩። ፩፡ ጢሞ፡ ፮፡ ፲፯።

፳፭፤ የግመል፡ መግባት፡ በመርፌ፡ ቀዳዳ፡ አያስቸግርም፡ ባለጠጋ፡ ወደ፡ እግዚአብሔር፡መንግሥት፡ ከመግባት።

፳፮፤ መደነቅም፡ አበዙ፡ እንደሁ፡ ሲሉ፡እርስ፡በርሳቸው። ማን፡ ይችላል፡ ይድን፡ ዘንድ።

፳፯፤ የሱስም፡ ወደርሳቸው፡አየ፡ አለም። በሰው፡ ዘንድ፡አይቻልም። ነገር፡ግን፡በእግዚአብሔር፡ዘንድ፡ አይደለም።በእግዚአብሔር፡ዘንድ፡ሁሉ፡ይቻላልና።

፳፰፤ ጴጥሮስም፡ ይለው፡ ጀመረ። እነሆ፡ እኛ፡ ሁሉን፡ ተውነና፡ ተከተልነህ።

፳፱፤ የሱስም፡ መለሰ፡ አለም። እውነት፡ እላችኋለሁ። ማንም፡ቤትን፡አልተውም፡ ወንድሞችንም፡ እኅቶችንም፡ አባትንም፡ እናትንም፡ ምሽትንም፡ ልጆችንም፡ እርሻውንም፡ ስለኔ፡ ስለ፡ ወንጌልም።

፴፤ መቶ፡ ዕፅፍ፡ይወስዳል፡ እንጂ፡ ዛሬ፡ በዚህ፡ ዘመን፡ ቤቶች፡ ወንድሞችም፡ እኅቶችም፡ እናቶችም፡ ልጆችም፡ እርሻም፡ ከመከራና፡ ከስደት፡ ጋራ። በሚመጣውም፡ ዓለም፡ የዘላለም፡ ሕይወት። ሮሜ፡ ፲፮፡ ፲፫።

፴፩፤ ነገር፡ ግን፡ ብዙ፡ የፊተኞች፡ ወደ፡ ኋላ፡ ይሆናሉ፡ የኋለኞችም፡ ወደ፡ ፊት።

፴፪፤በመንገድም፡ነበሩ፡ወደ፡የሩሳሌም፡ሲወጡ። የሱስም፡ በፊታቸው፡ ነበረ፡ እርሳቸውም፡ ይደነቁ፡ ነበሩ፡ ፈርተውም፡ ይከተሉት፡ ነበር። አሥራ፡ ሁለቱንም፡ ደግሞ፡ ወስዶቸው፡ ይደርስበት፡ ዘንድ፡ ያለውንም፡ ይነግራቸው፡ ጀመረ፡ እንደሁ፡ ሲል።

፴፫፤ እነሆ፡ እኛ፡ ወደ፡ የሩሳሌም፡ እንወጣለን፡ የሰው፡ልጅም፡ ወደ፡ካህናት፡ አለቆች፡ወደ፡ጻፎችም፡ እጅ፡ ይሰጣል። የሞት፡ ፍርድም፡ ይፈርዱበታል፡ ለአሕዛብም፡ አሳልፎ፡ ይሰጡታል። ማቴ፡ ፳፡ ፲፯፡—፲፱። ሉቃ፡ ፲፰፡ ፴፩፡—፴፬።

፴፬፡ ያፌዙበትማል፡ይገርፉትማል፡ይተፉበትማ
ል፡ ይገሉትማል። በሦስተኛውም፡ ቀን፡ ይነሣል።
፴፭፡ ወደርሱም፡ ቀረቡ፡ ያዕቆብና፡ ዮሐንስ፡ የዘ
ብደዎስ፡ ልጆች፡ እንደይህ፡ ሲሉ። መምህር፡ ሆይ፡ እ
ንሻለን፡ የለመንኸን፡ ታደርግልን፡ ዘንድ።

ማቴ፡ ፳፡ ፳፡—፳፰፡፡

፴፮፡ እርሱም፡ አላቸው። ምን፡ ትሻላችሁ፡ አደር
ግላችሁ፡ ዘንድ።

፴፯፡ እርሳቸውም፡ አሉት። ስጠነ፡አንደኛችን፡ በቀ
ኝህ፡ አንደኛችንም፡ በግራህ፡ እንቀመጥ፡ዘንድ፡ በም
ስጋናህ።

፴፰፡ የሱስ፡ ግን፡አላቸው። የምትለምኑትን፡አታ
ውቁም። ትጠጡ፡ዘንድ፡ ትችላላችሁን፡ እኔ፡ የምጠ
ጣን፡*ጽዋ። ትጠመቁስ፡ አላችሁን፡ እኔ፡ የምጠመ
ቃትን፡ †ጥምቀት። *ም፡ ፲፬፡ ፴፯፡፡ †ሉቃ፡ ፲፪፡ ፶፡፡

፴፱፡ እርሳቸውም፡ አሉ፡ እንችላለን። የሱስም፡
አላቸው፡ *ጽዋዬቱን፡ እኔ፡ የምጠጣትን፡ትጠጣላች
ሁ። ጥምቀትንም፡ እኔ፡ የምጠመቃትን፡ትጠመቃላ
ችሁ። *የሐዋ፡ ፲፪፡ ፪፡፡

፵፡ በቀኜና፡ በግራዬ፡ መቀመጥ፡ ግን፡እሰጠው፡ ዘ
ንድ፡ የለኝም። ለተዘጋጀላቸው፡ እንጂ።

፵፩፡ አሥሩም፡ በሰሙ፡ ጊዜ፡ በያዕቆብና፡ በዮሐ
ንስ፡ ተቈጡ።

፵፪፡ የሱስም፡ ወደርሱ፡ ጸራቸው፡ አላቸውም።
የአሕዛብ፡ አለቆች፡ እንደሚሆኑ፡ የሚመስላቸውን፡
አወቃችሁ፡በላያቸው፡ጌቶች፡ናቸው፡ታላላቆቻቸው
ም፡ ይገዟቸዋል።

፵፫፡ በላንትስ፡ እንደይህ፡ አይሆንባችሁም። ከላን
ት፡ ታላቅ፡ መሆን፡ የሚወድ፡ ለላንት፡ ሎሌ፡ ይሁን፡
እንጂ።

፵፬፡ በላንትም፡ የከበረ፡ መሆን፡ የሚወድ፡ ለሁ
ሉ፡ ሎሌ፡ ይሁን። ም፡ ፱፡ ፴፭፡፡

፵፭፡ የሰው፡ ልጅ፡ ደግሞ፡ አልመጣምና፡ ሊያገለ
ግሉት፡ ሊያገለግል፡ እንጂ፡ ነፍሱንም፡ ሊለውጥ፡ለብ
ዙ፡ ቤዛ።

፵፮፡ ወደ፡ ዬሪኮም፡ መጡ። ከዬሪኮም፡ በወጡ፡
ጊዜ፡ እርሱ፡ ደቀ፡ መዛሙርቱም፡ እጅግም፡ ሰዎች።
ዕውሩ፡ በርጢሚዎስ፡ የጢሚዎስ፡ ልጅ፡ በመንገድ፡
ላይ፡ ይቀመጥ፡ ነበረ፡ ሊለምን።

ማቴ፡ ፳፡ ፳፱፡—፴፬፡፡ ሉቃ፡ ፲፰፡ ፴፭፡—፵፫፡፡

፵፯፡ በሰማም፡ ጊዜ፡ የሱስ፡ የናዝሬቱ፡ እንደ፡ መ
ጣ፡ ይጮህ፡ ይልም፡ ጀመረ። የሱስ፡ ሆይ፡ የዳዊት፡
ልጅ፡ ማረኝ።

፵፰፡ ብዙ፡ ሰዎችም፡ ተቈጡት፡ ዝም፡ ይል፡ ዘን
ድ። እርሱ፡ግን፡ደግሞ፡ጩኸቱን፡ያበዛ፡ነበር፡ኢያለ።
የዳዊት፡ ልጅ፡ ሆይ፡ ማረኝ።

፵፱፡ የሱስም፡ ቆመና፡ ጽሩት፡ አለ። ዕውሩንም፡
ጸሩት፡ እንደይህ፡ ሲሉ። በርታ፡ ተነሣ፡ ይጸራሃልና።

፶፡ እርሱም፡ ልብሱን፡ አወጣ፡ ወደ፡ የሱስም፡
መጣ።

፶፩፡ የሱስም፡ መለሰ፡ እንደይህም፡ አለው። ምን፡
ትሻለህ፡ አደርግልህ፡ ዘንድ። ዕውሩም፡ አለው። መ
ምህር፡ ሆይ፡ ኢይ፡ ዘንድ።

፶፪፡ የሱስም፡ አለው። ሒድ። ሃይማኖትህ፡ አደነ
ህ። የዚያን፡ጊዜውም፡አየ፡የሱስንም፡በመንገድ፡ ተ
ከተለው።

## ምዕራፍ፡ ፲፩፡

፩፡ ወደ፡ የሩሳሌም፡ በቀረቡ፡ ጊዜ፡ ወደ፡ ፋጌቤ
ት፡ ወደ፡ቢታንያ፡ ወደ፡ደብረ፡ዘይቱ፡አጠገብ፡ሁለት፡
ከደቀ፡ መዛሙርቱ፡ ላከ፡ አላቸውም።

ማቴ፡ ፳፩፡ ፩፡—፱፡፡ ሉቃ፡ ፲፱፡ ፳፱፡—፴፰፡፡
ዮሐ፡ ፲፪፡ ፲፪፡—፲፯፡፡

፪፡ በፊታችሁ፡ ወደላች፡ አገር፡ ሒዱ። ወደርሷ
ም፡ በገባችሁ፡ ጊዜ፡ ያህያ፡ ግልገል፡ ታገኛላችሁ፡ ከሰ
ው፡ ማንም፡ ያልተቀመጠው። ፈቱትና፡ አምጡት።
፫፡ ማንም፡ ቢላችሁ፡ ለምን፡ እንደይህ፡ ታደርጋላች
ሁ። በሉ፡ ጌታ፡ ይሻዋል። የዚያን፡ ጊዜውም፡ ወደዚ
ህ፡ ይሰደዋል። ም፡ ፲፬፡ ፲፬፡፡

፬፡ እርሳቸውም፡ ሔዱ፡ ግልገሉንም፡ በደጁ፡ አጠ
ገብ፡ ታሥሮ፡ አገኙት፡ በሚደ፡ በሁለት፡ መንገድ፡ መ
ካከል። ፈቱትም።

፭፡ ከቆሙትም፡ሰዎች፡ አልዋቸው። ምን፡ ታደር
ጋላችሁ፡ አህያውን፡ የምትፈቱ።

፮፡ እርሳቸውም፡ አልዋቸው፡ የሱስ፡ እንደዘዘ።
ተውዋቸውም።

፯፡ ወደ፡ የሱስም፡ መጡ፡ግልገሉን፡ ይዘው፡ ልብሳ
ቸውንም፡ ጫኑበት፡ በላዩም፡ ተቀመጠ።

፰፡ የሚበልጡትም፡ ልብሳቸውን፡ በመንገድ፡ አነ
ጸፉ። ሌሎችም፡ የዛፋን፡ ጫፍ፡ ጫፋን፡ ቈረጡ፡ በ
መንገድም፡ አነጸፉ።

፱፡ በፊቱም፡ ይሔዱ፡ የነበሩ፡ በኋላውም፡ እንደ
ህ፡ ሲሉ፡ጮኹ። ሆሳዕና፡ በላይ። በእግዚአብሔር፡ ስ
ም፡ የሚመጣ፡ የተባረከ፡ ነው።

መዝ፡ ፻፲፰፡ ፳፭፡ ፳፮፡፡

፲፡ በእግዚአብሔር፡ ስም፡ የምትመጣ፡ ያባታችን፡
የዳዊት፡ መንግሥት፡ የተባረከች፡ ናት። ሆሳዕና፡ በአ
ርያም።

፲፩፡ የሱስም፡ ወደ፡ የሩሳሌም፡ ገባ፡ ወደ፡ መቅደ
ስም፡ ሁሉንም፡ በዙርያው፡ ተመለከተ። በመሸም፡
ጊዜ፡ ወደ፡ ቢታንያ፡ ወጣ፡ ካሥራ፡ ሁለቱ፡ ጋራ።

ማቴ፡ ፳፩፡ ፲፪፡—፳፪፡፡ ሉቃ፡ ፲፱፡ ፵፭፡—፵፰፡፡

፲፪፡ በነገውም፡ ከቢታንያ፡ በወጡ፡ ጊዜ፡ ተራበ።
፲፫፡ በለስም፡ ከሩቅ፡ አየ፡ ቅጠል፡ የነበረባት። መ
ጣም፡ ምናልባት፡ አንዳች፡ ያገኝባት፡ እንደ፡ ሆን። ወ
ደርስዋም፡ በመጣ፡ ጊዜ፡ አንዳች፡ አላገኘባትም፡ ከ
ቅጠል፡ በቀር። የበለስ፡ ወራት፡ አልደረሰም፡ ነበርና።

፲፬፤ የሱስም፡ መለሰ፡ አላትም። ማንም፡ ካንቺ፡
ፍሬ፡ አይብላ፡ ለዘላለም። ደቀ፡ መዛሙርቱም፡
ሰሙ። ቊ፡ ፳፤

፲፭፤ ወደ፡ የሩሳሌምም፡ መጡ። የሱስም፡ ወደ፡
መቅደስ፡ ገባ፡ በመቅደስም፡ የሚሸጡትን፡ የሚገዙ
ትንም፡ ያወጣ፡ ጀመረ። የለዋጮችንም፡ ማዕድ፡ የር
ግብ፡ ሻጮችንም፡ ወንበር፡ ገለበጠ።

፲፮፤ ማንም፡ እቃ፡ ይዞ፡ ወደ፡ መቅደስ፡ ይገባ፡ ዘን
ድ፡ አልተወም።

፲፯፤ ያስተምርም፡ ነበረ፡ እንዲህ፡ ሲል። የተጻፈ፡
አይደለምን። *ቤቴ፡ የጸሎት፡ ቤት፡ ይባላል፡ ለአሕዛ
ብ፡ ሁሉ። እላንተ፡ ግን፡ †የሌቦች፡ ዋሻ፡ አደረጋችሁት።
*ኢሳ፡ ፶፮፡ ፯። †ኤር፡ ፯፡ ፲፩።

፲፰፤ ጻፎችም፡ የካህናት፡ አለቆችም፡ ሰሙ፡ እን
ዲትም፡ ያጠፉት፡ ዘንድ፡ ፈለጉ። ይፈሩት፡ ነበሩና፡ ሰ
ው፡ ሁሉ፡ ያደንቅ፡ ነበርና፡ ከትምርቱ፡ የተነሣ።

፲፱፤ በመሸም፡ ጊዜ፡ ካገር፡ ወደ፡ ሜዳ፡ ወጣ።

፳፤ በነገውም፡ ሲያልፉ፡ በለሲቱን፡ ከስርዋ፡ ደርቃ፡
አዩ። ቊ፡ ፲፬።

፳፩፤ ጴጥሮስም፡ አሰበና፡ አለው። መምህር፡ ሆይ፡
እነሆች፡ የረገምሃት፡ በለስ፡ ደረቀች። ዕብ፡ ፮፡ ፳።

፳፪፤ የሱስም፡ መለሰ፡ አላቸውም። በእግዚአብ
ሔር፡ ሃይማኖት፡ ይሁንላችሁ። ዮሐ፡ ፲፬፡ ፩።

፳፫፤ እውነት፡ እላችኋለሁና። *ይህነን፡ ተራራ፡ ተነ
ቅለህ፡ ወደ፡ ባሕርም፡ ውደቅ፡ ያለው፡ በልቡም፡ የማ
ይጠራጠር፡ እንዲደረግለት፡ ግን፡ የሚያምን፡ ያለ
ው፡ ሁሉ፡ ይሆንለታል። *ማቴ፡ ፲፯፡ ፳።

፳፬፤ ስለዚህ፡ እላችኋለሁ። በጸሎት፡ የምትለም
ኑትን፡ *ሁሉ፡ እመኑ፡ እንድታገኙት፡ ይሆንላችኋል
ም። *ማቴ፡ ፯፡ ፯። ዮሐ፡ ፲፬፡ ፲፫።

፳፭፤ ለጸሎትም፡ በተነሣችሁ፡ ጊዜ፡ ይቅር፡ በሉ፡
በማንም፡ ላይ፡ አንዳች፡ እንዳላችሁ። የሰማዩ፡ አባ
ታችሁ፡ ደግሞ፡ ኃጢአታችሁን፡ ይቅር፡ እንዲላችሁ።
ማቴ፡ ፭፡ ፳፫።

፳፮፤ እላንተ፡ ግን፡ *ይቅር፡ ባትሉ፡ አባታችሁ፡ በሰ
ማይ፡ ያለው፡ ኃጢአታችሁን፡ ይቅር፡ አይላችሁም።
*ማቴ፡ ፮፡ ፲፬፡ ፲፭።

፳፯፤ ወደ፡ የሩሳሌም፡ ደግሞ፡ መጡ። እርሱም፡
በመቅደስ፡ ሲመላለስ፡ የካህናት፡ አለቆች፡ ጻፎችም፡
ሽማግሎችም፡ ወደርሱ፡ መጡ።
ማቴ፡ ፳፩፡ ፳፫፡—፳፯። ሉቃ፡ ፳፡ ፩፡—፰።

፳፰፤ አሉትም። ይህነን፡ በምን፡ ስልጣን፡ ታደርጋለ
ህ። ማንስ፡ ይህነን፡ ስልጣን፡ ሰጠህ፡ ይህን፡ ታደርግ፡
ዘንድ።

፳፱፤ የሱስም፡ መለሰ፡ አላቸውም። እኔም፡ ደግሞ፡
አንድ፡ ነገር፡ እጠይቃችኋለሁ። መልሱልኝም፡ እኔም፡
እላችኋለሁ፡ በምን፡ ስልጣን፡ ይህነን፡ እንደደርግ።

፴፤ የዮሐንስ፡ ጥምቀት፡ ከሰማይን፡ ነበረች፡ ወይ
ስ፡ ከሰው። መልሱልኝ።

፴፩፤ በልባቸውም፡ አሰቡ፡ እንዲህ፡ ሲሉ። ከሰማ
ይ፡ ብንል፡ ምነው፡ አላመናችሁትም፡ ይላል።

፴፪፤ ደግመንም፡ ከሰው፡ ብንል፡ ሕዝቡን፡ እንፈ
ራለን። ሁሉ፡ ዮሐንስን፡ ያዩት፡ ነበሩና፡ በውነት፡ ነቢ
ይ፡ እንደ፡ ነበረ።

፴፫፤ መለሱም፡ የሱስንም፡ አሉት። አናውቅም።
የሱስም፡ መለሰ፡ አላቸውም። እኔም፡ አልነግራችሁ፡
በምን፡ ስልጣን፡ ይህን፡ እንደደርግ።

ምዕራፍ፡ ፲፪፤

፩፤ በምሳሌም፡ ይላቸው፡ ጀመረ። ሰው፡ *ወይን፡
ተከለ፡ ቅጥርም፡ አዞረበት፡ መጥመቂያም፡ ማስለት፡
ግምብም፡ ሰራበት፡ ለጠባቆችም፡ ሰጠና፡ ወደ፡ ሌላ፡
አገር፡ ሔደ። *ኢሳ፡ ፭። ማቴ፡ ፳፩፡ ፴፫፡—፵፮።
ሉቃ፡ ፳፡ ፱፡—፲፱።

፪፤ በጊዜውም፡ ባርያውን፡ ወደ፡ ጠባቆች፡ ሰደደ፡
ከጠባቆች፡ የወይኑን፡ ፍሬ፡ ይወስድ፡ ዘንድ።

፫፤ እርሳቸውን፡ ግን፡ ያዙት፡ መቱትም፡ ባዶውን
ም፡ ሰደዱት።

፬፤ ደግሞም፡ ሌላውን፡ ባርያውን፡ ወደርሳቸው፡
ላከ። እርሱንም፡ ወገሩት፡ ደበደቡትም፡ ንቀውም፡
መለሱት።

፭፤ ደግሞም፡ ሌላውን፡ ላከ። እርሱንም፡ ገደሉት።
ደግሞም፡ ብዙ፡ ባሮች፡ ሌሎችን፡ ሰደደ። እኩሌታው
ንም፡ ገደሉ።

፮፤ አንድ፡ ልጅም፡ ነበረው፡ የሚወደው፡ እርሱን
ም፡ ወደርሳቸው፡ ሰደደው፡ ከሁሉ፡ በኋላ፡ እንዲህ፡
ሲል። እስኪ፡ ልጄን፡ ያፍሩት፡ እንደሆን።

፯፤ አሊያ፡ ግን፡ ጠባቆች፡ በልባቸው፡ አሉ። የሚወ
ርሰው፡ ይህ፡ ነው። ኑ፡ እንግደለው፡ ርስቱም፡ ለኛ፡ ይ
ሆናል።

፰፤ ወስደውም፡ ገደሉት፡ ከወይኑም፡ ወደ፡ *ሜዳ፡
አወጡት። *ዕብ፡ ፲፫፡ ፲፪።

፱፤ እንግዲህ፡ የወይኑ፡ ባለ፡ ቤት፡ ምን፡ ያደርጋል።
ይመጣል፡ ጠባቆችንም፡ ያጠፋል፡ ወይኑንም፡ ለሌሎ
ች፡ ይሰጣል።

፲፤ ይህነንም፡ መጽሐፍ፡ አላነበባችሁምን። አናጸ
ች፡ የናቁት፡ ደንጊያ፡ ይህ፡ የማዝን፡ ራስ፡ ሆነ።
መዝ፡ ፻፲፰፡ ፳፪፡ ፳፫።

፲፩፤ ይህች፡ ከእግዚአብሔር፡ ዘንድ፡ ሆነች። እርስ
ዋ፡ ባይናችን፡ ድንቅ፡ ናት።

፲፪፤ ሊይዙትም፡ ፈለጉ፡ ሰዎችንም፡ ፈሩ፡ ይህነን፡
ምሳሌ፡ ስለርሳቸው፡ እንደ፡ ተናገረው፡ አውቀዋልና።
ትተውትም፡ ሔዱ።

፲፫፤ ከፈሪሳውያንና፡ ከሄሮድስም፡ ወገን፡ ሰዎች፡
ወደርሱ፡ ሰደዱ፡ በነገር፡ ሊያስቱት። ምዕ፡ ፫፡ ፮።
ማቴ፡ ፳፪፡ ፲፭፡—፳፪። ሉቃ፡ ፳፡ ፳፡—፳፯።

፲፬፤ መጡም፡ አሉትም። መምህር፡ ሆይ፡ አወቅነ፡
እውነተኛ፡ እንደ፡ ሆንህ፡ ማነንም፡ አታፍርም። የሰ

ው፡ ፊት፡ አታደምና፡ነገር፡ ግን፡ በውነት፡ የእግዚአብሔርን፡ መንገድ፡ ታስተምራለህ። ይገባልን፡ ለቄሳር፡ ግብር፡ መስጠት፡ ወይስ፡ አይገባምን። እንስጥስ፡ ወይስ፡ አንስጥ።

፲፭፡ እርሱ፡ ግን፡ ግብዝነታቸውን፡አወቀ፡ አላቸውም። ለምን፡ ትፈትኑኛላችሁ። ወርቁን፡ አምጡልኝ፡ ልየው፡ ዘንድ።

፲፮፡ እርሳቸውም፡ አመጡለት። አላቸውም። ይህ፡ ጽፈት፡ መልኩስ፡ የማን፡ ነው። እርሳቸውም፡ አሉት፡ የቄሳር።

፲፯፡ የሱስም፡ መለሰ፡ አላቸውም። *የቄሳርን፡ ለቄሳር፡ ስጡ፡የእግዚአብሔርንም፡ለእግዚአብሔር። ከርሱም፡ ተደነቁ። *ሮሜ፡ ፲፫፡ ፯።

፲፰፡ ሰዱቃውያንም፡ መጡበት፡ትንሣኤ፡የለም፡ የሚሉ። እንደሁ፡ ሲሉም፡ ጠየቁት።

ማቴ፡ ፳፪፡ ፳፫—፴፫። ሉቃ፡ ፳፡ ፳፯—፵።

፲፱፡ መምህር፡ሆይ፡ *ሙሴ፡ ጻፈልነ። ላንድ፡ሰው፡ ወንድሙ፡ ሲሞት፡ሚስቱን፡ ትቶ፡ልጅም፡ አልወለደም። ወንድሙ፡ ሚስቱን፡ ይውሰድ፡ ለወንድሙም፡ ዘር፡ ያስነሣ። *ዘዳግ፡ ፳፭፡ ፭።

፳፡ ሰባት፡ወንድማማቾውም፡ነበሩ። መጀመርያውም፡ ሚስት፡ አገባ፡ ሞተም፡ ዘርም፡ አላስቀረም። ሁለተኛውም፡ ወሰዳት፡ ሞተም።

፳፩፡ እርሱም፡ ደግሞ፡ ዘር፡ አልተወም። ሦስተኛውም፡ እንዲሁ።

፳፪፡ ሰባቱም፡ አገቡዋት፡ ዘርም፡ አልተውም። ከሁሉ፡ በኋላ፡ ሴቲቱ፡ደግሞ፡ ሞተች።

፳፫፡ በትንሣኤም፡ በተነሡ፡ ጊዜ፡ ከርሳቸው፡ ለማን፡ ሚስት፡ ትሆናለች። ሰባቱ፡ ሚስት፡አድርገዋታልና።

፳፬፡ የሱስም፡ መለሰ፡ አላቸውም። ስለዚህ፡ የሳታችሁ፡ አይደላችሁምን። መጽሐፉ፡ አታውቁምና፡ የእግዚአብሔርንም፡ ኃይል።

፳፭፡ ከሙታን፡ በተነሡ፡ ጊዜ፡ አያገቡም፡ አያጋቡምና። በሰማይ፡ እንደሉ፡ መላእክት፡ ይሆናሉ፡ እንጂ።

፳፮፡ ስለ፡ ሙታን፡ ግን፡ እንዲነሡ፡ የሙሴን፡ መጽሐፉ፡ አላነበባችሁምን፡ እንዴት፡ተናገረው፡ እግዚአብሔር፡ በቍጥቋጦ፡ ውሥጥ፡እንዲህ፡ሲል። *እኔ፡ ነኝ፡ የአብርሃም፡ አምላክ፡ የይስሐቅም፡ አምላክ፡ የያዕቆብም፡ አምላክ። *ዘፀአ፡ ፫፡ ፪፡ ፮።

፳፯፡ እርሱ፡ የሙታን፡ አምላክ፡ አይደለም፡ የሕያዋን፡ አምላክ፡ እንጂ። እላንተ፡ ግን፡ እጅግ፡ ትስታላችሁ።

፳፰፡ ከጻፎችም፡ አንዱ፡ወደርሱ፡ መጣ፡ ሲከራከሩ፡ የሰማቸው፡ለርሳቸውም፡ የመለሱን፡ ማማር፡ አየ፡ ጠየቀውም፡እንዲህ፡ ሲል። ማናቸዪቱ፡ትእዛዝ፡ ከሁሉ፡ አስቀድማ፡ ናት። ማቴ፡ ፳፪፡ ፴፬—፵። ሉቃ፡ ፲፡ ፳፭—፳፰።

፳፱፡ የሱስ፡ ግን፡ መለሰለት፡ አለውም። የትእዛዝ፡ ሁሉ፡ መጀመርያ፡ ይህ፡ነው። *ስማ፡ እሥራኤል፡ ሆይ። እግዚአብሔር፡ አምላካችን፡ አንድ፡ እግዚአብሔር፡ ነው። *ዘዳግ፡ ፮፡ ፬፡ ፭።

፴፡ አንተም፡ እግዚአብሔርን፡ አምላክህን፡ ውደድ፡ በልብህ፡ ሁሉ፡ በነፍስህም፡ ሁሉ፡ በአሳብህም፡ ሁሉ፡ በኃይልህም፡ ሁሉ። ይህች፡ መጀመርያዪቱ፡ ትእዛዝ፡ናት።

፴፩፡ ሁለተኛዪቱም፡ እንደርስዋ፡ ያለች፡ ይህች፡ ናት። *ባልንጀራህን፡ውደድ፡ እንደራስህ። ሌላ፡ ትእዛዝ፡ የለም፡ ከለዚህ፡ የሚበልጥ። *ዘፀአ፡ ፲፱፡ ፲፰።

፴፪፡ ጻፊውም፡ አለው። መልካም፡ ተናገርህ፡ መምህር፡ ሆይ፡ በውነት፡ እግዚአብሔር፡ አንድ፡ ነውና፡ ከርሱ፡ በቀርም፡ ሌላ፡ የለም።

፴፫፡ እርሱንም፡ ትወደው፡ዘንድ፡በፍጹም፡ ልብ፡ በፍጽም፡ አሳብም፡ በፍጹም፡ነፍስም፡ በፍጹም፡ ኃይልም። ባልንጀራህንም፡ እንደ፡ ራስህ፡ ብትወድ፡ ይህ፡ ከቍርባን፡ ከመሥዋዕትም፡ ሁሉ፡ ይሻላል። ፩፡ ሳሙ፡ ፲፭፡ ፳፪።

፴፬፡ የሱስም፡ባየ፡ጊዜ፡በአእምሮ፡ እንደ፡መለሰ፡ አለው። *አንተ፡ከእግዚአብሔር፡መንግሥት፡የራቅህ፡ አይደለኽም። ማንም፡ ደግሞ፡ ይጠይቀው፡ ዘንድ፡ አልደፈረም። *የሐዋ፡ ፳፮፡ ፳፯—፳፱።

፴፭፡ የሱስም፡ መለሰ፡ አለም፡ እርሱም፡ በመቅደስ፡ ሲያስተምር። እንዴት፡ይላሉ፡ጻፎች፡ክርስቶስ፡ የዳዊት፡ ልጅ፡ እንደሆነ። ማቴ፡ ፳፪፡ ፵፩—፵፭። ሉቃ፡ ፳፡ ፵፩—፵፬።

፴፮፡ እርሱ፡ ዳዊት፡ በመንፈስ፡ቅዱስ፡ብልዋልና። *ጌታ፡ ጌታዬን፡ በቀኜ፡ ተቀመጥ፡ አለው። ጻላቶችህን፡ ለእግርህ፡ ድኳ፡ እስካደርግልህ፡ ድረስ። *መዝ፡ ፻፲፡ ፩።

፴፯፡ እርሱ፡ ዳዊት፡ ጌታ፡ ይለዋል። እንዴትም፡ እርሱ፡ ልጁ፡ ነው። ከሕዝቡም፡ እጅግ፡ ሰዎች፡ ደስ፡ ብልዋቸው፡ ይሰሙት፡ ነበሩ።

፴፰፡ ሲያስተምራቸውም፡ ይላቸው፡ ነበረ። ከጻፎች፡ ተጠበቁ፡መርቃን፡ሰላምም፡ኢየስጡ፡ በገቢያ፡ መሔድ፡ የሚወዱ፡ በረጅጅም፡ ልብስ። ማቴ፡ ፳፫፡ ፩—፴፬። ሉቃ፡ ፳፡ ፵፭—፵፯።

፴፱፡ በጉባዔም፡ በፊት፡ መቀመጥ፡ የሚወዱ፡ በሙብልም፡ ጊዜ፡ የማዕድ፡ ራስ።

፵፡ የባልቴቶችን፡ ቤት፡የሚበሉ፡ ለምክንያትም፡ ጸሎታቸውን፡ የሚያስረዝሙ። እሌህ፡ የሚበልጥ፡ ፍርድ፡ ይወስዳሉ።

፵፩፡ የሱስም፡በመዝገብ፡*ሣፅኑ፡ፊት፡ተቀመጠ፡ ያይም፡ ነበረ፡ ሰዎች፡ ናስ፡በሣፅኑ፡ እንዴት፡ እንደጣሉ። እጅግም፡ ባለጠጎች፡ እጅግ፡ ይጥሉ፡ ነበሩ። *፪፡ ነገሥ፡ ፲፪፡ ፱። ሉቃ፡ ፳፩፡ ፩—፬።

፵፪፡ ድኃ፡ ቤትም፡ ባልቴት፡ መጣች፡ ሁለት፡ ጀጀድም፡ ጣለች፡ ድሪም፡ የሚያህሉ። ሉቃ፡ ፲፪፡ ፶፪።

፵፫፤ ደቀ፡ መዛሙርቱንም፡ ጸራቸው፡ አላቸውም። እውነት፡ እላችኋለሁ፡ ይህች፡ ድኻ፡ ባልቴት፡ አብልጣ፡ እንደ፡ ጣለች፡ በሣፅን፡ ከጣሉት፡ ሁሉ።

፵፬፤ ሁሉ፡ ከኩብታቸው፡ የተረፈውን፡ ጣልዋልና። ይህች፡ ግን፡ ከድኻነትዋ፡ ያላትን፡ ሁሉ፡ ራትዋን፡ ሁሉ፡ ጣለች። ፪፤ ቆሮ፡ ፰፤ ፲፪፤

## ምዕራፍ፡ ፲፫፤

፩፤ እርሱም፡ ከመቅደስ፡ ሲወጣ፡ ከደቀ፡ መዛሙርቱ፡ አንዱ፡ አለው። መምህር፡ ሆይ፡ የዚህን፡ የታላቁን፡ ደንጊያ፡ መጠን፡ እይ፡ የዚህንም፡ ስራ፡ መጠን። ሉቃ፡ ፳፩፤ ፭፤

፪፤ የሱስም፡ መለሰ፡ አለውም። ይህነን፡ ታላቅ፡ ስራ፡ ታያለህን። ደንጊያ፡ በደንጊያ፡ ላይ፡ አይቀርም፡ ይፈርሳል፡ እንጂ።

፫፤ እርሱም፡ በደብረ፡ ዘይት፡ ተቀምጦ፡ ሳለ፡ በመቅደስ፡ ፊት፡ ጴጥሮስ፡ ያዕቆብም፡ ዮሐንስም፡ እንድርያስም፡ በሡውር፡ ጠየቁት፡ እንዲህ፡ ብለው።

፬፤ ንገረነ፡ መች፡ ይሆናል፡ ይህ፡ ነገር። ምልክቱስ፡ ምን፡ ይሆናል፡ ይህ፡ ሁሉ፡ እንዲፈጸም።

፭፤ የሱስም፡ መለሰላቸው፡ ይልም፡ ጀመረ። እወቁ፡ ማንም፡ አያስታችሁ።

፮፤ ብዙ፡ በስሜ፡ ይመጣሉና፡ እንደሁ፡ ሲሉ። እኔ፡ ክርስቶስ፡ ነኝ። ብዙውንም፡ ያስታሉ።

፯፤ ሰልፈንና፡ የሰልፈንም፡ ወሬ፡ በሰማችሁ፡ ጊዜ፡ አትደንግጡ። ይሆን፡ ዘንድ፡ ይገባልና። ነገር፡ ግን፡ ፍጻሜ፡ ገና፡ አይሆንም።

፰፤ ሕዝብ፡ በሕዝብ፡ ላይ፡ ይነሣልና፡ መንግሥትም፡ በመንግሥት፡ ላይ። በያገሩም፡ መናወጥ፡ ይሆናል። ራብም፡ ሁከትም፡ ይሆናል።

፱፤ ይህም፡ የምጥ፡ ጻር፡ መጀመርያ፡ ነው። እላንተ፡ ግን፡ ለራሳችሁ፡ ተጠበቁ። ወደ፡ ሸንጎ፡ ወደ፡ ጉባኤም፡ አሳልፈው፡ ይሰጥዋችኋልና፡ ትመቱማላችሁ። በነገሥታትም፡ በመኳንንትም፡ ፊት፡ ትቆማላችሁ፡ ስለ እኔ፡ ምስክር፡ ሊሆንባቸው። ማቴ፡ ፲፤ ፲፯፤—፳፪፤

፲፤ ለአሕዛብም፡ ሁሉ፡ አስቀድሞ፡ ወንጌል፡ ይሰበክ፡ ዘንድ፡ ይገባል። ም፡ ፲፯፤ ፲፭፤

፲፩፤ በወሰድዋችሁም፡ ጊዜ፡ አሳልፈውም፡ በሰጥዋችሁ፡ ጊዜ፡ በምትናገሩት፡ አታስቡ። አስቀድማችሁም፡ ምን፡ እንመልሳለን፡ አትበሉ። የዚያን፡ ጊዜ፡ የሚሰጣችሁን፡ ትናገራላችሁ፡ እንጂ። እላንተ፡ የምትናገሩ፡ አይደላችሁምና፡ ነገር፡ ግን፡ መንፈስ፡ ቅዱስ።

፲፪፤ ወንድም፡ ወንድሙን፡ ለሞት፡ አሳልፎ፡ ይሰጣል፡ አባትም፡ ልጁን። ልጆችም፡ ባባቶቻቸው፡ ላይ፡ ይነሣሉ፡ ይገድልዋቸዋልም።

፲፫፤ በሁሉም፡ የተጸላችሁ፡ ትሆናላችሁ፡ ስለ፡ ስሜ። እስከ፡ ፍጻሜ፡ የሚታገሥ፡ ግን፡ እርሱ፡ ይድናል።

፲፬፤ የመፍረሱንም፡ *ርኵሰት፡ ባያችሁ፡ ጊዜ፡ በነቢዩ፡ በዳንኤል፡ የተባለችውን፡ ወደማይገባው፡ ቆሞ። አንባቢውም፡ ያስተውል። የዚያን፡ ጊዜ፡ በይሁዳ፡ ያሉ፡ ወደ፡ ተራራ፡ ይሽሹ። *ዳን፡ ፱፤ ፳፯፤ ፲፪፤ ፲፩፤

፲፭፤ በሰገነትም፡ ያለ፡ ወደ፡ ቤት፡ አይውረድ፡ አይግባም፡ ከቤቱ፡ አንዳች፡ ይወስድ፡ ዘንድ።

፲፮፤ ወደ፡ እርሻም፡ ያለ፡ ወደ፡ ኋላው፡ አይመለስ፡ ልብሱን፡ ይወስድ፡ ዘንድ።

፲፯፤ ወዮላቸው፡ ግን፡ ለርጉዞች፡ ለሚያጠቡም፡ በዚያች፡ ወራት።

፲፰፤ ጸልዩም፡ መሸሻችሁ፡ በክረምት፡ እንዳይሆን።

፲፱፤ በዚያ፡ ወራት፡ መከራ፡ *ይሆናልና፡ እግዚአብሔር፡ ከፈጠረው፡ ፍጥረት፡ ጀምሮ፡ እስከ፡ ዛሬ፡ እንደርሱ፡ ያልሆነ፡ ደግሞም፡ አይሆንም። *ዳን፡ ፲፪፤ ፩፤

፳፤ እግዚአብሔርስ፡ ያችን፡ ወራት፡ ባያሳጥራት፡ ሥጋ፡ የለበሰ፡ ሁሉ፡ ባልዳነም። ነገር፡ ግን፡ ስለ፡ ተመረጡት፡ ያችን፡ ወራት፡ ያሳጥራል።

፳፩፤ የዚያን፡ ጊዜ፡ ማንም፡ ቢላችሁ። እነሆ፡ ክርስቶስ፡ ከዚህ፡ ነው፡ ወይም፡ ከዚያ፡ ነው፡ አትመኑ።

፳፪፤ አስተኞች፡ መሢሖች፡ ይነሣሉና፡ አስተኞችም፡ ነቢያት፡ ታምራትም፡ ምልክትም፡ ይሰጣሉ፡ የተመረጡትን፡ ደግሞ፡ ያስቱ፡ ዘንድ፡ ቢቻላቸው።

፳፫፤ እላንተ፡ ግን፡ እወቁ። እነሆ፡ ነገሬን፡ ሁሉ፡ አስቀድሜ፡ ነገርኋችሁ።

፳፬፤ ነገር፡ ግን፡ በዚያች፡ ወራት፡ ከዚያ፡ መከራ፡ በኋላ፡ ፀሐዩ፡ ትጨልማለች፡ ጨረቃም፡ ብርሃኑን፡ አይሰጥም።

፳፭፤ የሰማይም፡ ከዋክብት፡ ይወድቃሉ። በሰማይም፡ ያሉ፡ ኃይላት፡ ይናወጣሉ።

፳፮፤ የዚያን፡ ጊዜም፡ የሰው፡ ልጅ፡ በደመና፡ ሲመጣ፡ ያያሉ፡ ከብዙ፡ ኃይል፡ ከምስጋናም፡ ጋራ።

፳፯፤ የዚያን፡ ጊዜም፡ *መልክተኞቹን፡ ይሰዳል፡ የተመረጡትንም፡ ካራቱ፡ ነፋሳት፡ ይሰበስባል፡ ከምድር፡ ዳር፡ እስከ፡ ሰማይ፡ ዳርቻ። ማቴ፡ ፲፫፤ ፵፩፤

፳፰፤ ምሳሌውንም፡ *ከበለስ፡ እወቁ። ጫፍዋ፡ በለመለመ፡ ጊዜ፡ ቅጠልዋም፡ በወጣ፡ ጊዜ፡ በጋ፡ እንደ፡ ቀረበ፡ እወቃችሁ። *ማቴ፡ ፳፬፤ ፴፪፤

፳፱፤ እንደዚሁ፡ እላንተም፡ ደግሞ፡ ይህቺን፡ እንደ፡ ሆነች፡ ባያችሁ፡ ጊዜ፡ እወቁ፡ እንደ፡ ቀረበ፡ በደጅ፡ ላይ።

፴፤ እውነት፡ እላችኋለሁ። ይህ፡ ትውልድ፡ እንዳያልፍ፡ ይህች፡ ሁሉ፡ እስክትሆን፡ ድረስ።

፴፩፤ ሰማይና፡ ምድር፡ ያልፋሉ፡ ቃሌ፡ ግን፡ አያልፍም።

፴፪፤ ያነን፡ ቀን፡ ግን፡ ያችንም፡ ሰዓት፡ ማንም፡ አያውቅም። በሰማይም፡ የሚኖሩ፡ መላእክት፡ ልጅም፡ ከአብ፡ በቀር።

፴፫፤ ተጠበቁ፡ ትጉ፡ ጸልዩም። የሚሆንበቱን፡ ጊዜ፡ አታውቁምና።

፴፬፡ የሰው፡ ልጅ፡ *ቤቱን፡ ትቶ፡ ወደ፡ እንግደ፡ አገር፡ እንደ፡ ሔደ፡ ሰው፡ ነውና። ለባሮቹም፡ ስልጣን፡ ሰጣቸው፡ ለያንዳንዱም፡ ተግባሩን። በረኛውንም፡ እንዲተጋ፡ አዘዘው። *ማቴ፡ ፳፭፡ ፲፬፡፡ ሉቃ፡ ፲፱፡ ፲፪፡፡

፴፭፡ አሁንም፡ ትጉ፡ አታውቁምና፡ ባለ፡ ቤቱ፡ መቸ፡ እንዲመጣ። በማታን፡ ወይስ፡ ደር፡ ሲጮህ፡ ወይስ፡ በማለዳ። ሉቃ፡ ፲፪፡ ፴፰፡፡

፴፮፡ ድንገት፡ መጥቶ፡ ተኝታችሁ፡ እንዳያገኛችሁ።

፴፯፡ ለላንተም፡ የምነግራችሁን፡ ለሁሉ፡ እላለሁ። ትጉ።

## ምዕራፍ፡ ፲፬፡

፩፡ በዓለ፡ ፋሲካ፡ በዓለ፡ ናእትም፡ ከሁለት፡ ቀን፡ በኋላ፡ ነበረ። የካህናት፡ አለቆችም፡ ጻፎችም፡ በተንኰል፡ እንዴት፡ ይዙት፡ ዘንድ፡ ይሹ፡ ነበር፡ ይግሉትም፡ ዘንድ። ማቴ፡ ፳፮፡ ፩፡—፭፡፡ ዮሐ፡ ፲፫፡፡

፪፡ ይሉም፡ ነበሩ። በበዓል፡ አይደለም፡ በሕዝብ፡ ሁከት፡ እንዳይሆን። ማቴ፡ ፳፮፡ ፮፡—፲፫፡፡ ዮሐ፡ ፲፪፡ ፩፡—፰፡፡

፫፡ እርሱም፡ በቢታንያ፡ ሳለ፡ በለምጻሙ፡ በሲሞን፡ ቤት፡ ለመብል፡ ተቀምጦ፡ ሴት፡ መጣች፡ የሸቱ፡ ብርሌ፡ ይዛ፡ ናርዶስ፡ የሚሉት፡ የተፈተነ፡ ዋጋውም፡ የበዛ። ብርሌውንም፡ ሰበረችና፡ በራሱ፡ ላይ፡ ገለበጠችው።

፬፡ በልባቸው፡ የተቆጡ፡ ሰዎች፡ ነበሩ፡ እንዲህም፡ ያሉ። ለምን፡ ይህ፡ ጥፋት፡ በዚህ፡ ሽቱ፡ ሆነ።

፭፡ ይህ፡ ከሦስት፡ መቶ፡ ድሪም፡ በሚበልጥ፡ ይሸጥ፡ ዘንድ፡ ይሆን፡ ነበርና፡ ለድኆችም፡ ይሰጥ፡ ዘንድ፡ ይሆን፡ ነበርና፡ ገሠፁዋትም።

፮፡ የሱስ፡ ግን፡ አለ። ተውዋት። ለምን፡ ታደክሙዋታላችሁ። መልካም፡ ማድረግ፡ አደረገችብኝ።

፯፡ *ድኆችስ፡ ከላንተ፡ ዘንድ፡ ሁለግዜ፡ ናቸው። ከወደዳችሁስ፡ ትመጸውቷቸው፡ ዘንድ፡ ትችላላችሁ። እኔ፡ ግን፡ ከላንተ፡ ዘንድ፡ ሁለግዜ፡ አይደለሁም። *ዘዳግ፡ ፲፭፡ ፲፩፡፡

፰፡ ያላትን፡ ፈጽማ፡ አደረገችው። ሥጋዬን፡ ለመቃብሬ፡ ትቀባው፡ ቀደመች።

፱፡ እውነት፡ እላችኋለሁ። ይህ፡ ወንጌል፡ ወደሚሰበክበት፡ ዘንድ፡ በዓለሙ፡ ሁሉ፡ ይህች፡ ያደረገችው፡ ደግሞ፡ ይነገራል፡ ለርስዋ፡ መታሰቢያ፡ ይሆን፡ ዘንድ።

፲፡ ይሁዳም፡ ያስቆሮቱ፡ ካሥራ፡ ሁለቱ፡ አንዱ፡ ወደ፡ ካህናት፡ አለቆች፡ ሔደ፡ አሳልፎ፡ ሊሰጣቸው። ማቴ፡ ፳፮፡ ፲፬፡—፲፮፡፡ ሉቃ፡ ፳፪፡ ፫፡—፮፡፡

፲፩፡ እርሳቸውም፡ በሰሙ፡ ጊዜ፡ ደስ፡ አላቸው፡ ተስፋም፡ አስደረጉት፡ ብር፡ ይሰጡት፡ ዘንድ፡ ጊዜም፡ ይሻ፡ ነበር፡ እንዴት፡ እንዲያሲዘው።

፲፪፡ በናእት፡ ቀንም፡ መጀመርያ፡ ፋሲካን፡ በሚያርዱበት፡ ጊዜ፡ ደቀ፡ መዛሙርቱ፡ አሉት። ወዴት፡ ሒደን፡ ትወዳላህ፡ እናሰናዳልህ፡ ዘንድ፡ ፋሲካን፡ እንድትበላ።

፲፫፡ ከደቀ፡ መዛሙርቱም፡ ሁለት፡ ሰደደ፡ አላቸውም። ወደ፡ ገር፡ ሒዱ፡ ሰውም፡ ያገኛችኋል፡ ማድጋ፡ ውኃ፡ ተሸክሞ። ተከተሉት።

፲፬፡ ወደ፡ ገባበቱም፡ ባለ፡ ቤቱን፡ በሉት። መምህር፡ ይላል። ወዴት፡ ነው፡ የዕረፍት፡ ስፍራ፡ ፋሲካን፡ የምበላበት፡ ከደቀ፡ መዛሙርቴ፡ ጋራ። ም፡ ፲፩፡ ፫፡፡

፲፭፡ እርሱም፡ ታላቅ፡ ቤተ፡ ንጉሥ፡ ያሳያችኋል፡ የተነጸፈች፡ የተዘጋጀች። ከዚያ፡ አሰናዱልን።

፲፮፡ ደቀ፡ መዛሙርቱም፡ ወጥተው፡ ወደ፡ ገር፡ መጡ። እንደላቸውም፡ አገኙ፡ ፋሲካንም፡ አዘጋጁ።

፲፯፡ በመሸም፡ ጊዜ፡ መጣ፡ ካሥራ፡ ሁለቱ፡ ጋራ።

፲፰፡ እርሳቸውም፡ ተቀምጠው፡ ሲበሉ፡ የሱስ፡ አለ። እውነት፡ እላችኋለሁ። ከላንተ፡ አንዱ፡ ከኔ፡ ጋራ፡ የሚበላ፡ አሳልፎ፡ ይሰጠኛል።

፲፱፡ እርሳቸውም፡ ያዝኑ፡ ጀመሩ፡ ይሉትም፡ ኢያንዳንዱ። አንዳች፡ እኔ፡ እሆን። ሌላውም፡ አለ፡ እኔን፡ እሆን። ዮሐ፡ ፲፫፡ ፳፩፡—፳፮፡፡

፳፡ እርሱም፡ መለሰ፡ አላቸውም። አንዱ፡ ካሥራ፡ ሁለቱ፡ እጁን፡ ከኔ፡ ጋራ፡ በገበታ፡ የሚጠልቅ።

፳፩፡ የሰው፡ ልጅ፡ ግን፡ ይሔዳል፡ ስለርሱ፡ እንደ፡ ተጻፈ። ነገር፡ ግን፡ ወዮለት፡ ለዚያ፡ ሰው፡ በጁ፡ የሰው፡ ልጅ፡ የሚሰጥ። ይሻለው፡ ነበረ፡ ባይወለድ፡ ያሰው።

፳፪፡ እርሳቸውም፡ ሲበሉ፡ የሱስ፡ እንጀራ፡ ወሰደ፡ ባረከውም፡ ቈረሰውም፡ ሰጣቸውም፡ አለም። እንኩ፡ ብሉ። ይህ፡ ሥጋዬ፡ ነው። ፩፡ ቆሮ፡ ፲፩፡ ፳፫፡—፳፮፡፡

፳፫፡ ጽዋም፡ ወሰደ፡ አመሰገነም፡ ሰጣቸውም። ሁሉም፡ ከርሱ፡ ጠጡ።

፳፬፡ አላቸውም። ይህ፡ ደሜ፡ ነው፡ ላዲስ፡ ሥርዓት፡ ስለ፡ ብዙ፡ የሚፈስ።

፳፭፡ እውነት፡ እላችኋለሁ። ከወይኑ፡ ጥማቂ፡ እንዳልጠጣ፡ ከዚህ፡ በኋላ፡ እስከዚያ፡ ቀን፡ ድረስ፡ አዲሱን፡ በምጠጣበት፡ ጊዜ፡ በእግዚአብሔር፡ መንግሥት።

፳፮፡ *አመስግነውም፡ ወደ፡ ደብረ፡ ዘይት፡ ወጡ። *መዝ፡ ፻፲፫፡—፻፲፰፡፡

፳፯፡ የሱስም፡ አላቸው። ሁላችሁ፡ ትክዱኛላችሁ፡ በዚች፡ ሌሊት። *ተጽፏልና። ጠባቂውን፡ እገድላለሁ፡ በጎችም፡ ይበተናሉ። *ዘካ፡ ፲፫፡ ፯፡፡

፳፰፡ ነገር፡ ግን፡ *ከተነሣሁ፡ በኋላ፡ ወደ፡ ገሊላ፡ እቀድማችኋለሁ። *ም፡ ፲፮፡ ፯፡፡

፳፱፡ ጴጥሮስም፡ አለው። ሁሉም፡ ቢክዱ፡ እኔ፡ አልክድም።

፴፡ የሱስም፡ አለው። እውነት፡ እልሃለሁ። ዛሬ፡ በዚች፡ ሌሊት፡ ደሮ፡ ሁለት፡ ጊዜ፡ ሳይጮህ፡ ሶስት፡ ጊዜ፡ ትክደኛለህ። *ዮሐ፡ ፲፫፡ ፴፰፡፡

፴፩፡ እርሱ፡ ግን፡ ነገሩን፡ አበርትቶ፡ አለ። ካንተ፡ ጋራ፡ እሞት፡ ዘንድ፡ ስንኳ፡ ቢሆን፡ አልክድህም። ሁሉም፡ ደግሞ፡ እንዲህ፡ አሉ።

፴፪፡ ጌቴሴማኒም፡ ወደሚሉት፡ ስፍራ፡ ሔዱ፡ ደቀ፡ መዛሙርቱንም፡ አለ። ከዚህ፡ ተቀመጡ፡ እስክ ጸልይ፡ ድረስ።

፴፫፡ ጴጥሮስንም፡ ያዕቆብንም፡ ዮሐንስንም፡ ከርሱ፡ ጋራ፡ ይዞ፡ ሔደ። ይንቀጠቀጥም፡ ይጸጸርም፡ጀመረ።

፴፬፡ አላቸውም። ነፍሴ፡ አዝናለች፡እስከ፡ ሞት፡ ድረስ። ከዚህ፡ቈዩ፡ትጉም። ዮሐ፡ ፲፪፡ ፳፯።

፴፭፡ ጥቂትም፡ ፈቀቅ፡ አለ፡ በምድርም፡ ወደቀ፡ ጸለየም፡ ይቻል፡ እንደሆነስ፡ ጊዜዪቱ፡ ከርሱ፡ ታልፍ፡ ዘንድ።

፴፮፡ ይልም፡ ነበር። አባ፡ አባቴ፡ ሆይ፡ ሁሉ፡ ይቻልሃል። ይህችን፡ *ጽዋ፡ ከኔ፡ አሳልፋት። ነገር፡ ግን፡ እኔ፡ እንድወድ፡ አይደለም፡ አንተ፡ እንድትወድ፡እንጂ።
*ም፡ ፲፡ ፴፰።

፴፯፡ መጥቶም፡ ተኝተው፡ አገኛቸው። ጴጥሮስንም፡ አለው። ሲሞን፡ሆይ፡ አንተን፡ተኝትሃል። አልቻልህምን፡ ትተጋ፡ ዘንድ፡ አንዲት፡ ሰዓት፡ ስንኳ።

፴፰፡ ትጉ፡ጸልዩም፡ወደ፡ መከራ፡እንዳትገቡ። ነፍስ፡ የተዘጋጀ፡ ነው፡ ሥጋ፡ ግን፡ የደከመ፡ ነው።

፴፱፡ ደግሞም፡ ሔደ፡እርስዋንም፡ ያችን፡ጸሎት፡ ጸለየ።

፵፡ ደግሞ፡ ተመልሶም፡ ተኝተው፡ አገኛቸው። ዓይኖቻቸውም፡ ከብደው፡ ነበሩና። የሚመልሱለትንም፡ አያውቁም፡ ነበር።

፵፩፡ ሦስተኛም፡መጣ፡አላቸውም። እንግዲህስ፡ ተኙ፡ ዕረፉም። ይበቃል። ጊዜዪቱ፡ ደረሰች። እነሆ፡ የሰው፡ ልጅ፡ በኃጥኣን፡ እጅ፡ ይሰጣል።

፵፪፡ ተነሡ፡እንሒድ። እነሆ፡ደረሰ፡አሳልፎ፡የሚ ሰጠኝ።

፵፫፡ የዚያን፡ ጊዜም፡ይህነን፡ሲናገር፡ይሁዳ፡ ካሥራ፡ ሁለቱ፡ አንዱ፡ መጣ። ከርሱ፡ ጋራም፡ እጅግ፡ ስዎች፡ ሰይፍ፡ ጎመድም፡ ይዘው፡ ከካህናት፡ አለቆች፡ ከጻፎችም፡ ከሽማግሎችም። ዮሐ፡ ፲፰፡ ፪፡—፲፩።

፵፬፡ የሚያሲዘውም፡ ምልክት፡ ሰጥቶአቸው፡ ነበረ፡ እንዲህ፡ ሲል። የምስመው፡ እርሱ፡ ነው። ያዙት፡ ምናለብን፡ ብላችሁ፡ ውሰዱት።

፵፭፡ መጥቶም፡ የዚያን፡ ጊዜ፡ ወደርሱ፡ ቀረበ፡ አለም። መምህር፡ ሆይ፡ መምህር፡ ሆይ። ሳመውም።

፵፮፡ እርሳቸውም፡ እጃቸውን፡ ጣሉበት፡ ያዙትም።

፵፯፡ ከቆሙቱ፡አንዱም፡ሰይፍ፡መዘዘ፡የካህናቱን፡ አለቃ፡ባርያም፡ መታው፡ ጆሮውንም፡ ቈረጠው።

፵፰፡ የሱስም፡ መለሰ፡ አላቸውም። በሌባ፡ ላይ፡ እንድትወጡን፡ ወጣችሁ፡ ሰይፍና፡ጎመድ፡ይዛችሁ፡ ልትይዙኝ።

፵፱፡ ሁለግዜ፡ ከላንት፡ ጋራ፡ ነበርሁ፡ በመቅደስ፡ ሳስተምር፡ አልያዛችሁኝምም። ነገር፡ ግን፡ መጸሕፍት፡ ይፈጸሙ፡ ዘንድ፡ ነው።

፶፡ ሁሉም፡ ትተውት፡ ሸሹ።

፶፩፡ ጐበዝም፡ ይከተለው፡ ነበር፡ ነጸላ፡ የለበሰ። ጐበዛዝቱም፡ ያዙት።

፶፪፡ እርሱም፡ነጸላውን፡ትቶ፡ራቁቱን፡ከርሳቸው፡ አመለጠ።

፶፫፡ የሱስንም፡ ይዘው፡ ወደ፡ ካህናት፡ አለቃ፡ መጡ። የካህናትም፡ አለቆች፡ ሁሉ፡ ሽማግሎችም፡ ጻፎችም፡ ወደርሱ፡ ተሰበሰቡ።

፶፬፡ ጴጥሮስም፡ ከሩቅ፡ ይከተለው፡ ነበር፡ እስከ፡ ካህናቱ፡ አለቃ፡ ቤት፡ ውሥጥ፡ ድረስ፡ ከሎሌች፡ ጋራም፡ ተቀምጦ፡ ነበር፡ እሳትም፡ ይሞቅ፡ ነበር።

፶፭፡ የካህናት፡ አለቆች፡ ግን፡ ሸንጎም፡ ሁሉ፡ ምስክሮች፡ ይሹ፡ ነበሩ፡ የሱስን፡ ሊገሉት። አላገኙም።
ዮሐ፡ ፲፰፡ ፲፱፡—፳፬።

፶፮፡ ብዙ፡ በሐሰት፡ ይመስክሩበት፡ነበሩና፡ ምስክርነታቸውም፡ አልተስማማም።

፶፯፡ ሰዎችም፡ ተነሡ፡ባስትም፡ መሰከሩበት፡ እንዲህ፡ ሲሉ።

፶፰፡ እኛ፡ ሰማነው፡ሲል። እኔ፡ ይህነን፡ *መቅደስ፡ አፈርሳለሁ፡ እጅ፡ የሰራውን። በሦስተኛ፡ ቀንም፡ ሌላ፡ አሰነሣለሁ፡ በጅ፡ ያልተሰራ።
*ዮሐ፡ ፪፡ ፲፱፡—፳፩።

፶፱፡ እንዲሁም፡ደግሞ፡ምስክራቸው፡አልተሰማማቸም።

፷፡ የካህናትም፡አለቃ፡ በመካከል፡ ቆመ፡የሱስንም፡ ጠየቀ፡እንዲህ፡ሲል። አንዳች፡ አትመልስምን። እሌህ፡ ካንተ፡ ምን፡ ይመስክሩብሃል።

፷፩፡ እርሱ፡ ግን፡ *ዝም፡ ብሎ፡ ነበር፡ አንዳችም፡ አልመለሰም። ደግሞ፡ ጠየቀው፡ የካህናት፡ አለቃ፡ አለውም። አንተን፡ክርስቶስ፡ነህ፡የተባረከው፡ልጅ።
*ም፡ ፲፭፡ ፪። ኢሳ፡ ፶፫፡ ፯።

፷፪፡ የሱስም፡አለ፡እኔ፡ነኝ። ታዩማላችሁ፡የሰው፡ ልጅ፡ በኃይል፡ ቀኝ፡ ተቀምጦ፡ ከሰማይ፡ ደመናም፡ ጋራ፡ ሲመጣ።

፷፫፡ የካህናት፡ አለቃ፡ ግን፡ ልብሱን፡ ቀደደ፡ አለም። ደግሞ፡ ምስክሮችን፡ምን፡ ያሻልና።

፷፬፡ ስድቡን፡ ሰማችሁ። ምን፡ ይመስላችኋል። ሁሉም፡ ፈረዱበት፡ ሞት፡ እንዲገባው።
ዮሐ፡ ፲፱፡ ፯።

፷፭፡ ሰዎችም፡ ይተፉበት፡ ጀመሩ፡ ፊቱንም፡ ሸፍነው፡ ይጸፉት፡ ነበሩ፡ ይሉትም፡ ነበሩ፡ ትንቢት፡ ተናገር። ሎሌችም፡ ይጸፉት፡ ነበሩ።

፷፮፡ ጴጥሮስም፡ በታችኛው፡ቤት፡ ሳለ፡ከካህናት፡ አለቃ፡ ገረዶች፡ አንዲቱ፡ መጣች።
ዮሐ፡ ፲፰፡ ፲፭፡—፳፯።

፷፯፡ ጴጥሮስንም፡ እሳት፡ሊሞቅ፡ ተቀምጦ፡ ብታየው፡ አስተዋለችው፡ አለችም። አንተም፡ ደግመህ፡ ከናዝሬቱ፡ ከየሱስ፡ ጋራ፡ ነበርህ።

፷፰፡ እርሱ፡ግን፡ካደ፡እንደህ፡ሲል። አላውቅም፡

አንችም፡ የምትዪውን፡ አላስተውልም። ሚደም፡ ወጣ፡ ወደ፡ ቤት፡ ደጅ። ዶሮም፡ ጮኸ።

፷፱፤ ገረድም፡ደግማ፡አየችው፡ለቆሙቱም፡ትል፡ ጀመረች። ይህም፡ ከርሳቸው፡ ወገን፡ ነው።

፸፤ እርሱ፡ግን፡ደግሞ፡ካደ። ጥቂትም፡ቈይተው፡ የቆሙት፡ጴጥሮስን፡ደግሞ፡አሉት። አንተ፡ በውነት፡ ከርሳቸው፡ ወገን፡ ነህ። አንተም፡ ደግመህ፡ የገሊላ፡ ሰው፡ ነህና። ነገርህም፡ነገራቸውን፡ ይመስላል።

፸፩፤ እርሱ፡ግን፡ይረግም፡ ይምልም፡ ጀመረ። እኔ፡ ይህነን፡ሰው፡ የምትሉትን፡እንደላውቀው።

፸፪፤ ደግሞም፡ ሁለተኛ፡ ዶሮ፡ ጮኸ። ጴጥሮስም፡ የሱስ፡ *ያለው፡ ነገር፡ አሰበ። ዶሮ፡ ሁለትግዜ፡ሳይጮህ፡ ሶስትግዜ፡ እንድትክደኝ። ነገሩንም፡ ባሰበ፡ ጊዜ፡ አለቀሰ። *ቍ፡ ፴።

ምዕራፍ፡ ፲፭።

፩፤ የዚያን፡ ጊዜውን፡ ሲጸባም፡ የካህናት፡ አለቆች፡ከሽማግሎች፡ከጸፎችም፡ጋራ፡ተሰበሰቡ፡ሸንጎም፡ ሁሉ። የሱስንም፡ አሠሩት፡ ወሰዱትም፡ ለጲላጦስም፡ አሳልፈው፡ሰጡት። ማቴ፡ ፳፯። ሉቃ፡ ፳፫። ዮሐ፡ ፲፰።

፪፤ ጲላጦስም፡ ጠየቀው። አንተን፡ ነህ፡ የአይሁድ፡ንጉሥ። እርሱም፡መለሰ፡አለውም፡አንተ፡አልህ፡

፫፤ የካህናትም፡አለቆች፡እጅግ፡አጣሉት። እርሱ፡ ግን፡ አንዳች፡ አልመለሰም።

፬፤ ጲላጦስም፡ ደግሞ፡ ጠየቀው፡ እንዲህ፡ ሲል። አንዳች፡ አትመልስምን። እይ፡ ስንት፡ ይመሰክሩብሃል።

፭፤ የሱስ፡ግን፡ ከዚያም፡ በኋላ፡ አንዳች፡ *አልመለሰለትም፡ ጲላጦስ፡እስኪደነቅ፡ ድረስ። *ም፡ ፲፯፡ ፳፩። ኢሳ፡ ፶፫፡ ፯።

፮፤ በየበዓሉም፡ አንድ፡ የታሠረ፡ ይተውላቸው፡ ነበር፡ የወደዱትን።

፯፤ በርባንም፡ የሚሉት፡ ነበር፡ታሥሮ፡የነበረ፡ ከሸፍቶች፡ጋራ፡ በሁከት፡ መግደል፡ ያደረጉ።

፰፤ ሕዝቡም፡ጮኹ፡ ይለምኑም፡ ጀመሩ፡ ያደርግላቸው፡ ዘንድ፡ ወትሮ፡ እንደደረገላቸው።

፱፤ ጲላጦስ፡ግን፡ መለሰላቸው፡እንዲህ፡ሲል። ትወደላችሁን፡ የአይሁድን፡ንጉሥ፡ እተውላችሁ፡ ዘንድ።

፲፤ ያውቅ፡ነበርና፡ የካህናት፡ አለቆች፡ በቅንዓት፡ እርሱን፡ አሳልፈው፡እንደ፡ሰጡት። ዮሐ፡ ፲፩፡ ፵፰።

፲፩፤ የካህናት፡ አለቆችም፡ ሕዝቡን፡ አባበሉ፡ይለምኑት፡ ዘንድ፡ በርባንን፡ ቢተውላቸው፡ እንዲሻል።

፲፪፤ ጲላጦስም፡ መለሰ፡ደግሞም፡ አላቸው። ምን፡ ትሻላችሁ፡ በርሱ፡ አደርግበት፡ ዘንድ፡ የአይሁድ፡ ንጉሥ፡ እንደ፡ ሆነ፡ በምትሉት።

፲፫፤ እርሳቸውም፡ደግሞ፡ስቀለው፡ኢያሉ፡ጮሁ።

፲፬፤ ጲላጦስም፡ይላቸው፡ነበር። ምን፡ ክፋ፡አደረገ። እርሳቸው፡ግን፡ጩኸት፡አበዙ፡ኢያሉ፡ስቀለው።

፲፭፤ ጲላጦስም፡ሕዝቡን፡ደስ፡ያሰኛቸው፡ዘንድ፡ ወደደ፡ በርባንንም፡ ተወላቸው፡ የሱስንም፡ ገርፎ፡ ሰጣቸው፡ ይሰቀል፡ ዘንድ።

፲፮፤ ጭፍሮችም፡ ወደ፡ ፍርድ፡ሰፍራ፡ይዘውት፡ ሔደ፡ ወደ፡ ቤት፡ ውሥጥ፡ ጭፍራንም፡ ሁሉ፡ አከማቹበት።

፲፯፤ ቀይ፡ ሐርም፡አለበሱት። የሾህም፡ዘውድ፡ ጉነጉኑና፡ በላዩ፡ ደፉበት።

፲፰፤ ሰላምም፡ ይሰጡት፡ ጀመሩ፡ እንዲህ፡ ሲሉ። ደኅንነት፡ ላንተ፡ ይሁን፡ የአይሁድ፡ ንጉሥ፡ ሆይ።

፲፱፤ ራሱንም፡በዘንግ፡ ይመቱት፡ ነበሩ። ይተፉበትም፡ ነበሩ፡ በጕልበታቸውም፡ ተንበርክከው፡ ይሰግዱለት፡ ነበሩ።

፳፤ ከተሣለቁበትም፡በኋላ፡ ቀዩን፡ ሐር፡ ገፈፉት፡ ልብሱንም፡ አለበሱት፡ ሊሰቅሉትም፡ አወጡት።

፳፩፤ መስቀሉንም፡ ይሸከም፡ ዘንድ፡ አንድ፡ መንገድ፡ አላፊ፡ ጕተቱ፡ ሲሞን፡ የቀሬና፡ የሚባል፡ ከሜዳ፡ ሲመጣ። እርሱም፡ የሰከንድሮስና፡ *የሩፎስ፡ አባት። *ሮሜ፡ ፲፮፡ ፲፫።

፳፪፤ ወደ፡ጎልጎታም፡ሰፍራ፡አመጡት። ትርጓሜውን፡ የራስ፡ ቅል፡ ሰፍራ፡ የሚሉት።

፳፫፤ በከርቤ፡ የተደባለቀም፡ ወይን፡ *ሰጡት፡ ይጠጣ፡ ዘንድ። እርሱ፡ ግን፡ አልተቀበለውም። *መዝ፡ ፷፱፡ ፳፪።

፳፬፤ በሰቀሉትም፡ጊዜ፡ልብሱን፡ ተካፈሉ፡ዕፃም፡ ተጣጣሉበት፡ ኢየራሱ፡ሁሉ፡ የደረሰውን፡ይውሰድ፡ ዘንድ። መዝ፡ ፳፪፡ ፲፰።

፳፭፤ ጊዜውም፡ ሶስት፡ ሰዓት፡ ነበረ፡ ሰቀሉትም።

፳፮፤ የኃጢአቱም፡ ነገር፡ በላዩ፡ ተጽፎበት፡ ነበር፡ እንዲህ፡ሲል። ይህ፡ የአይሁድ፡ንጉሥ፡ ነው።

፳፯፤ ሁለት፡ ወንበዴችንም፡ ሰቀሉ፡ ከርሱ፡ ጋራ። አንዱን፡ በቀኙ፡ ሁለተኛውንም፡ በግራው።

፳፰፤ መጽሐፉም፡*ተፈጸመ፡የሚል።ከተላላፊችም፡ጋራ፡ ተቈጠረ። *ኢሳ፡ ፶፫፡ ፲፪።

፳፱፤ የሚያልፉም፡ ይሰድቡት፡ ነበሩ፡ ራሳቸውንም፡ይነቀንቁ፡ይሉም፡ነበሩ። እወይ። *ቤተ፡መቅደስን፡የምታፈርስ፡ ሆይ፡በሶስት፡ቀንም፡ የምትሰራው። *ም፡ ፲፬፡ ፶፰።

፴፤ ራስህን፡ አድን፡ ከመስቀልም፡ ውረድ።

፴፩፤ እንዲሁም፡ የካህናት፡ አለቆች፡ ደግሞ፡ እርሱ፡ በርሳቸው፡ ያፈዙበት፡ ነበሩ፡ ከጻፎች፡ ጋራ፡ሲሉ። ሌሎችን፡ አዳነ፡ ራሱን፡ ሊያድን፡ አይችልም።

፴፪፤ ክርስቶስ፡ የእሥራኤል፡ ንጉሥ፡ ዛሬ፡ ከመስቀል፡ይውረድ፡አይተን፡እንድናምን። ከርሱም፡ ጋራ፡ የተሰቀሉት፡ ደግሞ፡ ይላገዱት፡ ነበሩ። ማቴ፡ ፲፯፡ ፩፡ ፮።

፴፫፤ ስድስት፡ ሰዓትም፡ በሆነ፡ ጊዜ፡ ጨለማ፡ ሆነ፡ በምድር፡ ሁሉ፡ ላይ፡ እስከ፡ ዘጠኝ፡ ሰዓት፡ ድረስ።

፴፬፤ በዘጠኛውም፡ ሰዓት የሱስ፡ በታላቅ፡ ቃል፡

ጮኸ፡ እንዲህ፡ ሲል። *ኤሎሄ፡ ኤሎሄ፡ ለማ፡ ሰበቅ ታኒ። ትርጓሜው፡የሚሆን። አምላኬ፡ አምላኬ፡ ለ ምን፡ ተውኸኝ። መዝ፡ ፳፪፡ ፪።

፴፭፡ ስዎችም፡ ከቆሙት፡ በሰሙ፡ ጊዜ፡ አሉ። እ ነሆ፡ ኤልያስን፡ ይጸራል።

፴፮፡ አንድም፡ ፈጠነ፡ ሰፍነጉንም፡ መጣጣ፡ መላ በት፡ በዘንግም፡ አደረገው፡ አጠጣውም፡ እንዲህ፡ ሲል። ተውት፡ እንይ፡ ኤልያስ፡ መጥቶ፡ ያወርደው፡ እንደሆን።

፴፯፡ የሱስ፡ ግን፡ በታላቅ፡ ቃል፡ ጮኸ፡ ነፍሱንም፡ ሰጠ።

፴፰፡ የመቅደሱም፡ መጋረጃ፡ ከሁለት፡ ሁና፡ ተቀ ደደ፡ ከላይ፡ እስከ፡ ታች።

፴፱፡ የመቶውም፡ አለቃ፡ባንጻሩ፡ቁሞ፡የነበረው፡ እንደህ፡ ጮኾ፡ ነፍሱን፡ እንደ፡ ሰጠ፡ ባየ፡ ጊዜ፡ አለ። በውነት፡ ይህ፡ ሰው፡ የእግዚአብሔር፡ ልጅ፡ ኑርዋል።

፵፡ ሴቶችም፡ ደግሞ፡ ከሩቅ፡ የሚያዩ፡ ነበሩ። ከር ሳቸውም፡ አንዲቱ፡ ማርያም፡ የመግደላዊቱ፡ ነበረ ች። ማርያምም፡የታናሹ፡ የያዕቆብ፡እናት፡የዮሳም፡ እናት። ሰሎሜም። ሉቃ፡ ፰፡ ፪፡ ፫።

፵፩፡ እሉዚህ፡ ደግሞ፡ በገሊላ፡ ሳለ፡ ይከተሉት፡ ያገለግሉትም፡ የነበሩ። ብዙም፡ ሌሎች፡ ወደ፡ የሩሳ ሌም፡ ከርሱ፡ጋራ፡ ያወጡ።

፵፪፡ በመሸም፡ ጊዜ፡ የማዘጋጀት፡ ቀን፡ ነበረችና፡ ከሰንበት፡ በፊት። ዮሐ፡ ፲፱፡ ፴፰—፵፪።

፵፫፡ ዮሴፍ፡የአርማትያስ፡ የከበረ፡የምክር፡ አዋ ቂ፡ እርሱም፡ ደግሞ፡የእግዚአብሔርን፡ መንግሥት፡ ተስፋ፡ ያደርግ፡ የነበረ፡ መጣ፡ ደፍሮም፡ ወደ፡ ጲላጦ ስ፡ ገባ፡ ከርሱም፡ የየሱስን፡ ሥጋ፡ ለመነ።

፵፬፡ ጲላጦስ፡ ግን፡ ተፈጽሞ፡ እንደሞተ፡ የመቶ ውን፡ አለቃ፡ ወደርሱ፡ ጸራው፡ ከርሱም፡ ጠየቀ፡ ሙ ቶ፡ እንደሆነ፡ ከብዙ፡ ጊዜ።

፵፭፡ ነገሩንም፡ ከመቶው፡ አለቃ፡ ባወቀ፡ ጊዜ፡ ሥ ጋውን፡ ለዮሴፍ፡ ሰጠው።

፵፮፡ በፍታም፡ ገዛ፡አውርደም፡ በበፍታ፡ ጠቀለለ ው። በመቃብርም፡አኖረው፡ መቃብሩም፡ ከተጸረበ፡ ደንጊያ፡ ነበር። ደንጊያም፡ ገጠመ፡በመቃብሩ፡ ደጅ።

፵፯፡ ማርያምም፡ የመግደላዊቱ፡ ማርያምም፡ የዮሳ፡ እናት፡ ያዩ፡ ነበሩ፡ ወደት፡ እንደኖሩት።

## ምዕራፍ፡ ፲፮፡

፩፡ ሰንበትም፡ ባለፈ፡ጊዜ፡ ማርያም፡ የመግደላዊ ቱ፡ ማርያምም፡ የያዕቆብ፡ እናት፡ ሰሎሜም፡ ሽቱ፡ ገዙ፡ ሊመጡ፡ እርሱን፡ም፡ ሊቀቡት። ማቴ፡ ፳፰፡ ፩ ሉቃ፡ ፳፬። ዮሐ፡ ፳። ፩፡ ቆር፡ ፲፭።

፪፡ እጅግም፡ ማልደ፡ ከስምንት፡በመጀመርያው፡ ቀን፡ ወደ፡ መቃብር፡ መጡ፡ ፀሐይ፡ በወጣች፡ ጊዜ።

፫፡ እርሱ፡ በርሳቸውም፡ አሉ። ማን፡ ደንጊያውን፡ ከመቃብሩ፡ ደጅ፡ ይገለብጥልናል።

፬፡ ተመለከቱም፡ አዩም፡ ደንጊያው፡ ተገልብጦ፡ እንደ፡ ነበረ። እጅግ፡ ታላቅ፡ ነበርና።

፭፡ ወደ፡መቃብርም፡በገቡ፡ጊዜ፡ጐልማሳ፡አዩ፡በቀ ኝ፡ ተቀምጦ፡ ነጭ፡መጐናጸፊያ፡ለብሶ። ደነገጡም።

፮፡ እርሱ፡ግን፡አላቸው። አትደንግጡ። የናዝሬቱ ን፡ የሱስን፡የተሰቀለውን፡ትሻላችሁ። እርሱ፡ ተነሣ፡ ከዚህም፡ የለም። እነሆ፡ቦታው፡እርሱን፡ ያኖሩበት።

፯፡ ነገር፡ ግን፡ ሒዱ፡ ለደቀ፡ መዛሙርቱም፡ ንገርዋ ቸው፡ ለጴጥሮስም። ወደ፡ ገሊላ፡ ይቀድማችኋል። ከዚያ፡ታዩታላችሁ፡እንደ፡ ነገራችሁ። ም፡ ፲፬፡ ፳፰።

፰፡ ፈጥነውን፡ ወጡ፡ከመቃብርም፡ ሸሹ። ፍርሃት ና፡ መደነቅ፡ ይዞዋቸው፡ ነበርና። ለማንም፡ አንዳች፡ አልተናገሩም፡ ፈርተው፡ ነበሩና።

፱፡ የሱስ፡ ግን፡ ማልዶ፡ በተነሣ፡ ጊዜ፡ ከሳምንት፡ በ መጀመርያ፡ ቀን። አስቀድሞ፡ ለማርያም፡ ለመግደ ላዊቱ፡ ታየ፡ *ሰባት፡ አጋንንት፡ ያወጣላት።

*ሉቃ፡ ፰፡ ፪።

፲፡ እርስዋም፡ ሔደች፡ ከርሱ፡ ጋራ፡ ለነበሩትም፡ ነገረች፡ ሲያዝኑ፡ ሲያለቅሱም፡ የነበሩ።

፲፩፡ እርሳቸውም፡ በሰሙ፡ ጊዜ፡ ሕያው፡ እንደ፡ ሆነ፡ እርስዋም፡ እንዳየችው፡ አላመኑም።

፲፪፡ ከዚህም፡ በኋላ፡ ከርሳቸው፡ ለሁለቱ፡ በሌላ፡ መልክ፡ በመንገድ፡ ተገለጠ፡ ወደ፡ አገር፡ ሲሔዱ።

ሉቃ፡ ፳፬፡ ፲፫—፴፩።

፲፫፡ እርሳቸውም፡ ለቀሩት፡ ሒደው፡ነገርዋቸው። እለዚያንም፡ አላመኑም።

፲፬፡ ኋላም፡ ላሥራ፡ አንዱ፡ ታየ፡ ተቀምጠው፡ ሲ በሉ፡ ስለ፡ ሃይማኖታቸውም፡ መጕደል፡ ስለ፡ ልባቸ ውም፡ ጽናት፡ ገሠፃቸው፡ ያዩትን፡እንደ፡ ተነሣ፡ አላ መኑምና።

፲፭፡ አላቸውም። ወደ፡ ዓለም፡ ሁሉ፡ ሒዱ፡ ወን ጌልንም፡ ስበኩ፡ ለፍጥረት፡ ሁሉ።

ማቴ፡ ፳፰፡ ፲፰፡ ፲፱።

፲፮፡ ያመነ፡ የተጠመቀም፡ ይድናል። ያላመነ፡ግን፡ ይፈረድበታል። ዮሐ፡ ፫፡ ፴፮።

፲፯፡ ያመኑትንም፡ይህች፡ ታምራት፡ትከተላለች። በስሜ፡ ሰይጣናትን፡ ያወጣሉ። ባዲስ፡ ቋንቋ፡ ይናገ ራሉ። የሐዋ፡ ፪፡ ፬፡ ፲፩። ፲፡ ፵፮። ፲፱፡ ፮።

፲፰፡ እባብ፡ ይይዛሉ። የሚገድል፡ነገርም፡ቢጠጡ፡ አይጐዳቸውም። እጃቸውን፡ በድውያን፡ ላይ፡ይጭ ናሉ፡ እርሳቸውም፡ ይድናሉ። ሉቃ፡ ፲፡ ፲፱።

የሐዋ፡ ፳፰፡ ፫። ያዕ፡ ፭፡ ፲፬፡ ፲፭።

፲፱፡ ጌታም፡ ከነገራቸው፡ በኋላ፡ ወደ፡ ሰማይ፡ ከ ፍ፡ ከፍ፡ አለ፡ በእግዚአብሔርም፡ ቀኝ፡ ተቀመጠ።

የሐዋ፡ ፩፡ ፩—፲፩።

፳፡ እርሳቸው፡ ግን፡ ወጡ፡ በስፍራውም፡ ሁሉ፡ ሰበኩ፡ *ጌታም፡ ከርሳቸው፡ ጋራ፡ ያደርግ፡ ነበር፡ ቃላ ቸውንም፡ በምትከተል፡ ታምራት፡ ያጸና፡ ነበረ። አሜን። *ዕብ፡ ፪፡ ፬።

ተፈጸመ ፡ የማርቆስ ፡ ወንጌል ።

# የ ሉ ቃ ስ ፡ ወ ን ጌ ል።

# የጌታችን : የየሱስ : ክርስቶስ : ቅዱስ : ወንጌል : እንደ : ጻፈው፡ ቅዱስ : ሉቃስ።

ምዕራፍ፡ ፩፡

፩፤ አጅግ፡ ናቸውና፡ የሰራውን፡ ወሬ፡ በኛ፡ ዘንድ፡ ፈጽሞ፡ የታመነውን፡ በሥርዓት፡ ሊጽፉ፡ የፈተኑ።

፪፤ እንደ፡ ስጡኑ፡ ከጥንት፡ የዓይን፡ ምስክሮችና፡ የነገሩ፡ አገልጋዮች፡ የነበሩ። ዮሐ፡ ፩፡ ፲፬።
፪፡ ጴጥ፡ ፩፡ ፲፮።

፫፤ እኔም፡ ደግሞ፡ ከጥንት፡ ሁሉን፡ በውነት፡ ተከትዬ፡ ሳለሁ፡ በተራ፡ አጽፌልህ፡ ዘንድ፡ ወደድሁ፡ የከበርህ፡ ቴዎፊሎስ፡ ሆይ። የሐዋ፡ ፩፡ ፩።

፬፤ ታውቅ፡ ዘንድ፡ የተማርህበቱን፡ የነገሩን፡ እውነት። ፩፡ ጢሞ፡ ፫፡ ፲፭።

፭፤ በሄሮድስ፡ በይሁዳ፡ ንጉሥ፡ ዘመን፡ ካህን፡ ነበረ፡ ስሙም፡ ዘካርያስ፡ ነበር፡ ከአቢያ፡ *ሥርዓት። ምሽቱም፡ ከሐሮን፡ ልጆች፡ ስምዋም፡ ኤልሳቤጥ።
*፩፡ ዜና፡ ፳፭፡ ፲።

፮፤ ሁለቱም፡ ጻድቃን፡ ነበሩ፡ በእግዚአብሔር፡ ፊት፡ በትእዛዝ፡ ሁሉ፡ በእግዚአብሔርም፡ ሥርዓት፡ ያለ፡ ነውር፡ የሚሔዱ። ዘፍ፡ ፲፯፡ ፩።
የሐዋ፡ ፳፫፡ ፩።

፯፤ ልጅም፡ አልነበራቸውም። ኤልሳቤጥ፡ መካን፡ ነበረችና። ሁለቱም፡ በዘመናቸው፡ አርጅተው፡ ነበሩ። ዘፍ፡ ፲፰፡ ፲፩።

፰፤ እርሱም፡ በእግዚአብሔር፡ ፊት፡ ሲያገለግል፡ በተሠራው፡ በማገልገሉ፡ ወራት።

፱፤ እንደ፡ ካህናት፡ ልማድ፡ *የማጠኑ፡ ጊዜ፡ በዕፃ፡ ደረሰበት፡ ወደ፡ እግዚአብሔርም፡ መቅደስ፡ ገባ።
*ዘፀአ፡ ፴፡ ፩፡—፰።

፲፤ ሰውም፡ ሁሉ፡ በሚያ፡ ይጸልይ፡ ነበረ፡ በዕጣን፡ ጊዜ። ዘሌዋ፡ ፫፡ ፲፮፡ ፲፯። የሐዋ፡ ፫፡ ፩፡—፲።

፲፩፤ የእግዚአብሔርም፡ መልአክ፡ ታየው፡ በዕጣን፡ መሠዊያው፡ በቀኝ፡ ቁሞ። ዘፀአ፡ ፴፡ ፩።

፲፪፤ ዘካርያስም፡ ባየው፡ ጊዜ፡ ደነገጠ፡ ፍርሃትም፡ ወደቀበት። መሳ፡ ፲፫፡ ፮፡ ፳፪።

፲፫፤ መልአኩም፡ አለው። አትፍራ፡ ዘካርያስ፡ ሆይ። ጸሎትህ፡ ተሰምታለችና። ምሽትህም፡ ኤልሳቤጥ፡ ልጅ፡ ትወልድልሃለች፡ ስሙንም፡ ዮሐንስ፡ ትለዋለህ። ፩፡ ዮሐ፡ ፭፡ ፲፬።

፲፬፤ ደስታም፡ እልልታም፡ ይሆንልሃል። ብዙ፡ ሰዎችም፡ በመወለዱ፡ ደስ፡ ይላቸዋል። ቍ፡ ፶፰፡—፷።

፲፭፤ በእግዚአብሔር፡ ፊት፡ ታላቅ፡ ይሆናልና። የወይን፡ ፀጁም፡ አይጠጣም፡ የሚያሰክርም፡ ነገር፡ ሁሉ። መንፈስ፡ ቅዱስም፡ ይመላበታል፡ ከናቱ፡ ሆድ፡ ጀምሮ። መሳ፡ ፲፫፡ ፬፡ ፭። ማቴ፡ ፲፩፡ ፱፡ ፲።

፲፮፤ ከእሥራኤል፡ ልጆችም፡ አጅግ፡ ወደ፡ እግዚአብሔር፡ ወደምላካቸው፡ ይመልሳል።

፲፯፤ እርሱም፡ በፊቱ፡ ይሔዳል፡ በኤልያስ፡ መንፈስ፡ በኃይሉም። ያባቶችም፡ ልብ፡ ወደ፡ ልጆች፡ ይመልስ፡ ዘንድ፡ የማይታዘዙትንም፡ ወደ፡ ጻድቃን፡ ጥበብ፡ የቀና፡ ሕዝብም፡ ለእግዚአብሔር፡ ያዘጋጅ፡ ዘንድ።
ማቴ፡ ፲፯፡ ፲፩። ማልክ፡ ፫፡ ፩። ፬፡ ፮።

፲፰፤ ዘካርያስም፡ መልአኩን፡ አለው። ይህነን፡ በምን፡ አውቃለሁ። ሽማግሌ፡ ነኝና፡ ምሽቴም፡ ዘመንዋ፡ አለፈ።

፲፱፤ መልአኩም፡ መለሰ፡ አለውም። እኔ፡ *ገብርኤል፡ ነኝ፡ በእግዚአብሔር፡ ፊት፡ የምቆመው። ተልኬም፡ መጣሁ፡ ይህችን፡ የምስራች፡ እነግርህ፡ ዘንድ።
*ዳን፡ ፰፡ ፲፮። ዕብ፡ ፩፡ ፲፬።

፳፤ እነሆም፡ ድዳ፡ ትሆናለህ፡ መናገርም፡ አይቻልህም፡ ይህ፡ ነገር፡ እስከሚሆንበት፡ ቀን፡ ድረስ። *በነገሬ፡ አላመንኸምና፡ በጊዜው፡ የሚፈጸም።
*ቍ፡ ፵፭።

፳፩፤ ሕዝቡም፡ ዘካርያስን፡ ይጠብቁት፡ ነበሩ፡ በመቅደስ፡ ውሥጥ፡ ስለ፡ ዘገየ፡ ተደንቀው።

፳፪፤ በወጣም፡ ጊዜ፡ ይናገራቸው፡ ዘንድ፡ አልቻለም። አወቁም፡ ራእይ፡ እንደየ፡ በመቅደስ። እርሱ፡ ግን፡ በጁ፡ ይጠቅሳቸው፡ ነበር፡ ድዳም፡ ሁኖ፡ ተቀመጠ።

፳፫፤ የማገልገሉም፡ ወራት፡ በተፈጸመ፡ ጊዜ፡ ወደ፡ ቤቱ፡ ሔደ።

፳፬፤ ከዚያም፡ ቀን፡ በኋላ፡ ምሽቱ፡ ኤልሳቤጥ፡ ፀነሰች፡ ስውነትዋንም፡ አምስት፡ ወር፡ ሰውራ፡ ነበረች፡ እንደዚህ፡ ስትል።

፳፭፤ እንደዚህ፡ ሰራብኝ፡ እግዚአብሔር፡ በዚች፡ እኔን፡ ባየባት፡ ቀን፡ *እሳሬን፡ በሰው፡ ዘንድ፡ ሊያወጣው።
*ዘፀአ፡ ፴፡ ፳፫።

፳፮፤ በስድስተኛውም፡ ወር፡ ገብርኤል፡ መልአክ፡ ከእግዚአብሔር፡ ዘንድ፡ ተላከ፡ ወደ፡ ገሊላ፡ አገር፡ *ናዝሬት፡ የምትባል። *ዮሐ፡ ፩፡ ፵፮።

፳፯፤ ወደ፡ ቀንጆ፡ ላንድ፡ ሰው፡ የታጨች፡ ስሙን፡ ዮሴፍ፡ የሚሉት፡ ከዳዊት፡ ወገን። የቀንጆዪቱም፡ ስም፡ ማርያም፡ ነበረ። መዝ፡ ፴፫፡ ፲፰።
ማቴ፡ ፩፡ ፲፮፡ ፲፰።

፳፰፤ መልአኩም፡ ወደርሷ፡ በገባ፡ ጊዜ፡ አለ። ደስ፡ ይበልሽ፡ ጸጋ፡ ያገኘሽ፡ ሆይ፡ እግዚአብሔር፡ ካንቺ፡ ጋራ፡ ነው። በሴቶች፡ ዘንድ፡ የተባረክሽ፡ ነሽ።
ዮሐ፡ ፩፡ ፲፮።

፳፱፡ እርስዋም፡ ባየችው፡ ጊዜ፡ ከነገሩ፡ ደነገጠች፡ አሰበችም፡ እንደ፡ህ፡ ስትል። ይህ፡ ሰላም፡ ምንድር፡ ነው።

፴፡ መልአኩም፡አላት። አትፍሪ፡ማርያም፡ሆይ። ከእግዚአብሔር፡ ዘንድ፡ ጸጋ፡ አግኝተሻልና።
የሐዋ፡ ፯፡ ፵፮።።

፴፩፡ እነሆም፡ በሆድ፡ *ትፀንሻለሽ፡ ልጅም፡ ትወልጂለሽ፡ ስሙንም፡ †የሱስ፡ ትዪው፡ አለሽ።
*ኢሳ፡ ፯፡ ፲፬።። †ማቴ፡ ፩፡ ፳፩—፳፫።።

፴፪፡ ይህ፡ ታላቅ፡ ይሆናል፡ የልዑል፡ ልጅም፡ ይባላል። እግዚአብሔር፡አምላክም፡ *የደዊትን፡ያባቱን፡ ዙፋን፡ ይሰጠዋል።
*፪፡ ሳሙኤ፡ ፯፡ ፲፪።።

፴፫፡ በያዕቆብም፡ ወገን፡ ላይ፡ ለዘላለም፡ ይነግሣል። ለመንግሥቱም፡ ፍጻሜ፡ የለውም።
ዳን፡ ፯፡ ፲፬።። ሚክ፡ ፬፡ ፯።።

፴፬፡ ማርያምም፡ መልአኩን፡ አለችው። ይህ፡እንዴት፡ ይሆናል፡ ወንድ፡ ሳላውቅ።

፴፭፡ መልአኩም፡ መለሰ፡ አላትም። *መንፈስ፡ ቅዱስ፡ይመጣብሻል፡ የልዑልም፡ኃይል፡ያጸልልሻል። ስለዚህም፡ደግሞ፡ ቅዱሱ፡ ካንቸ፡ የተወለደው፡ የእግዚአብሔር፡ ልጅ፡ ይባላል።
*ማቴ፡ ፩፡ ፲፰፡ ፳።።
ዳን፡ ፱፡ ፳፬።።

፴፮፡ እነሆችም፡ኤልሳቤጥ፡ ዘመድሽ፡እርስዋም፡ ደግሞ፡ ልጅ፡ ፀነሰች፡ በርጅናዋ። ይህም፡ ወር፡ ስድስተኛ፡ ነው፡ ለዚያች፡ መካን፡ ለምትባለው።

፴፯፡ ነገር፡ ሁሉ፡ በእግዚአብሔር፡ ዘንድ፡ አይሳንምና።
ኤር፡ ፴፪፡ ፲፯፡ ፳፯።። ዘካ፡ ፰፡ ፮።።
ሮሜ፡ ፬፡ ፳፩።።

፴፰፡ ማርያም፡ አለች። እነሆኝ፡ የእግዚአብሔር፡ ባሪያ። እንደ፡ ነገርህ፡ ይሁንልኝ። መልአኩም፡ ከርስዋ፡ ተመለሰ።

፴፱፡ በዚያ፡ ወራትም፡ ማርያም፡ ተነሣች፡ ፈጥናም፡ ወደ፡ ተራራ፡ ሔደች፡ ወደ፡ ይሁዳ፡ አገር።

፵፡ ወደ፡ ዘካርያስም፡ ቤት፡ ገባች፡ ለኤልሳቤጥም፡ ሰላም፡ ሰጠቻት።

፵፩፡ ሆነም፡ ኤልሳቤጥ፡የማርያምን፡ ሰላም፡ በሰማች፡ ጊዜ፡ ፅንሱ፡ በሆድዋ፡ ተንላበጠ። በኤልሳቤጥም፡ መንፈስ፡ ቅዱስ፡ መላባት።
ቍ፡ ፲፭።።

፵፪፡ በታላቅ፡ ቃልም፡ ጮኸች፡ አለችም። አንቺ፡ በሴቶች፡ *የተባረክሽ፡ ነሽ፡ የሆድሽም፡ ፍሬ፡ የተባረከ፡ ነው።
*ቍ፡ ፳፰።።

፵፫፡ ለኔም፡ እንዴት፡ ይገባኛል፡ የጌታዬ፡ እናት፡ ወደኔ፡ ትመጭ፡ ዘንድ።

፵፬፡ እነሆ፡ የሰላምሽ፡ ድምፅ፡ በጆሮዬ፡ በሆነ፡ ጊዜ፡ ፅንሱ፡ በሆዴ፡ ተዘልዋልና፡ በደስታ።

፵፭፡ ምስጋናም፡ ለምታምን፡ይገባታል። ለርስዋ፡ የተነገረው፡ፍጻሜ፡ ይሆንላታልና፡ ከእግዚአብሔር፡ ዘንድ።
ም፡ ፲፩፡ ፳፰።።

፵፮፡ ማርያም፡ አለች። ነፍሴ፡ እግዚአብሔርን፡ ታላቅ፡ ታደርገዋለች።
፩፡ ሳሙኤ፡ ፪፡ ፩—፲።።

፵፯፡ መንፈስም፡ በእግዚአብሔር፡ በመድኃኒቴ፡ ደስ፡ ይላታል።
አንባ፡ ፫፡ ፲፰።።

፵፰፡ የባሪያዪቱን፡መዋርድ፡ *አይትዋልና። እነሆ፡ ከዛሬ፡ ጀምር፡ ትውልድ፡ ሁሉ፡ †ያመሰግኑኛልና።
*መዝ፡ ፻፲፫፡ ፯፡ ፰።። ዘፍ.ጥ፡ ፴፡ ፲፫።። †ም፡ ፲፩፡ ፳፰።።

፵፱፡ እርሱ፡ ብርቱ፡ የሚሆን፡ ታላቅ፡ ስራ፡ በኔ፡ አድርጓልና፡ ስሙም፡ ቅዱስ፡ ነው።
መዝ፡ ፻፳፮፡ ፫።።
ኢሳ፡ ፮፡ ፫።።

፶፡ በሚፈሩትም፡ምሕረቱ፡ ለልጅ፡ልጅ፡ ነው።
መዝ፡ ፻፫፡ ፲፫—፲፯።።

፶፩፡ ኃይልን፡ በክንዱ፡አደረገ። ትቢተኞችን፡ በልባቸው፡ አሳብ፡ በተነ።
፪፡ ሳሙኤ፡ ፳፪፡ ፳፰።።

፶፪፡ ብርቶችን፡ከዙፋናቸው፡አወረደ። የተዋረዱትንም፡ ከፍ፡ ከፍ፡ አደረጋቸው።
መዝ፡ ፻፵፯፡ ፮።።

፶፫፡ የተራቡትን፡በበጎ፡ነገር፡መላ። ባለጠጎችንም፡ ባዶ፡እጃቸውን፡ ሰደዳቸው።
መዝ፡ ፴፬፡ ፲፩።።
፻፯፡ ፱።። ዮሐ፡ ፩፡ ፲፩።።

፶፬፡ እሥራኤል፡ ባሪያውን፡ ተቀበለ፡ ምሕረቱን፡ እንዲያስብ።
ዘዳግ፡ ፯፡ ፯፡ ፰።።

፶፭፡ ላባቶቻችን፡ እንዳለ፡ ለአብርሃም፡ ለዘሩም፡ እስከ፡ ዘላለም፡ ድረስ።
ዘፍ.ጥ፡ ፲፯፡ ፯።። ፲፰፡ ፲፰።።

፶፮፡ ማርያምም፡ ከርስዋ፡ ዘንድ፡ ተቀመጠች፡ ሶስት፡ ወር፡ የሚያህል። ወደ፡ ቤትዋም፡ ተመለሰች።

፶፯፡ ኤልሳቤጥ፡ግን፡ ወራትዋ፡ ደረሰ፡ ልትወልድ፡ ወንድ፡ ልጅም፡ ወለደች።
ቍ፡ ፲፫።።

፶፰፡ ጎረቤቶችዋም፡ ዘመዶችዋም፡ ሰሙ፡ እግዚአብሔር፡ ምህረቱን፡ እንዳገነነላት፡ ከርስዋም፡ጋራ፡ ደስ፡ አላቸው።

፶፱፡ በስምንተኛውም፡ ቀን፡ ሕፃኑን፡ ሊገዝሩት፡ መጡ፡ ባባቱ፡ ስምም፡ዘካርያስ፡አሉት።
ዘፍ.ጥ፡ ፲፯፡ ፲፪።።

፷፡ እናቱ፡ ግን፡ መለሰች፡ አለችም፡ አይደለም፡ ነገር፡ግን፡ ዮሐንስ፡ ይባላል።
ቍ፡ ፲፫።።

፷፩፡ አልዋትም። ከወገንሽ፡በዚህ፡ስም፡ማንም፡ አይጠራም።

፷፪፡ አባቱንም፡ ጠቀሱት፡ ምን፡ ይወዳል፡ ይጠሩት፡ ዘንድ።

፷፫፡ ብራናም፡ እኝ፡ ጻፈም፡ እንደህ፡ሲል። ስሙ፡ ዮሐንስ፡ ነው። ሁሉም፡ አደነቁ።

፷፬፡ የዚያን፡ ጊዜም፡ አፉ፡ ተከፈተ፡ ምላሱም፡ ተፈታ። እግዚአብሔርንም፡ኢያመሰገነ፡ ተናገረ።
- መዝ፡ ፻፲፮፡ ፲።።

፷፭፡ ፍርሃትም፡ በጎረቤቶቻቸው፡ሁሉ፡ ሆነ። በይሁዳም፡ ተራራ፡ ሁሉ፡ ይህ፡ ነገር፡ ወጣ።
መዝ፡ ፴፬፡ ፫፡ ፬።።

፷፮፡ የሰሙትም፡ በልባቸው፡ አሰቡ፡ እንደህ፡ ሲሉ። እንጃ፡ ምን፡ ይሆን፡ይህ፡ ሕፃን። የእግዚአብሔ

ርም፡ እጅ፡ ከርሱ፡ ጋራ፡ ነበረች። ዕዝ፡ ፯፡ ፮።
ሉቃ፡ ፪፡ ፲፭።

፷፯፡ ዘካርያስም፡ አባቱ፡ መንፈስ፡ ቅዱስ፡ መላ፡ እንደሀ፡ ሲልም፡ ተነበየ።

፷፰፡ የእሥራኤል፡ አምላክ፡ እግዚአብሔር፡ ይባረክ። ወገኑን፡ ጐብኝቶዋልና፡ ለርሳቸውም፡ መድኀኒት፡ ሰድዋልና። መዝ፡ ፵፩፡ ፲፫። ኢሳ፡ ፵፫፡ ፩።
ሉቃ፡ ፯፡ ፲፮።

፷፱፡ የመድኀኒትም፡ ቀንድ፡ አስነሣልን፡ በባርያው፡ በዳዊት፡ ቤት። መዝ፡ ፻፴፪፡ ፲፯።
የሐዋ፡ ፱፡ ፲፰።

፸፡ ከጥንት፡ ጀምሮ፡ በነበሩት፡ በቅዱሳን፡ በነቢያቱ፡ አፍ፡ እንደ፡ ተናገረ። ኤር፡ ፳፫፡ ፮።
የሐዋ፡ ፫፡ ፳፩፡ ፳፬።

፸፩፡ ከቦደረኞቻችን፡ያድነ፡ ዘንድ፡ ከሚጸሉትም፡ ሁሉ፡ እጅ። መዝ፡ ፻፮፡ ፲። ዘሌዋ፡ ፳፮፡ ፵፪።

፸፪፡ ምሕረቱን፡ካባቶቻችን፡ጋራ፡ያደርግ፡ዘንድ። የተቀደሰውንም፡ ኪዳኑን፡ ያስብ፡ ዘንድ።
ዘፍ፡ ፳፪፡ ፲፮። ሚክ፡ ፯፡ ፳።

፸፫፡ መሐላውን፡ ለአብርሃም፡ላባታችን፡ የማለበቱን፡ ይሰጠን፡ዘንድ።

፸፬፡ ከጠላቶቻችን፡እጅ፡በደነ፡ጊዜ፡እናገለግለው፡ ዘንድ፡ ያለ፡ ፍርሃት። ቲቶ፡ ፪፡ ፲፪—፲፬።

፸፭፡ በቅድስና፡ በጽድቅም፡ በፊቱ፡ በሕይወታችን፡ ዘመን፡ ሁሉ። ገላት፡ ፪፡ ፳። ቀል፡ ፩፡ ፳፪።

፸፮፡ አንተም፡ ሕፃን፡ ሆይ፡ የልዑል፡ ነቢይ፡ ትባላለህ። በእግዚአብሔር፡ ፊት፡ ትሔዳለህና፡ መንገዱን፡ ልታበጅ። ማቴ፡ ፫፡ ፫። መልክ፡ ፬፡ ፭።

፸፯፡ የድኅነትን፡ እውቀት፡ ለወገኑ፡ ትሰጥ፡ ዘንድ፡ በኀጢአታቸው፡ መስተስረያ። ኢሳ፡ ፶፫፡ ፲፩።
ኤር፡ ፴፩፡ ፴፬።

፸፰፡ ባምላካችን፡መራራት፡በምሕረቱም፡እኛን፡ በርሱዋ፡ ያሰበነ፡ ብርሃን፡ ከላይ፡ ይወጣልን፡ ዘንድ።
ዘኍል፡ ፳፬፡ ፲፯። ኢሳ፡ ፷፡ ፩፡ ፪።

፸፱፡ ያበራ፡ ዘንድ፡ በጨለማ፡በሞትም፡ ጽላ፡ ለተቀመጡት። እግሮቻችነን፡ በሰላም፡ መንገድ፡ ያቀና፡ ዘንድ። ኢሳ፡ ፱፡ ፪። ፷፡ ፩። ሮሜ፡ ፫፡ ፲፯።

፹፡ ሕፃኑም፡ አደገ፡ በመንፈስም፡ ይጸና፡ ነበረ፡ *በምድረ፡ በደም፡ ነበረ፡ ለእሥራኤል፡ እስከታየበት፡ ቀን፡ ድረስ። ም፡ ፪፡ ፵፡ ፶፪። *ማቴ፡ ፫፡ ፩።

## ምዕራፍ፡ ፪፡

፩፡ በዚያም፡ ወራት፡ ትእዛዝ፡ ከአውጉስጦስ፡ ቄሣር፡ ወጣ፡ አገሩ፡ ሁሉ፡ ይጻፍ፡ ዘንድ።

፪፡ ይህ፡ ጽፈት፡ መጀመርያ፡ ነበረ፡ ቀሬኔዎስ፡ በሶርያ፡ አገር፡ ሹም፡ በነበረ፡ ጊዜ። የሐዋ፡ ፭፡ ፴፯።

፫፡ ሁሉም፡ ሔደ፡ ይጻፍ፡ ዘንድ፡ ኢያንዳንደ፡ ወደ፡ አገሩ።

፬፡ ዮሴፍም፡ ደግሞ፡ ከገሊላ፡ወጣ፡ ከናዝሬት፡ አገር፡ ወደ፡ ይሁደ፡ ወደ፡ ዳዊት፡ አገር፡ ቤተ፡ ልሔም፡ ወደምትባል። ከዳዊት፡ወገን፡ነበርና፡ከዘመዶቹም።
ም፡ ፩፡ ፳፯። ሚክ፡ ፭፡ ፩።

፭፡ ይጻፍ፡ ዘንድ፡ ከሙሽራው፡ ከማርያም፡ ጋራ። እርሱዋም፡ ፀንሳ፡ ነበረች። ም፡ ፩፡ ፳፯።

፮፡ እርሳቸውም፡ ከዚያው፡ ሳሉ፡ የመውለድዋ፡ ዘመን፡ ደረሰ።

፯፡ የበኵር፡ ልጅዋንም፡ ወለደች። በመጠቅለያም፡ ጠቀለለችው፡ በበረትም፡ አኖረችው። ስፍራ፡ አልነበራቸውምና፡ በእንግዶች፡ ማደርያ። ማቴ፡ ፩፡ ፳፭።

፰፡ በዚያችም፡ አገር፡ እረኞች፡ ነበሩ፡ በሜዳ፡ የተቀመጡ፡ የሌትም፡ ትጋት፡ የተጉ፡ ስለ፡ መንጋቸው።

፱፡ እነሆም፡ የእግዚአብሔር፡ መልአክ፡ በርሳቸው፡ ላይ፡ ቁሞ፡ ነበረ፡ በእግዚአብሔር፡ ብርሃንም፡ በዙርያቸው፡ አበራ፡ ታላቅ፡ ፍርሃትም፡ ፈሩ። ኢሳ፡ ፮፡ ፩።

፲፡ መልአኩም፡ አላቸው። አትፍሩ። እነሆ፡ እኔ፡ የሕዝብ፡ ሁሉ፡ የሚሆን፡ ታላቅ፡ የደስታ፡ የምሥራች፡ እነግራችኋለሁና። ኢሳ፡ ፱፡ ፮—፯።

፲፩፡ ዛሬ፡ መድኀን፡ ተወልዶላችኋልና፡ እርሱም፡ ክርስቶስ፡ ጌታ፡ በዳዊት፡ አገር። ዮሐ፡ ፬፡ ፵፪።

፲፪ ይህም፡ መልክት፡ ይሁንላችሁ። ሕፃኑን፡ ታገኙላችሁ፡ በመጠቅያ፡ ተጠቅልሎ፡ በበረትም፡ ተጋድሞ።

፲፫፡ ድንገትም፡ ብዙ፡ *የሰማዊ፡ ሠራዊት፡ ከመልአኩ፡ ጋራ፡ ነበረ፡ እግዚአብሔርን፡ ሲያመሰግኑ፡ እንደህ፡ ሲሉም። *ዳን፡ ፯፡ ፲። ራእ፡ ፭፡ ፲፩።

፲፬፡ ምስጋና፡ ይሁን፡ ለእግዚአብሔር፡ በላይ። ሰላምም፡ በምድር፡ ላይ፡ በሰውም፡ ፈቃድ።
ኢሳ፡ ፶፯፡ ፲፱። ሮሜ፡ ፭፡ ፩። ኤፌ፡ ፪፡ ፲፬—፲፯።

፲፭፡ መላእክትም፡ ከርሳቸው፡ ወደ፡ ሰማይ፡ በሔዱ፡ ጊዜ፡ ጠባቂች፡ ሰዎች፡ እርሱ፡ በርሳቸው፡ አሉ። ወደ፡ ቤተ፡ ልሔም፡ እንሒድ፡ ይህነን፡ ነገር፡ እናይ፡ ዘንድ፡ እግዚአብሔር፡ ያስታወቀነን።

፲፮፡ ፈጥነውም፡ መጡ፡ ማርያምንም፡ አገኙ፡ ዮሴፍንም፡ ሕፃኑንም፡ በበረት፡ ወድቆ። ማቴ፡ ፪፡ ፲፩።

፲፯፡ ባዩም፡ ጊዜ፡ ለርሳቸው፡ ስለዚህ፡ ሕፃን፡ የተባለውን፡ ነገር፡ አወሩ። ቍ፡ ፲—፲፪።

፲፰፡ የሰሙትም፡ ሁሉ፡ ተደነቁ፡ እረኞች፡ ከርሳቸው፡ ጋራ፡ ከተናገሩበት፡ የተነሣ።

፲፱፡ ማርያም፡ ግን፡ ይህነን፡ ነገር፡ ሁሉ፡ ትጠብቀው፡ በልብዋም፡ ታስበው፡ ነበረች። ም፡ ፩፡ ፳፱፡ ፷፮፡ ፶፩።

፳፡ እረኞችም፡ ተመለሱ፡ እግዚአብሔርን፡ ኢያከበሩ፡ ኢያመሰገኑም፡ በሰሙት፡ ባዩትም፡ ሁሉ፡ እንደ፡ ተባለላቸው። መዝ፡ ፻፵፯፡ ፩።

፳፩፡ ስምንት፡ ቀንም፡ በተፈጸመ፡ ጊዜ፡ ሕፃኑ፡ ሊገዘር፡ ስሙ፡ የሱስ፡ ተጸራ፡ ከመልአኩ፡ አስቀድሞ፡ የተባለበት፡ በሆድ፡ ሳይረገዝ። ም፡ ፩፡ ፴፩፡ ፶፱።

፳፪፡ የመንጻትዋም፡ ወራት፡ በተፈጸመ፡ ጊዜ፡ እንደ፡ ሙሴ፡ ሕግ፡ ወደ፡ የሩሳሌም፡ ይዘውት፡ ወጡ፡ በእግዚአብሔር፡ ፊት፡ ያቀሙት፡ ዘንድ። ዘሌዋ፡ ፲፪፡ ፪።

፳፫፥ በእግዚአብሔር፡ሕግ፡እንደ፡ተጻፈ። ወንድ፡ ሁሉ፡የእናቱን፡ማሕፀን፡የሚከፍት፡ለእግዚአብሔር፡ የተቀደሰ፡ ይባል። ዘፀአ፡ ፲፫፡ ፪።

፳፬፥ መሥዋዕትም፡ሊያቀርቡ፡ በእግዚአብሔር፡ *ሕግ፡እንደ፡ ተባለ፡ ሁለት፡ ዋልያ፡ ወይም፡ ሁለት፡ የርግብ፡ግልግል። *ዘሌዋ፡ ፲፪፡ ፰።

፳፭፥ እነሆም፡ ሰው፡ ነበረ፡ በየሩሳሌም፡ ስሙን፡ ስምዖን፡የሚሉት። ይህም፡ ሰው፡ጻድቅ፡የዋህም፡ ነበረ፡ የእሥራኤልንም፡ ደስታ፡ *ተስፋ፡ ያደርግ፡ ነበረ። መንፈስ፡ቅዱስም፡ነበረበት። *ሐጌ፡ ፪፡ ፰።

፳፮፥ ከመንፈስ፡ ቅዱስም፡ ተገልጦለት፡ ነበረ፡ ሞት፡ እንደያይ፡ የእግዚአብሔርን፡ መሢሕ፡ ሳያይ። ሙዝ፡ ፹፱፡ ፵፱።

፳፯፥ በመንፈስም፡ ወደ፡ መቅደስ፡ ደረሰ። አባት፡ እናቱም፡ ብላቴናውን፡ የሱስን፡ ይዘው፡ በገቡ፡ ጊዜ፡ እንደ፡ ሕጉ፡ ልማድ፡ ያደርጉለት፡ ዘንድ።

ቍ፡ ፳፪፡—፳፬።

፳፰፥ እርሱ፡ ደግሞ፡ በክንዱ፡ ተሸከመው፡ እግዚአብሔርንም፡ ባረከ፡ አለም።

፳፱፥ ዛሬ፡ ባርያህን፡ በሰላም፡ ትሰዳለህ፡ አቤቱ፡ እንደ፡ ነገርህ። ዘፍ፡ ፵፮፡ ፴። ራእ፡ ፲፬፡ ፲፫።

፴፥ ዓይኖቼ፡ማዳንህን፡አይተዋልና።

ዘፍ፡ ፵፱፡ ፲፡ ፲፰።

፴፩፥ በአሕዛብ፡ ሁሉ፡ ፊት፡ ያዘጋጀኸውን።

ኢሳ፡ ፶፪፡ ፲።

፴፪፥ ብርሃን፡ለአሕዛብ፡ ማብራት፡ ክብርም፡ለእሥራኤል፡ለወገንህ። ኢሳ፡ ፵፪፡ ፮። ፵፱፡ ፮።

፴፫፥ ዮሴፍም፡ እናቱም፡ ይደነቁ፡ ነበር፡ ስለርሱ፡ ስለተባለው።

፴፬፥ስምዖንም፡ባረካቸው፡ለናቱ፡ለማርያምም፡ አለ። እነሆ፡ ይህ፡ የተቀመጠ፡ ነው፡ *ለመውደቅ፡ ለመነሣትም፡ ለብዙ፡ ሰዎች፡ ከእሥራኤል፡ ወገን፡ ለምትከራከርም፡ ምልክት። *ኢሳ፡ ፰፡ ፲፬።

ማቴ፡ ፳፩፡ ፵፪። ሮሜ፡ ፱፡ ፴፪፡ ፴፫።

፴፭፥ ባንቺም፡ ደግሞ፡ በልብሽ፡ ሰይፍ፡ ይገባል፡ አሳቦች፡ ከብዙ፡ ሰዎች፡ ልብ፡ ይገለጡ፡ ዘንድ።

ዮሐ፡ ፲፱፡ ፳፭፡ ፳፯።

፴፮፥ ሐናም፡ ነቢዪቱ፡ የፋኑኤል፡ ልጅ፡ ከአሴር፡ ወገን፡የምትሆን፡ነበረች። ይህችም፡አርጅታ፡ነበረች፡ በብዙ፡ ዘመን። ከባልዋም፡ ጋራ፡ ተቀመጠች፡ ከድንግልናዋ፡ በኋላ፡ ሰባት፡ አመት።

፴፯፥ እርስዋም፡ የሰማንያ፡ አራት፡ አመት፡ መበለት፡ ነበረች። ከቤተ፡ መቅደስም፡ ሳትለይ፡ በጾም፡ በጸሎትም፡ ሌትና፡ ቀን፡ ታገለግል፡ ነበረች።

፩፡ ጢሞ፡ ፭፡ ፭።

፴፰፥ እርስዋም፡ በዚያ፡ ጊዜ፡ መጣች፡ እግዚአብሔርንም፡ ባረከች፡ ስለርሱም፡ ትናገር፡ ነበረች፡ የየሩሳሌምን፡ መድኃኒት፡ ተስፋ፡ ለሚያደርጉ፡ ሁሉ።

ቍ፡ ፳፭።

፴፱፥ ሁሉንም፡ እንደ፡ እግዚአብሔር፡ ሕግ፡ በጨረሱ፡ ጊዜ፡ወደ፡ ገሊላ፡ ተመለሱ፡ ወደ፡ አገራቸው፡ ወደ፡ ናዝሬት። ቍ፡ ፳፪።

፵፥ ሕፃኑ፡ግን፡አደገ፡ በመንፈስም፡ጸና፡ጥበብም፡ መላበት። የእግዚአብሔርም፡ ጸጋ፡ በርሱ፡ ነበረች በት። ቍ፡ ፶፪። ም፡ ፩፡ ፹።

፵፩፥ አባቱና፡ እናቱ፡ ኢያመቱ፡ ወደ፡ የሩሳሌም፡ ይሔዱ፡ ነበሩ፡ *በፋሲካ፡ በዓል።

*ዘፀአ፡ ፳፫፡ ፲፬፡—፲፯።

፵፪፥ አሥራ፡ ሁለት፡ አመትም፡ በሆነው፡ ጊዜ፡ ወደ፡ የሩሳሌም፡ ወጡ፡ እንደ፡ በዓሉ፡ ወግ።

፵፫፥ ወራቱም፡ በተፈጸመ፡ጊዜ፡ ሲመለሱ፡ ብላቴናው፡የሱስ፡ በየሩሳሌም፡ ቀረ። ዮሴፍም፡እናቱም፡ አላወቁም።

፵፬፥ ከባልንጀሮቹ፡መንገደኞች፡ ጋራ፡ የነበረ፡ ይመስላቸው፡ ነበርና፡ ያንድ፡ ቀን፡መንገድ፡ ሒደው፡ ከዘመዶቻቸው፡ ከሚያውቋቸውም፡ ዘንድ፡ ፈለጉት።

፵፭፥ ባላገኙትም፡ጊዜ፡ ወደ፡ የሩሳሌም፡ ተመለሱ፡ ሊሹት።

፵፮፥ ከሦስት፡ ቀንም፡ በኋላ፡አገኙት፡ በመቅደስ፡ ተቀምጦ፡ በመምህራን፡ መካከል፡ ሲሰማቸው፡ ሲጠይቃቸውም።

፵፯፥ የሚሰሙትም፡ሁሉ፡ይደነቅ፡ነበረ፡ከማስተዋሉ፡ከምላሹም፡የተነሣ። ም፡ ፪፡ ፵፱። ዮሐ፡ ፯፡ ፲፭።

፵፰፥ ባዩትም፡ጊዜ፡ አደነቁ። እናቱም፡ አለችው። ልጄ፡ ሆይ፡ ለምን፡ እንደህ፡ አደረግህነ። እነሆ፡አባትህና፡ እኔ፡ እንሻሃለን፡ ተጨንቀን።

፵፱፥ አላቸውም። ለምን፡ አሻችሁኝ። አታውቁምን፡ *ላባቴ፡ በሚሆነው፡ እሆን፡ ዘንድ፡ እንዲገባኝ።

*ዮሐ፡ ፪፡ ፲፮።

፶፥ እርሳቸው፡ ግን፡ ያላቸውን፡ ነገር፡ አላስተዋሉም።

፶፩፥ ከርሳቸውም፡ ጋራ፡ ወረደ፡ ወደ፡ ናዝሬትም፡ መጣ፡ ለርሳቸውም፡ ይታዘዝ፡ ነበረ። እናቱም፡ ይህነን፡ ሁሉ፡ ነገር፡ በልብዋ፡ ትጠብቀው፡ ነበረች።

*ቍ፡ ፲፱። ዘፀአ፡ ፴፡ ፲፩።

፶፪፥ የሱስም፡ በጥበብና፡ በቁመት፡ ያድግ፡ ነበረ፡ በጸጋም፡ በእግዚአብሔር፡በሰውም፡ ዘንድ።

ቍ፡ ፵። ሳሙ፡ ፪፡ ፳፮።

ምዕራፍ፡ ፫፥

፩፥ ጢቤርዮስ፡ ቄሳር፡ በነገሠ፡ ባሥራ፡ አምስት፡ አመት፡ የጳንጠያዊ፡ ጲላጦስ፡ በይሁዳ፡በተሾመ፡ ጊዜ፡ ሄሮድስም፡ ያራተኛ፡ አለቃ፡ በገሊላ፡ወንድሙም፡ ፊልጶስ፡ ያራተኛ፡ አለቃ፡ በኢጡርያ፡በጥራኮኒጢስ፡ አገርም፡ ሊሳንያስም፡ ያራተኛ፡ አለቃ፡ በአቢሌኔ።

፪፥ ሐና፡ ቀያፋም፡ የካህናት፡አለቆች፡በሆኑ፡ጊዜ፡ የእግዚአብሔር፡ ነገር፡ በዮሐንስ፡ በዘካርያስ፡ ልጅ፡ ሆነ፡ በምድረ፡ በዳ።

፫፡ በዮርዳኖስም፡ ዙርያ፡ ባለው፡ አገር፡ *ሁሉ፡ መ
ጣ፡ በንስሐ፡ ጥምቀት፡ ሲሰበክ፡ ለኃጢአት፡ሰርየት።
*ማቴ፡ ፫፡ ፩፡ ፪።። ማር፡ ፩፡ ፩—፮።።
፬፡ በነቢዩ፡በኢሳይያስ፡ መጽሐፍ፡ነገር፡እንደ፡ተጻ
ፈ፡ እንደሁ፡ ሲል። ያዋጅ፡ ነጋሪ፡ ቃል፡ በምድረ፡ በደ፡
የሚጮሁ። የእግዚአብሔርን፡ መንገድ፡ አዘጋጁ። ጎ
ደናውንም፡ አቅኑ።። *ኢሳ፡ ፵፡ ፫፡ ፬።።
፭፡ ቈላ፡ ሁሉ፡ ክፍ፡ ይበል። ተራራውና፡ ኮረፍታ
ውም፡ ሁሉ፡ ዝቅ፡ ይበል። ጠማማውም፡ይቅና፡አቀ
በቱም፡ ሜዳ፡ ይሁን።
፮፡ ሥጋም፡ የለበሰ፡ሁሉ፡የእግዚአብሔርን፡ መድ
ኃኒት፡ ያያል። ኢሳ፡ ፶፪፡ ፲።።
፯፡ ከርሱም፡ ሊጠመቁ፡ ለወጡ፡ አሕዛብ፡ ይል፡
ነበረ። እላንት፡ *የጉበና፡ ልጆች፡ ማን፡ አመለከታች
ሁ፡ እንድታመልጡ፡ ከሚመጣው፡ ቍጣ።
*ማቴ፡ ፳፫፡ ፴፫።።
፰፡ አሁንም፡ ፍሬ፡ አድርጉ፡ ንስሐ፡ የሚገባው።
አትጀምሩም፡ ትሉ፡ ዘንድ፡ በልባችሁ፡ አባታችን፡ አ
ብርሃም፡ ነው። እኔ፡ እላችኋለሁና፡ እግዚአብሔር፡
ቻይ፡ እንደሆነ፡ከለዚህ፡ድንጋዮች፡ለአብርሃም፡ልጆች፡
ያስነሣ፡ ዘንድ። ማቴ፡ ፫፡ ፱።። ዮሐ፡ ፰፡ ፴፱።።
፱፡ አሁንም፡ ደግሞ፡ ምሳር፡ *በዛፎች፡ ስር፡ ላይ፡
ተቀምጦዋል። ዛፍም፡ ሁሉ፡ መልካም፡ †ፍሬ፡ የማ
ያፈራ፡ ይቈረጣል፡ ወደሳትም፡ ይጣላል።
*ማቴ፡ ፯፡ ፲፱።። †ዮሐ፡ ፲፭፡ ፪፡ ፮።።
፲፡ የሰው፡ ብዛትም፡ ጠየቁት፡ እንደሁ፡ ሲሉ። ም
ን፡ እናድርግ። የሐዋ፡ ፪፡ ፴፯።።
፲፩፡ እርሱም፡መለሰ፡አላቸውም። ሁለት፡ልብስ፡
ያለው፡ ለሌለው፡ ይስጥ። ምግብም፡ ያለው፡ እንደ
ሁ፡ ያድርግ። ኢሳ፡ ፶፰፡ ፯።። ያዕ፡ ፪፡ ፲፫፡ ፲፭።።
፲፪፡ ቀራጮችም፡ ደግሞ፡ሊጠመቁ፡መጡ፡ አሉት
ም። መምህር፡ ሆይ፡ ምን፡ እንዝራ። ማቴ፡ ፳፩፡ ፴፪።።
፲፫፡ እርሱም፡ አላቸው። ከታዘዘላችሁ፡ አብልጣ
ችሁ፡ አትውሰዱ።
፲፬፡ ጭፍሮችም፡ ደግሞ፡ ጠየቁት፡ እንደሁ፡ሲሉ።
እኛም፡ ደግሞ፡ ምን፡እናድርግ፡ አላቸውም። በማን
ም፡ ግፍ፡ አትስሩ። ማንንም፡በሐሰት፡ አትክሰሱ። ደ
መወዛችሁም፡ ይብቃችሁ። ዘሌዋ፡ ፲፱፡ ፲፫።።
፲፭፡ ሕዝቡም፡ ሲጠብቁ፡ሁሉም፡በልባቸው፡ስለ፡
ዮሐንስ፡ ሲያስቡ፡ ክርስቶስ፡ እንደ፡ ሆነ፡ ብለው።
ዮሐ፡ ፩፡ ፲፱፡ ፳።።
፲፮፡ ዮሐንስ፡ መለሰ፡ ለሁሉም፡ አላቸው። እኔስ፡
በውኃ፡ አጠምቃችኋለሁ። ከኔ፡ የሚበረታ፡ ግን፡ ይ
መጣል፡የማይገባኝ፡የጫማውን፡ሲር፡እፈታ፡ዘንድ።
እርሱ፡ ያጠምቃችኋል፡ በመንፈስ፡ ቅዱስ፡ በእሳት
ም። ማቴ፡ ፫፡ ፲፩፡ ፲፪።። ዮሐ፡ ፩፡ ፳፮።።
፲፯፡ ማፍለሻው፡ በጁ፡ ይዞ፡ አውድማውን፡ በጣ
ም፡ ያጠራል፡ ስንዴውንም፡ በጎተራው፡ ያከማቻል፡
ገለባውን፡ ግን፡ በማይጠፋ፡ እሳት፡ ያቃጥለዋል።

፲፰፡ ሕዝቡንም፡ ያጽና፡ ነበረ፡ በሌላም፡ በብዙ፡ ነገ
ር፡ የምስራች፡ ይነግራቸው፡ ነበር።
፲፱፡ ሄሮድስ፡ ግን፡ ያራተኛው፡ ንጉሥ፡ ከርሱ፡ በገ
ሠፀ፡ ጊዜ፡ ስለ፡ ሄሮድያደ፡ ስለ፡ወንድሙ፡ ስለ፡ ፊል
ጶስ፡ ምሽት፡ ሄሮድስ፡ ያደረገውም፡ ስለ፡ ነበረ፡ ክፉ
ው፡ ነገር፡ ሁሉ። ማር፡ ፮፡ ፲፯፡ ፲፰።።
፳፡ ደግሞ፡ ይህነን፡ በሁሉ፡ ላይ፡ ጨመረ፡ ዮሐንስ
ን፡ በግዞት፡ እንደገዛው።
፳፩፡ ሕዝብ፡ ሁሉም፡ በተጠመቀ፡ ጊዜ፡ የሱስም፡
ደግሞ፡ ተጠመቀ። ሆነም፡ እርሱ፡ ሲጸልይ፡ ሰማይ፡
ተከፈተ። ማቴ፡ ፫፡ ፲፫—፲፯።። ማር፡ ፩፡ ፱—፲፩።።
፳፪፡ መንፈስ፡ ቅዱስም፡ በአካል፡ ምሳሌ፡ እንደ፡
ርግብ፡ ወረደበት፡ ድምፅም፡ ከሰማይ፡ መጣ፡ እንደ
ህ፡ ሲል። አንተ፡ ነህ፡ ልጁ፡ የምወድህ፡ ባንተ፡ ደስታ
ዬን፡ አያለሁ። *ም፡ ፱፡ ፴፭።። ፪፡ ጴጥ፡ ፩፡ ፲፯።።
፳፫፡ እርሱ፡ የሱስም፡ የሠላሳ፡ አመት፡ ሊሆነው፡
ጀመረ። የዮሴፍም፡ ልጅ፡ ይመስላቸው፡ ነበር። የኤ
ሊ፡ ልጅ። ም፡ ፬፡ ፳፪።።
፳፬፡ የማታት፡ልጅ፡የሌዊ፡ ልጅ። የመልኪ፡ ልጅ።
የያና፡ ልጅ። የዮሴፍ፡ ልጅ።
፳፭፡ የማጠትዩ፡ ልጅ። የአሞስ፡ ልጅ። የናሆም፡
ልጅ። የአስሊ፡ ልጅ። የናጌ፡ ልጅ።
፳፮፡ የማዓት፡ ልጅ። የማጣትዩ፡ ልጅ። የሰምዒ፡
ልጅ። የዮሴፍ፡ ልጅ። የይሁዳ፡ ልጅ።
፳፯፡ የዮና፡ ልጅ። የሬሳ፡ ልጅ። የዘሩባቤል፡ ልጅ።
የሰላትያል፡ ልጅ። የኔሪ፡ ልጅ።
፳፰፡ የመልኪ፡ልጅ። የአዲ፡ልጅ። የቆሳም፡ልጅ።
የኤልሞዳም፡ ልጅ። የኤር፡ ልጅ።
፳፱፡ የዮሴ፡ ልጅ። የአልዓዛር፡ ልጅ። የዮሪም፡ ል
ጅ። የማታት፡ ልጅ። የሌዊ፡ ልጅ።
፴፡ የስምዖን፡ልጅ። የይሁዳ፡ልጅ። የዮሴፍ፡ልጅ።
የዮናን፡ ልጅ። የኤልያቂም፡ ልጅ።
፴፩፡ የመሊያ፡ ልጅ። የማይናን፡ ልጅ። የማጣታ፡
ልጅ። *የናታን፡ ልጅ። የዳዊት፡ ልጅ።
*፪፡ ሳሙኤ፡ ፭፡ ፲፬።።
፴፪፡ *የእሴይ፡ ልጅ። የኦቦድ፡ ልጅ። የቦኤዝ፡
ልጅ። የሰልሞን፡ የነአሶን፡ ልጅ። *ሩት፡ ፬፡ ፲፰።።
፴፫፡ የአሚናዳብ፡ ልጅ። የአራም፡ ልጅ። የኤስሮ
ም፡ልጅ። የፋሬስ፡ልጅ። *የይሁዳ፡ልጅ።
*ዘፍ፡ ፳፱፡ ፴፭።።
፴፬፡ የያዕቆብ፡ ልጅ። የይስሐቅ፡ ልጅ። የአብርሃ
ም፡ ልጅ። የታራ፡ ልጅ። የናሆር፡ ልጅ።
ዘፍ፡ ፳፩፡ ፪፡ ፫።።
፴፭፡ የሳርቅ፡ ልጅ። የራጉ፡ ልጅ። የፋሌቅ፡ ልጅ።
የኤብር፡ ልጅ። የሳላ፡ ልጅ።
፴፮፡ የቃይናን፡ልጅ። የአርፋክሳድ፡ልጅ። የሴም፡
ልጅ። የኖህ፡ ልጅ፡ *የላሜክ፡ ልጅ።
*ዘፍ፡ ፭፡ ፫፡ ፴፪።።

፴፯፤ የማቱሳላ፡ ልጅ። የሄኖክ፡ ልጅ። የያሬድ፡ ል
ጅ። የመላልኤል፡ ልጅ። የቃይናን፡ ልጅ።
፴፰፤ የሄኖስ፡ልጅ፡ የሴት፡ ልጅ። የአደም፡ ልጅ።
የእግዚአብሔር፡ ልጅ። ዘፍ፡ ፭፤ ፩፡—፫።

ምዕራፍ፡ ፬፤

፩፤ የሱስ፡ ግን፡ መንፈስ፡ቅዱስ፡ መልቶበት፡ ከዮር
ዳኖስ፡ ተመለሰ፡ ከመንፈስም፡ወደ፡ ምድረ፡ በዳ፡ ተ
መርቶ፡ ሔደ። ማቴ፡ ፬፤ ፩፡—፲፩። ማር፡ ፩፤ ፲፪፤ ፲፫።
፪፤ አርባ፡ ቀንም፡ ከሰይጣን፡ ተፈትኖ፡ ምንም፡ አ
ልበላም፡ በዚያ፡ ወራት። በተፈጸመም፡ ጊዜ፡ ኋላ፡
ተራበ። ዘፀአ፡ ፴፬፤ ፳፰።
፫፤ ሰይጣንም፡ አለው። የእግዚአብሔር፡ ልጅስ፡
እንደ፡ ሆንህ፡ ይህነን፡ ደንጊያ፡ በል፡ እንጀራ፡ እንዲ
ሆን።
፬፤ የሱስም፡ መለሰለት፡ እንዲህ፡ ሲል። ተጽፎዋ
ል፡ ሰው፡ በንጀራ፡ ብቻ፡ እንደይድን፡ በእግዚአብሔ
ር፡ ነገር፡ ሁሉ፡ እንጂ። *ዘዳግ፡ ፰፤ ፫።
፭፤ ሰይጣንም፡ወደ፡ረጅም፡ ተራራ፡አወጣው። የ
ዓለሙንም፡ሁሉ፡ግዛት፡በዓይን፡ቅጽበት፡አሳየው።
፮፤ ሰይጣንም፡ አለው። ይህነን፡ ግዛት፡ ሁሉ፡ ላን
ተ፡ እሰጣለሁ፡ ክብሩንም። ለኔ፡ ተሰጥትዋልና፡ እኔ
ም፡ ለምወደው፡ እሰጣለሁ።
፯፤ አንተም፡በፊቴ፡ ብትሰግድ፡ ሁሉ፡ይሆንልሃል።
፰፤ የሱስም፡ መለሰ፡ አለውም። ወደ፡ ኋላዬ፡ ሒ
ድ፡አንተ፡ሰይጣን። *ተጽፎዋልና። ለእግዚአብሔር፡
ለአምላክህ፡ ስገድ፡ እርሱንም፡ ብቻ፡ አምልክ።
*ዘዳግ፡ ፲፤ ፲፪።
፱፤ ወደ፡ የሩሳሌምም፡ ይዞት፡ መጣ፡ በመቅደስ፡
በጫፉ፡ ላይ፡ አቆመው፡ አለውም። የእግዚአብ
ሔር፡ ልጅስ፡ እንደ፡ ሆንህ፡ ራስህን፡ ከዚህ፡ ወደ፡ ታ
ች፡ ወርውር።
፲፤ *ተጽፎዋልና፡መላእክቱን፡ስላንተ፡እንዲያዝ፡
ይጠብቁህ፡ ዘንድ። *መዝ፡ ፺፩፤ ፲፩፤ ፲፪።
፲፩፤ በእጃቸውም፡ ያነሡሃል፡ እግርህ፡ በደንጊያ፡
እንዳትሰናከል።
፲፪፤ የሱስም፡ መለሰ፡አለውም። ተብልዋልና። እ
ግዚአብሔር፡ አምላክህን፡ አትፈታተን።
*ዘዳግ፡ ፮፤ ፲፮።
፲፫፤ ሰይጣንም፡ ፈተናውን፡ ሁሉ፡ በፈጸመ፡ ጊዜ፡
ከርሱ፡ ቀረ፡ እስከ፡ *ጊዜው። ዮሐ፡ ፲፬፤ ፴።
*ዕብ፡ ፬፤ ፲፭።
፲፬፤ የሱስም፡ በመንፈስ፡ ቅዱስ፡ ኃይል፡ ወደ፡ ገሊ
ላ፡ ተመለሰ፡ ወሬውም፡ በዙርያው፡ ባሉቸው፡አገር፡
ሁሉ፡ ወጣ። ማቴ፡ ፬፤ ፲፪፡—፲፯። ማር፡ ፩፤ ፲፬፤ ፲፭።
፲፭፤ እርሱም፡ በጉባዔያቸው፡ ያስተምር፡ ነበረ፡ በ
ሁሉ፡ ዘንድ፡ ተመሰገነ።
፲፮፤ ወደ፡ ናዝሬትም፡ ወደደገበቱ፡ አገር፡ መጣ።
እንደ፡ ልማዱም፡ ቅዳሜ፡ ቀን፡ ወደ፡ ጉባዔያቸው፡
ገባ፡ ሊያነብም፡ ተነሣ። ማቴ፡ ፲፫፤ ፶፫።
ማር፡ ፮፤ ፩፡—፮።
፲፯፤ የነቢዩን፡የኢሳይያስንም፡መጽሐፍ፡ሰጡት።
መጽሐፉንም፡ በገለጸ፡ ጊዜ፡ የተጻፈበቱን፡ ስፍራ፡
አገኘ።
፲፰፤ የእግዚአብሔር፡ *መንፈስ፡ በላዬ፡ነው። እር
ሱ፡ ለድኆች፡ የምስራች፡ እነግር፡ ዘንድ፡ ስለ፡ ቀባኝ።
ልባቸው፡ የተሰበረትን፡ እፈውስ፡ ዘንድ፡ ላከኝ።
የታሠሩትን፡በመፈታት፡ ተስፋ፡ አስደርግ፡ ዘንድ፡ ዕ
ውሮችንም፡ በማየት። የተጋዙትን፡ እፈታ፡ ዘንድ፡
በማውፃት። *ኢሳ፡ ፷፩፤ ፩፤ ፪።
፲፱፤ የተቀበለች፡ በሆነችም፡ በእግዚአብሔር፡ አ
መት፡ አስተምር፡ ዘንድ። ዘሌዋ፡ ፳፭፤ ፲።
፳፤ ደግሞም፡ መጽሐፉን፡ አጠፈው፡ ለአገልጋዩ
ም፡ ሰጠው፡ ተቀመጠም። በጉባዔም፡ የነበሩ፡ ሁሉ፡
ዓይናቸው፡ ወደርሱ፡ ይመለከት፡ ነበር።
፳፩፤ እንዲህም፡ይላቸው፡ ጀመረ። ዛሬ፡ ይህ፡ መ
ጽሐፍ፡ በጆሮዋችሁ፡ ተፈጸመ።
፳፪፤ ሁሉም፡ ይመሰክሩለት፡ ነበሩ፡ ካፉ፡ ከሚወ
ጣውም፡ ከጸጋው፡ ነገር፡ የተነሣ፡ ይደነቁ፡ ነበሩ፡ ይሉ
ም፡ ነበሩ፡ ይህ፡ የዮሴፍ፡ ልጅ፡አይደለምን።
መዝ፡ ፵፭፤ ፫። ኢሳ፡ ፶፤ ፬።
፳፫፤ እርሱም፡ አላቸው። በውነት፡ ይህነን፡ ነገር፡
ትሉኛላችሁ። ባለ፡መድኃኒት፡ሆይ፡ራስህን፡ፈውስ።
*በከፍርናሆም፡ የሰራኸውን፡ እንደ፡ ሰማነው፡ በዚ
ህ፡ ባገርህ፡ ደግመህ፡ አድርገው። *ማቴ፡ ፬፤ ፲፫።
ዮሐ፡ ፯፤ ፵፪።
፳፬፤ አለም፡ እውነት፡ እላችኋለሁ፡ *ነቢይ፡ ባገሩ፡
የተቀበለ፡ እንደይደለ። *ዮሐ፡ ፬፤ ፵፬።
፳፭፤ ደግሞም፡ እውነት፡ እላችኋለሁ፡ እጅግ፡ ባ
ልቴቶች፡ በእሥራኤል፡ እንደ፡ ነበሩ፡ *በኤልያስ፡ ዘ
መን። ሰማይ፡ በተዘጋ፡ ጊዜ፡ ሶስት፡ አመት፡ ከስድስ
ት፡ ወር፡ ታላቅ፡ ራብ፡ በምድር፡ ሁሉ፡ እስኪሆን፡ ድ
ረስ። *፩፤ነገሥ፡ ፲፯፥፩፤ ፱። ፲፰፤ ፩፤ ፲።
፳፮፤ ኤልያስም፡ ከርሳቸው፡ ወደንዲት፡ አልተላ
ከም፡ የሲዶና፡ ወገን፡ ወደምትሆን፡ ወደ፡ ሰራጵታ፡
ወደ፡ መበለት፡ ቤት፡ በቀር።
፳፯፤ እጅግም፡ ለምጻሞች፡ በእሥራኤል፡ ነበሩ፡
በነቢዩ፡ በኤልሳእ፡ ዘመን። ከርሳቸውም፡ እንዲ፡ አ
ልነጻም፡ ከሶርያዊው፡ ከንዕማን፡ በቀር።
፪፤ ነገሥ፡ ፭፤ ፲፬።
፳፰፤ ሁሉም፡ ተቈጡ፡ በጉባዔ፡ ይህነን፡ በሰሙ፡
ጊዜ። የሐዋ፡ ፳፪፤ ፳፪።
፳፱፤ ተነሡም፡ ካገር፡ ወደ፡ ሜደም፡ አወጡት፡
ወደ፡ ተራራም፡ ደር፡ አመጡት፡ አገራቸው፡ ተሰርታ
በት፡ ወደ፡ ነበረችው፡ ገፍተው፡ ሊጥሉት።
፴፤ እርሱ፡ ግን፡ *በመካከላቸው፡ አልፎ፡ ሔደ።
*ዮሐ፡ ፰፤ ፶፱።

፴፩፤ ወደ፡ ቅፍርናሆም፡ ወደ፡ ገሊላ፡አገር፡ ወረደ፡ በሰንበትም፡ ያስተምራቸው፡ ነበር።

ማቴ፡ ፬፤ ፲፫፡—፲፯። ማር፡ ፩፤ ፳፩፤— ፳፪።

፴፪፤ ከትምህርቱም፡ *ተደነቁ። ነገሩ፡ በትእዛዝ፡ ነበርና። *ማቴ፡ ፯፤ ፳፰፤ ፳፱። ኤር፡ ፳፫፤ ፳፱። ዮሐ፡ ፯፤ ፵፮።

፴፫፤ በጉባኤም፡ ሰው፡ ነበረ፡ ርኩስ፡ ሰይጣን፡ ያደረበት። በታላቅ፡ ቃልም፡ ጮኸ።

፴፬፤ እንደዚህ፡ሲል። ተው፡በኛና፡ ባንተ፡ መካከል፡ ምን፡ አለ፡ የሱስ፡ ሆይ፡ የናዝሬቱ። ልታጠፋነን፡ መጣህ። ፈጽሚ፡ አወቅሁ፡ አንተ፡ ማነህ፡ የእግዚአብሔር፡ ቅዱስ፡ ሆይ።

፴፭፤ የሱስም፡ ገሠፀው፡ እንደዚህ፡ ሲል። ዝምበል፡ ከርሱም፡ ወጣ፡ አልጐዳውምም።

፴፮፤ በሁሉም፡ ድንጋጤ፡ሆነ፡እርሱ፡ በርሳቸውም፡ ይጫወቱ፡ ነበሩ፡ እንደዚህ፡ሲሉ። ይህ፡ ነገር፡ ምንድር፡ ነው። በትእዛዝ፡ በኀይልም፡ አጋንንትን፡ ርኩሳንን፡ ያዛልና፡ ይወጡማል። ፩፤ ጴጥ፡ ፫፤ ፳፪።

፴፯፤ ወሬውም፡ ወጣ፡ በዙርያው፡ አገር፡ ስፍራ፡ ሁሉ።

፴፰፤ ከጉባኤውም፡ ተነሥቶ፡ ወደ፡ ሲሞን፡ ቤት፡ ገባ። የሲሞንም፡ የምሽቱ፡ እናት፡በብርቱ፡ ንደድ፡ ታማ፡ ነበረች፡ ስለርስዋም፡ ለመኑት።

ማቴ፡ ፰፤ ፲፬፡—፲፯። ማር፡ ፩፤ ፳፱፡—፴፪።

፴፱፤ ወደርስዋም፡ ቀመ፡ ደዌዋንም፡ ገሠፀው፡ ተዋትም፡ የዚያን፡ ጊዜውንም፡ ተነሣች፡ ታገለግላቸውም፡ ነበረች። ምዕ፡ ፲፤ ፵። ማቴ፡ ፰፤ ፲፭፤ ፲፯።

፵፤ ጸሐይም፡ በገባች፡ ጊዜ፡ ልዩ፡ ልዩ፡ ደዌ፡ ያለባቸውን፡ ድውያን፡ወደርሱ፡አመጡ። እርሱም፡ ከርሳቸው፡ በያንዳንዱ፡ እጁን፡ ኢየጫነ፡ ይፈውሳቸው፡ ነበረ።

፵፩፤ ሰይጣናትም፡ ደግሞ፡ ከብዙ፡ ይወጡ፡ ነበር፡ ይጮኹም፡ ይሉም፡ ነበሩ። አንተ፡ክርስቶስ፡ ነህ፡ የእግዚአብሔር፡ልጅ። ይቈጣቸውም፡ ነበር፡ይናገሩም፡ ዘንድ፡ አልተዋቸውም፡ እርሱ፡ ክርስቶስ፡እንደ፡ሆነ፡ አውቀዋልና። ማቴ፡ ፰፤ ፳፱። ማር፡ ፫፤ ፲፪።

፵፪፤ ቀንም፡ በሆነ፡ ጊዜ፡ ወጣ፡ ወደ፡ ምድረ፡ በደም፡ ሔደ። አሕዛብም፡ ይሹት፡ ነበሩ፡ ወደርሱም፡ መጡ፡ ከርሳቸውም፡ እንዳይሔድ፡ ያዙት።

፵፫፤ እርሱ፡ ግን፡ አላቸው። የቀሩትን፡ አገሮች፡ በእግዚአብሔር፡ መንግሥት፡ አስተምር፡ ዘንድ፡ ይገባኛልና፡ለዚህ፡ተልኪያለሁና። ቈ፡ ፲፰፤ ፳። ም፡ ፰፤ ፩።

፵፬፤ በገሊላም፡ መስጊዶች፡ ይሰብክ፡ ነበረ።

ቈ፡ ፲፭።

ምዕራፍ፡ ፭፤

፩፤ ብዙ፡ሰዎችም፡ወደርሱ፡ በተከማቹ፡ ጊዜ፡ የእግዚአብሔርን፡ ነገር፡ ይሰሙ፡ ዘንድ። እርሱ፡ በጌንሳሬጥ፡ ባሕር፡ አጠገብ፡ ቁሞ፡ ነበረ።

ማቴ፡ ፬፤ ፲፰፡—፳፪። ማር፡ ፩፤ ፲፯፡—፲፰።

፪፤ ሁለት፡ ታንኮችም፡ አየ፡በባሕር፡ዳር፡ ቁመው። አጥማጆችም፡ ከርሳቸው፡ ወጡ፡ መርበብታቸውን፡ ሊያጥቡ።

፫፤ ለሲሞንም፡ ወደ፡ ነበረችው፡ ወደንዲቱ፡ ወጥቶ፡ ተቀመጠ፡ ከምድርም፡ጥቂት፡ ፈቀቅ፡ ያደርጋት፡ ዘንድ፡ ለመነው። አሕዛብንም፡ ያስተምር፡ ነበረ፡ በመርከብ፡ ተቀመጦ።

፬፤ ነገሩንም፡ በፈጸመ፡ ጊዜ፡ ሲሞንን፡ አለው። ወደ፡ ጥልቁ፡ ቅረብ፡ መርበብታችሁንም፡ ለማጽመድ፡ ጣሉ። ዮሐ፡ ፳፩፤ ፯።

፭፤ ሲሞንም፡ መለሰ፡ አለው። መምህር፡ሆይ፡ ሌቱን፡ ሁሉ፡ ፈጽመን፡ ደከምነ፡ምንም፡ አልያዝነም። ነገር፡ ግን፡ በነገርህ፡ መርበብቱን፡ እጥላለሁ።

መዝ፡ ፻፳፯፤ ፩፤ ፪።

፮፤ ይህነንም፡ ባደረጉ፡ ጊዜ፡ ካሣው፡ እጅግ፡ ብዙ፡ ወሰደ። መርበብታቸውም፡ ለመቀደድ፡ ቀረበች።

፯፤ ባልንጀሮቻቸውንም፡ በሌላ፡ ታንኳ፡ የነበሩትን፡ ጠቀሱ፡ ያግዝዋቸው፡ ዘንድ። መጡም፡ ሁለቱንም፡ መርከቦች፡ መሉ፡ እስኪሠጥሙ፡ ድረስ።

ቈ፡ ፲።

፰፤ ሲሞን፡ ጴጥሮስም፡ያነን፡ባየ፡ ጊዜ፡ በየሱስ፡ ጕልበት፡ ላይ፡ ወደቀ፡ እንደዚህ፡ ሲል። ከኔ፡ ራቅ፡ ጌታ፡ ሆይ፡ እኔ፡ ኃጢአተኛ፡ ሰው፡ ነኝና።

፱፤ መደነቅ፡ ስላስደነገጠው፡ ከርሱም፡ ጋራ፡የነበሩትን፡ ሁሉ፡ ስለ፡ ጸመዲት፡ ዓሣ።

፲፤ እንደሁም፡ ደግሞ፡ያዕቆብንና፡ ዮሐንስን፡ የዘብዴዎስን፡ ልጆች፡ የሲሞን፡ አንጋሮች፡ የነበሩ። የሱስም፡ ሲሞንን፡ አለው። አትፍራ። ከንግዲህ፡ ወዲህ፡ *ሰው፡ የምታጸምድ፡ትሆናለህ። *ኤር፡ ፲፯፤ ፲፮።

ማቴ፡ ፲፫፤ ፵፯።

፲፩፤ መርከቢቱንም፡ ወደ፡ ምድር፡ ጕተቱ፡ ሁሉንም፡ *ትተው፡ ተከተሉት። *ማቴ፡ ፲፱፤ ፳፯።

፲፪፤ ተደረገም፡ ባንድ፡ አገር፡ በተቀመጠ፡ ጊዜ፡ እነሆ፡ ሰው፡ ለምጽ፡ የመላበት፡ ነበረ። የሱስንም፡ ባየው፡ ጊዜ፡ በግምባሩ፡ ተደፋ፡ እንደዚህ፡ ሲል። አቤቱ፡ ብትወድስ፡ ትችላለህ፡ ታነጻኝ፡ ዘንድ።

ማቴ፡ ፰፤ ፩፡—፬። ማር፡ ፩፤ ፵፡—፵፭።

፲፫፤ የሱስም፡ እጁን፡ ዘረጋና፡ ዳሰሰው፡ እንደዚህ፡ ሲል። ወደድሁ፡ንጻ። የዚያን፡ ጊዜውም፡ ለምጹ፡ ከርሱ፡ ሔደ።

፲፬፤ እርሱም፡ አዘዘው፡ ለማንም፡ እንዳይናገር። ነገር፡ ግን፡ ሒድ፡ ራስህን፡ ለካህን፡ አስፈትን፡ ስለ፡ነጻህም፡ አቅርብ፡ *ሙሴ፡ እንደዘዘ፡ ምስክር፡ ሊሆንባቸው። *ዘሌዋ፡ ፲፬፤ ፪።

፲፭፤ ወሬውም፡ ስለርሱ፡ እጅግ፡ ወጣ፡ ብዙ፡ አሕዛብም፡ ወደርሱ፡ ተሰበሰቡ፡ ከርሱ፡ ሊሰሙ፡ ከደዌያቸውም፡ ሊፈወሱ።

፲፮፡ እርሱ፡ ግን፡ወደ፡ *ምድረ፡ በደ፡ ፈቀቅ፡ ብሎ፡ ይጸልይ፡ ነበረ። *ማር፡ ፩፡ ፴፭።

፲፯፡ ሆነም፡ ባንድ፡ ቀን፡ እርሱ፡ ሲያስተምር፡ፈሪሳውያን፡ የኦሪትም፡መምህሮች፡ ከገሊላ፡ አገር፡ ሁሉ፡ ከይሁደም፡ከየሩሳሌምም፡የመጡ፡ከዚያ፡ ተቀምጠው፡ ነበሩ፡ የእግዚአብሔር፡ *ኃይልም፡ለመፈወሳቸው፡ ነበረች። ም፡ ፱፡ ፩—፰። ማር፡ ፪፡ ፩—፲፪። *ም፡ ፮፡ ፲፱።

፲፰፡ እነሆ፡ ሰዎችም፡አንድ፡ ሰው፡ መፃጉ፡ ባልጋ፡ ላይ፡ አመጡ፡አግብተውም፡በፊቱ፡ሊያኖሩት፡ ይሹ፡ ነበር።

፲፱፡ ባለገኙም፡ ጊዜ፡ እንዲት፡ ይዘውት፡ ይገቡ፡ ዘንድ፡ ስለ፡ ሰው፡ ብዛት፡ ወደ፡ሰገነቱ፡ ወጡ፡በጡብና፡ በጡብ፡ መካከልም፡ አወረዱት፡ ካልጋው፡ ጋራ፡ በየሱስ፡ ፊትም፡ አኖሩት።

፳፡ ሃይማኖታቸውንም፡ባየ፡ጊዜ፡አለው። አንተ፡ ሰው፡ ኃጢአትህ፡ ተሰረየችልህ። ም፡ ፯፡ ፵፰።

፳፩፡ ጻፎችም፡ ፈሪሳውያንም፡ ያስቡ፡ ጀመሩ፡ እንዲህ፡ ሲሉ። ማነው፡ እርሱ፡ ኢየተሳደበ፡የሚናገር። ማን፡ይችላል፡ኃጢአት፡ ይሰርይ፡ዘንድ፡ ካንዱ፡ ከእግዚአብሔር፡በቀር። ኢሳ፡ ፵፫፡ ፳፭።

፳፪፡ የሱስም፡ አሳባቸውን፡ ባወቀ፡ ጊዜ፡ መለሰ፡ አላቸውም። ምን፡ ታስባላችሁ፡ በልባችሁ።

፳፫፡ ማናቸው፡ ይቀል፡ ኃጢአትህ፡ ተሰረየችልህ፡ ማለትን። ወይስ፡ ተነሣና፡ ሒድ።

፳፬፡ ነገር፡ ግን፡ ታውቁ፡ ዘንድ፡ ለሰው፡ ልጅ፡ ስልጣን፡ እንደለው፡ በምድር፡ ላይ፡ ኃጢአት፡ ይሰርይ፡ ዘንድ (ድውዩን፡ አለው)። አንተን፡ እላለሁ። ተነሣ፡ አልጋህንም፡ አንሣ፡ ወደ፡ ቤትህም፡ ሒድ።

፳፭፡ የዚያን፡ ጊዜውንም፡ በፊታቸው፡ ተነሣ፡ ተኝቶበት፡ የነበረውንም፡ ተሸከመ፡ ወደ፡ ቤቱም፡ ሔደ፡ እግዚአብሔርን፡ ኢያመሰገነ።

፳፮፡ ሁሉንም፡ ድንጋጼ፡ ያዛቸው፡ እግዚአብሔርንም፡ አመሰገኑ፡እጅግም፡ፈሩ፡ እንዲህ፡ ሲሉ። ዛሬ፡ ድንቅ፡ ነገር፡ አየነ።

፳፯፡ ከዚህም፡ በኋላ፡ወጣ፡ቀራጭም፡ አየ፡ ስሙን፡ ሌዊ፡ የሚሉት፡ በቀረጥ፡ ላይ፡ተቀምጦ። አለውም፡ ተከተለኝ። ማቴ፡ ፱፡ ፱—፲፫። ማር፡ ፪፡ ፲፫—፲፯።

፳፰፡ ሁሉንም፡ ትቶ፡ ተነሥቶም፡ ተከተለው።

፳፱፡ ሌዊም፡ ታላቅ፡ ምሳ፡ አደረገለት፡በቤቱ። ከቀራጮችም፡ እጅግ፡ ሰዎች፡ ነበሩ፡ ሌሎችም፡ከርሳቸው፡ ጋራ፡ ለምሳ፡ ጥቀምጠው፡ የነበሩ። ም፡ ፲፭፡ ፩።

፴፡ ጻፎቻቸውም፡ፈሪሳውያንም፡በደቀ፡መዛሙርቱ፡ ላይ፡ እንዲህ፡ ሲሉ፡ አንጐረጐሩ። ለምን፡ ከቀራጮችና፡ ከኃጢአተኞች፡ ጋራ፡ ትበላላችሁ፡ ትጠጡም፡ አላችሁ።

፴፩፡ የሱስም፡መለሰ፡ አላቸውም። ባለ፡ ጤናች፡ ባለ፡ መድኃኒት፡አይሹም፡ድውያን፡ እንጂ።

፴፪፡ ጻድቃንን፡ ልጸራ፡ አልመጣሁም። ነገር፡ ግን፡ ኃጢአተኞችን፡ ወደ፡ ንስሐ። ም፡ ፲፭፡ ፯፡ ፲።

፴፫፡ እርሳቸውም፡ አሉት። ምነው፡የዮሐንስ፡ ደቀ፡ መዛሙርት፡ እጅግ፡ ይጾማሉ፡ ጸሎትም፡ ያደርጋሉ። እንደዚሁም፡ የፈሪሳውያን፡ደቀ፡ መዛሙርት። ደቀ፡ መዛሙርትህ፡ ግን፡ ይበላሉ፡ ይጠጣሉም። ማቴ፡ ፱፡ ፲፬—፲፯። ማር፡ ፪፡ ፲፰—፳፪።

፴፬፡ እርሱ፡ ግን፡ መለሰ፡ አላቸውም። ትችላላችሁን፡ በሙሽራ፡ ጉርጂ፡ ያሉን፡ ሚዜዮች፡ ሙሽራ፡ ከርሳቸው፡ ጋራ፡ ሳለ፡ ታስጦሙ፡ ዘንድ።

፴፭፡ ወራትም፡ ይመጣል፡ ሙሽራ፡ ከርሳቸው፡ በተለየ፡ጊዜ። ከዚያ፡በኋላ፡ ይጾማሉ፡በዚያች፡ወራት።

፴፮፡ ደግሞም፡ምሳሌ፡ ይላቸው፡ ነበረ። ማንም፡ ያዲስ፡ ልብስ፡ ቍራጭ፡ ባርጌ፡ ልብስ፡ ላይ፡ አይጥፍም። ያለዚያስ፡ አዲሱ፡ ይቀደዋል፡ አዲሱም፡ ቍራጭ፡ ላርጌው፡ አይሰማማም።

፴፯፡ አዲስ፡ ፀጅም፡ ዓርጌ፡ አቀማደ፡ የሚያደርግ፡ የለም። ያለዚያስ፡ አዲሱ፡ ፀጅ፡አቀማደውን፡ይቀደል። እርሱም፡ይፈሳል፡ አቀማደውን፡ ይጠፋል።

፴፰፡ ነገር፡ ግን፡ አዲስ፡ ፀጅ፡ ባዲስ፡ አቀማደ፡ ይደረጋል፡ እርሱ፡ በርሳቸውም፡ ይጠባበቃሉ።

፴፱፡ ማነው፡ የከረመ፡ ፀጅ፡ ጠጥቶ፡ የዚያን፡ ጊዜውን፡ አዲስ፡ የሚሻ። የከረመው፡ ይጣፍጣል፡ ይላልና።

ምዕራፍ፡ ፮፡

፩፡ ሆነም፡ በሁለተኛው፡ሰንበት፡ እርሱ፡ በርሻ፡መካከል፡ ሲያልፍ፡ ደቀ፡ መዛሙርቱ፡ እሸት፡ ኢየቀጠፉ፡ በጆቻቸውም፡ ኢያሹ፡ ይበሉ፡ ነበረ። ማቴ፡ ፲፪፡ ፩—፰። ማር፡ ፪፡ ፳፫፡ ፳፰።

፪፡ ከፈሪሳውያንም፡ ሰዎች፡አልዋቸው። ለምን፡ ታደርጋላችሁ፡ ማደርጉ፡ የማይገባውን፡ በሰንበት። ዘፀአ፡ ፳፡ ፱—፲፪።

፫፡ የሱስም፡ መለሰላቸው፡ አለም። ይህነን፡ ስንኳ፡ አላነበባችሁምን፡ *ዳዊት፡ ያደረገውን፡ እርሱ፡ በተራበ፡ ጊዜ፡ ከርሱም፡ ጋራ፡ የነበሩ። *፩፡ ሳሙኤ፡ ፳፩፡ ፮።

፬፡ ወደ፡ እግዚአብሔር፡ ቤት፡ እንደ፡ ገባ፡ የመሥዋዕቱንም፡ እንጀራ፡ ውስደ፡ እንደ፡ በላው፡ ከርሱም፡ ጋራ፡ ላሉት፡ ሰጠ። ሙብሉ፡ የማይገባውን፡ ለካህናት፡ ብቻ፡ እንጅ። ዘሌዋ፡ ፳፬፡ ፳፡ ፱።

፭፡ አላቸውም። የሰንበት፡ ጌታ፡ ደግሞ፡ የሰው፡ ልጅ፡ ነው።

፮፡ ሆነም፡ ደግሞ፡ በሌላው፡ ሰንበት፡ ወደ፡ ጉባኤ፡ ገብቶ፡ አስተማረ። ከዚያም፡ ሰው፡ ነበረ፡ ቀኝ፡ እጁም፡ ደርቃ፡ ነበረች። ማቴ፡ ፲፪፡ ፱—፲፬። ማር፡ ፫፡ ፩—፮።

፯፡ ጻፎችም፡ ፈሪሳውያንም፡ *ያደቡ፡ ነበረ፡ በሰንበት፡ያድነው፡ እንደሆን፡ የሚያጸሉበት፡ ምክንያት፡ ሊያገኙ። *ም፡ ፲፬፡ ፩።

፰፡ እርሱ፡ ግን፡ አሳባቸውን፡ ያውቅ፡ ነበር። እጁ፡ የደረቀውንም፡ ሰው፡ አለው። ተነሣ፡በመካከልም፡ ቁም። እርሱም፡ ተነሥ፡ ቀመም። ም፡ ፭፡ ፳፪፡፡

፱፡ የሱስም፡ አላቸው። እጠይቃችኋለሁ፡ ምን፡ ይገባል፡ በሰንበት፡ ይደረግ፡ዘንድ። መልካምን፡ ወይስ፡ ክፋ። ነፍስ፡ ትድንን፡ ወይስ፡ ትሙት።

፲፡ ወደርሳቸውም፡ ሁሉ፡ ዙሮ፡ ባየ፡ ጊዜ፡ ሰውን፡ አለው፡እጅህን፡ዘርጋ። እርሱም፡ እንደሁ፡ አደረገ። እጁም፡ ደህና፡ ሁና፡ ሰለች፡ እንደ፡ ሁለተኛዋ። ፩፡ ነገሥ፡ ፲፫፡ ፮፡፡

፲፩፡ እርሳቸው፡ ግን፡ እጅግ፡አበዱ፡እርሱ፡ በርሳቸው፡ ተናገሩ፡ በየሱስ፡ ምን፡ እንዲያደርጉበት።

፲፪፡ ሆነም፡ በዚያች፡ ወራት፡ ወደ፡ ተራራ፡ ወጣ፡ ይጸልይ፡ ዘንድ። በእግዚአብሔር፡ ጸሎትም፡ተግተ፡ ነበረ፡ ሌቱን፡ ሁሉ። ማቴ፡ ፲፬፡ ፳፫፡፡ ማር፡ ፫፡ ፲፫—፲፱፡፡

፲፫፡ ቀንም፡ በሆነ፡ጊዜ፡ ደቀ፡ መዛሙርቱ፡ጸራ፡ ከርሳቸውም፡ አሠራ፡ ሁለት፡ መረጸ፡ ሐዋርያት፡ ደግሞ፡ ያላቸውን። ማቴ፡ ፲፡ ፩፡፡

፲፬፡ እርሳቸውም፡ ሲሞን፡ ደግሞ፡ ጴጥሮስ፡ ያለው፡ እንድርያስም፡ ወንድሙ። ያዕቆብና፡ ዮሐንስ፡ ፊልጶስና፡ በርተሎሜዎስ።

፲፭፡ ማቴዎስና፡ ቶማስ። ያዕቆብ፡ የእልፍዮስ፡ ልጅ፡ ሲሞንም፡ ቀናዒ፡ የሚባለው።

፲፮፡ ይሁዳ፡ የያዕቆብ፡ ወንድም፡ ይሁዳም፡ የአስቆሮቱ፡ ደግሞ፡ አሰያዡ፡ የሆነው።

፲፯፡ ከርሳቸውም፡ ጋራ፡ ወረደ፡ በሰፌ፡ ቦታም፡ ቆመ። ደቀ፡ መዛሙርቱም፡ ተሰበሰቡ፡ ከሕዝቡም፡ ብዙ፡ ሰዎች፡ ከይሁዳ፡ ሁሉ፡ ከየሩሳሌምም፡ ከጢሮስና፡ ከሲዶና፡ ደርም፡ የመጡ፡ ሊሰሙት፡ ከደዌያቸውም፡ ሊፈወሱ። ማር፡ ፫፡ ፯—፲፡፡

፲፰፡ ከርኩሳን፡ መናፍስትም፡ ይሣቀዩ፡ የነበሩ። ይፈወሱም፡ ነበሩ። ማቴ፡ ፬፡ ፳፭፡፡

፲፱፡ ሕዝብ፡ሁሉ፡ ሊደሱት፡ ይሹ፡ነበሩ። ኃይል፡ ከርሱ፡ ትወጣ፡ ነበረችና፡ ሁሉንም፡ ፈወሰች።

፳፡ እርሱ፡ ግን፡ ወደ፡ ደቀ፡ መዛሙርቱ፡ ዓይኑን፡ አነሣ፡ አለም። ብፁዓን፡ ናችሁ፡ እላንት፡ ድኆች። የእግዚአብሔር፡ መንግሥት፡ የላንት፡ ነውና። ማቴ፡ ፭፡ ፫—፵፰፡፡

፳፩፡ ብፁዓን፡ናችሁ፡የተራባችሁ፡ ዛሬ። ትጸግባላችሁና። ብፁዓን፡ ናችሁ፡ እላንት፡ዛሬ፡የምታለቅሱ፡ ትስቃላችሁና። ራእ፡ ፯፡ ፲፮፡፡ መዝ፡ ፻፳፮፡ ፭፡ ፯፡፡ ኢሳ፡ ፷፩፡ ፫፡፡

፳፪፡ ብፁዓን፡ናችሁ፡ሰዎች፡ቢጸልዋችሁ፡ በለይዋችሁና፡ ባሳደድዋችሁ፡ በተላገድዋችሁም፡ጊዜ፡ስማችሁንም፡ እንደ፡ ክፋ፡ባወጡ፡ጊዜ፡ ስለ፡ ሰው፡ ልጅ። ዮሐ፡ ፲፮፡ ፪፡፡

፳፫፡ ደስ፡ ይበላችሁ፡ በዚያ፡ ቀን፡ሐሤትም፡አድርጉ። እነሆ፡ ዋጋችሁ፡ በሰማይ፡እጅግ፡ ነውና። እንደሁ፡ አባቶቻቸው፡ በነቢያት፡ ያደርጉ፡ ነበሩና። ማቴ፡ ፳፫፡ ፴፬፡፡

፳፬፡ ነገር፡ ግን፡ ወዮላችሁ፡እላንት፡ ባለጠጎች። ደስታችሁን፡ ወስዳችኋልና። ያዕ፡ ፭፡ ፩—፭፡፡

፳፭፡ ወዮላችሁ፡ እላንት፡ ጽጋበኞች፡ ትራባላችሁና። ወዮላችሁ፡እላንት፡ ዛሬ፡ የምትስቁ፡ ታለቅሳላችሁና። ኢሳ፡ ፭፡ ፳፪፡፡ ፷፭፡ ፲፫፡፡ ያዕ፡ ፬፡ ፱፡፡

፳፮፡ ወዮላችሁ፡ ሰው፡ሁሉ፡መልካም፡ ቢናገርላችሁ። አባቶቻቸው፡ ባሰቀኞች፡ ነቢያት፡ እንደሁ፡ አድርገዋልና። ሚክ፡ ፪፡ ፲፩፡፡ ያዕ፡ ፬፡ ፬፡፡

፳፯፡ ነገር፡ግን፡እላችኋለሁ፡እላንት፡የምትሰሙ። ጸላቶቻችሁን፡ውደዱ። ለሚጠልዋችሁ፡ መልካም፡ አድርጉ። ዘፀአ፡ ፳፫፡ ፬፡፡

፳፰፡ የሚረግምዋችሁን፡ መርቁ። ስለሚበድልዋችሁም፡ ጸልዩ። ም፡ ፳፫፡ ፴፬፡፡

፳፱፡ ፊትህን፡ለጸፋህ፡ሁለተኛውን፡ መልስለት። መጐናጸፊያህንም፡ ለወሰደ፡ቀሚስህንም፡ ደግሞ፡ አትንሣው።

፴፡ ለለመነህ፡ ሁሉ፡ስጥ። ከብትህንም፡የሚወስድ፡ ከርሱ፡ አትሻው። ዘዳግ፡ ፲፭፡ ፯፡ ፰፡፡

፴፩፡ ሰውም፡ ሊያደርግላችሁ፡ እንድትወዱ፡ እላንትም፡ እንደሁ፡ አድርጉላቸው። ማቴ፡ ፯፡ ፲፪፡፡

፴፪፡ የሚወድዋችሁንም፡ የምትወዱ፡ ከሆናችሁ፡ ምን፡ ጸጋ፡ አላችሁ። ኃጢአተኞች፡ ደግሞ፡ የሚወድዋቸውን፡ ይወዳሉና።

፴፫፡ መልካም፡ የሚያደርግላችሁስ፡ መልካም፡ ብታርጉ፡ ምን፡ ምስጋና፡ አላችሁ። ኃጢአተኞች፡ ደግሞ፡ እንደሁ፡ ያደርጋሉና።

፴፬፡ የምታበድሩም፡ ብትሆኑ፡ ተስፋ፡ለምታደርጉዋቸው፡ እንደ፡ መልሱላችሁ። ምን፡ ጸጋ፡ አላችሁ። ኃጢአተኞች፡ ደግሞ፡ ለኃጢአተኞች፡ ያበድራሉና፡ ያበደሩትን፡ ሊወስዱ። ዘሌዋ፡ ፳፭፡ ፴፭፡ ፴፮፡፡

፴፭፡ ነገር፡ ግን፡ጸላቶቻችሁን፡ውደዱ። መጽውቱም፡ አበድሩም፡ ምንም፡ ተስፋ፡ ሳታደርጉ። ዋጋችሁም፡እጅግ፡ ይሆናል፡ የልዑልም፡ ልጆች፡ትሆናላችሁ። እርሱ፡ በማያመሰግኑ፡ በክፉችም፡ ቸር፡ ነውና።

፴፮፡እንግዲህ፡የምትራሩ፡ሁኑ፡አባታችሁ፡ደግሞ፡ የሚራራ፡እንደ፡ ሆነ። ማቴ፡ ፯፡ ፪፡፡ ማር፡ ፬፡ ፳፬፡፡

፴፯፡ አትፍረዱም፡ አይፈረድባችሁምም። አትኰንኑ፡አትኰነኑምም። ተው፡ እንደሁም፡ ይተውላችኋል። ሮሜ፡ ፲፬፡ ፬፡ ፲፡፡ ማቴ፡ ፮፡ ፲፬፡፡ ፯፡ ፩፡፡

፴፰፡ ስጡ፡ ይሰጣችሁማል። መልካም፡ የተጨቋቍነ፡ የተነቀነቀ፡ የተረፈረፈም፡ መስፈርያ፡ በብብታችሁ፡ ይሰጣችኋል። በምትሰፍሩት፡ መስፈርያ፡ ይሰፈርላችኋልና። ማቴ፡ ፯፡ ፪፡፡ ማር፡ ፬፡ ፳፬፡፡

፴፱፡ ምሳሌም፡ነገራቸው። ዕውር፡ ዕውርን፡ ሊመራ፡ ይችላልን። ሁለቱ፡ በገደል፡ አይወድቁምን። ማቴ፡ ፲፭፡ ፲፬፡፡

፵፡ ደቀ፡ መዝሙር፡ከመምህሩ፡የሚበልጥ፡ አይ ደለም፡ ፍጹም፡ ሁሉ፡ ግን፡ እንደ፡ መምህር፡ ይሆና ል። ማቴ፡ ፲፡ ፳፬፡ ፳፭። ዮሐ፡ ፲፭፡ ፳።
፵፩፡ ለምንስ፡ ታያለህ፡ በወንድምህ፡ ዓይን፡ ያለ ውን፡ ስንጣቂ። ባይንህ፡ ያለውንም፡ ግንድ፡ አታስተ ውለውም። ማቴ፡ ፯።
፵፪፡ ወይስ፡ እንዴት፡ ትቾላለህ፡ ወንድምህን፡ ት ለው፡ ዘንድ። ወንድሜ፡ ሆይ፡ ተወኝ፡ ስንጣቂውን፡ ካይንህ፡ላውጣ። አንተም፡ባይንህ፡ያለውን፡ ግንድ፡ አታይም። አንተ፡ ግብዝ፡ አስቀድመህ፡ የዓይንህን፡ ግንድ፡ አውጣ፡ ከዚያ፡ ወዲያም፡ ታያለህ፡ በወንድ ምህ፡ ዓይን፡ ያለውን፡ ስንጣቂ፡ ታወጣ፡ ዘንድ።
፵፫፡ መልካም፡ ዛፍ፡ ክፉ፡ ፍሬ፡ አታወጣምና። ክፉም፡ ዛፍ፡ መልካም፡ ፍሬ፡ አታፈራም። ማቴ፡ ፲፪፡ ፴፫፡ ፴፬።
፵፬፡ ዛፍ፡ ሁሉ፡ ከፍሬው፡ ይታወቃልና። ከሾህ፡ በለስ፡ አይለቀምምና፡ ከአጣጥም፡ ቍጥቋጦ፡ ወይ ን፡ አይቈረጥምና።
፵፭፡ ቸር፡ ሰው፡ ከቸር፡ ልቡ፡ መዝገብ፡ ቸርነት፡ ያ ወጣል። ክፉ፡ሰውም፡ከክፉ፡ ልቡ፡መዝገብ፡ ክፋት፡ ያውጣል፡ አፉ፡ ከልቡ፡ ምላት፡ ይናገራልና።
፵፮፡ ለምንስ፡ትሉኛላችሁ፡አቤቱ፡አቤቱ። የምለ ውንም፡ አታደርጉም። ሚልክ፡ ፩፡ ፮። ማቴ፡ ፳፭፡ ፲፩፡ ፲፪።
፵፯፡ ወደኔ፡ የሚመጣ፡ ሁሉ፡ ነገሬንም፡ የሚሰ ማ፡ የሚያደርገውም፡ አሳያችኋለሁ፡ ማንን፡ እንደ ሚመስል።
፵፰፡ ቤት፡ የሰራን፡ ሰው፡ ይመስላል፡ እርሱም፡ ቈፈረ፡ አጠለቀም፡ መሠረቱንም፡ በሕንፃ፡ ላይ፡አ ደረገ። ጕርፉም፡ በመጣ፡ ጊዜ፡ ፈሳሹ፡ ያነን፡ ቤት፡ መታው፡ ሊያንቀሳቅሰውም፡ አልቻለም፡ በሕንፃ፡ ላይ፡ ተመሥርትዋልና።
፵፱፡ የሚሰማም፡ የማያደርገውም፡ ቤቱን፡ ያለ፡ መሠረት፡ በምድር፡ ላይ፡ የሰራ፡ሰው፡ ይመስላል። ፈ ሳሹም፡ በገፋው፡ ጊዜ፡ የዚያን፡ጊዜውን፡ ወደቀ። የ ዚያ፡ ቤት፡ መፍረሱም፡ ታላቅ፡ ሆነ።

## ምዕራፍ፡ ፯፡

፩፡ ነገሩንም፡ ሁሉ፡ በሕዝቡ፡ ጆሮ፡ በፈጸመ፡ ጊዜ፡ ወደ፡ ቅፍርናሆም፡ ገባ። ማቴ፡ ፰፡ ፭፡—፲፫።
፪፡ ያንዱ፡ የመቶ፡ አለቃም፡ ባርያ፡ ለርሱ፡ ውድ፡ የነበረ፡ ታመመ፡ ሊሞትም፡ ቀረበ።
፫፡ የየሱስንም፡ ወሬ፡ በሰማ፡ ጊዜ፡ የአይሁድን፡ ሽማግሎች፡ ወደርሱ፡ላከ፡ መጥቶ፡ ባርያውን፡ እንዲ ያድን፡ ይለምኑት፡ ዘንድ።
፬፡ እርሳቸውም፡ በመጡ፡ ጊዜ፡ አጽንተው፡ ወደ፡ የሱስ፡ ለመኑት፡ እንደህ፡ ሲሉ። ይህነን፡ታደርግለት፡ ዘንድ፡ ይገባዋልና።
፭፡ ወገናችነን፡ይወዳልና፡የጸሎት፡ቤትም፡ሰራልነ።
፮፡ የሱስም፡ ከርሳቸው፡ ጋራ፡ ሔደ። እርሱም፡ ከ ቤት፡ ሳይርቅ፡ የመቶው፡ አለቃ፡ወዳጆቹን፡ ላከበት፡ እንዲህ፡ ሲል። አቤቱ፡ አድከም። *አይገባኝምና፡ ት ገባ፡ ዘንድ፡ ከጠፈሬ፡ በታች። ም፡ ፲፭፡ ፲፱።
*ዘፍ.ጥ፡ ፴፪፡ ፲።
፯፡ ስለዚህም፡ ስውነቴን፡ አልቈጠርሁም፡ እንዲ ገባኝ፡ ወዳንተ፡ እመጣ፡ ዘንድ። ነገር፡ ግን፡ አንዲት፡ ነገር፡ ተናገር፡ ብላቴናዬም፡ ይፈወሳል።
፰፡ እኔም፡ ደግሞ፡መኰንን፡ሰው፡ ነኝና፡ከንጉሥ፡ በታች፡ ከጆም፡ በታች፡ ወታደር፡ አለኝ። ለዚህም፡ እ ላለሁ፡ሒድ፡ይሔዳልም። ለዚያም፡ና፡ይመጣልም። ባርያዬንም፡ ይህነን፡ አድርግ፡ ያደርጋልም።
፱፡ የሱስም፡ ይህነን፡ በሰማ፡ ጊዜ፡ ከርሱ፡ ተደነቀ። ተመለሰም፡ ለሚከተሉት፡ሰዎችም፡አላቸው። እላ ችኋለሁ፡ በእሥራኤል፡ ስንኳ፡ እንደዚህ፡ ያለ፡ ታላ ቅ፡ ሃይማኖት፡ እንዳላገኘሁ።
፲፡ የተላኩትም፡ወደ፡ቤት፡ተመለሱ፡የታመመው ንም፡ ባርያ፡ ደህና፡ አገኙት።
፲፩፡ በሚመታውም፡ ቀን፡ ሆነ፡ ወደገር፡ እንደ፡ ሔ ደ፡ ስምዋን፡ናይን፡የሚሉዋት። ከርሱ፡ጋራም፡ብዙ፡ ደቀ፡ መዛሙርቱ፡እጅግም፡ ሰዎች፡ አብረው፡ሔዱ።
፲፪፡ ወደገሩ፡ ደጅም፡ በደረሰ፡ ጊዜ፡ እነሆ፡ሙቶ፡ የተሸከሙት፡አገኘ። ለናቱም፡ *አንድ፡ልጅ፡ ነበር፡ ደ ህቺም፡ ባል፡ አልነበራትም፡ ከርሰዋ፡ ጋራም፡ እጅግ፡ ሰዎች፡ ነበሩ፡ ካገሩ፡ ወገን። *፩፡ ነገሥ፡ ፲፯፡ ፲፯።
ኤር፡ ፯፡ ፳፯።
፲፫፡ ጌታም፡ ባያት፡ ጊዜ፡ አዘነላት. አላት። አታል ቅሽ። *ም፡ ፰፡ ፶፪።
፲፬፡ ቀርቦም፡ ቃሬዛውን፡ ነካ፡ የተሸከሙትም፡ ቆ ሙ። አለም። አንተ፡ ጕበዝ፡ እልሃለሁ፡ ተነሣ።
፲፭፡ የሞተውም፡ተቀመጠ፡ይጫወትም፡ጀመረ። *ለናቱም፡ አሳልፎ፡ ሰጣት። ፩፡ ነገሥ፡ ፲፯፡ ፳፫።
፲፮፡ ሁሉንም፡ ፍርሃት፡ ያዛቸው፡ እግዚአብሔርን ም፡ አመዘገኑ፡ እንደህ፡ ሲሉ። ታላቅ፡ ነቢይ፡ ተነሣ ልነ፡ *እግዚአብሔር፡ ሕዝቡን፡ ጐብኝትዋልና። *ም፡ ፩፡ ፷፰። ዘዳግ፡ ፲፰፡ ፲፭።
፲፯፡ ይህም፡ ወሬ፡ ስለርሱ፡ በይሁዳ፡ ሁሉ፡ ወጣ፡ በዙርያውም፡ ባለች፡ አገር፡ ሁሉ።
፲፰፡ ደቀ፡ መዛሙርቱም፡ ይህነን፡ ነገር፡ ሁሉ፡ ለዮ ሐንስ፡ ነገሩት። ማቴ፡ ፲፩፡ ፪፡ ፲፱።
፲፱፡ ዮሐንስም፡ ከደቀ፡ መዛሙርቱ፡ሁለት፡ ጸራ፡ ወደ፡ የሱስም፡ ላካቸው፡ እንደህ፡ ሲል። አንተ፡ ነህ፡ የሚመጣው፡ ወይስ፡ ሌላውን፡ ተስፋ፡እናድርግ።
፳፡ ሁለቱም፡ ሰዎች፡ ወደርሱ፡ በመጡ፡ ጊዜ፡ አሉ ት። መጥምቁ፡ ዮሐንስ፡ ወዳንተ፡ ላከነ፡ እንደህ፡ ሲ ል። አንተን፡ ነህ፡ የሚመጣው፡ወይስ፡ ሌላውን፡ ተስ ፋ፡እናድርግ።
፳፩፡ በዚያም፡ ጊዜ፡ እጅግ፡ ሰዎች፡ ከደዌ፡ ከጸር

ም፡ ከክፉ፡ም፡ አጋንንት፡ፈወሰ፡ ለብዙ፡ም፡ ዕውሮች፡ ማየት፡ ሰጠ።

፳፪፡ የሱስም፡ መለሰ፡አላቸው፡ም። ሒዱ፡ለዮሐ ንስም፡ ያያችሁትን፡የሰማችሁትም፡ነገሩት። ዕውሮ ች፡ ያያሉ፡ አንካሶች፡ ይሔዳሉ። ሙታን፡ ይነሣሉ። ለድኆችም፡ ወንጌል፡ ይሰበካል። ኢሳ፡ ፳፱፡ ፲፰፡፡ ፴፭፡ ፭፡፡

፳፫፡ የማይጠራጠርብኝም፡ ምስጉን፡ ነው።

፳፬፡ የዮሐንስም፡ መልክተኞች፡ በሔዱ፡ ጊዜ፡ ለ ተሰበሰቡት፡ ይል፡ ጀመረ፡ ስለ፡ ዮሐንስ። ለምን፡ ወ ደ፡ ምድረ፡ በዳ፡ ወጣችሁ፡ታዩት፡ዘንድ። ሸምበቆን፡ ነፋስ፡ የሚያንቀሳቅሰው።

፳፭፡ ነገር፡ ግን፡ ለምን፡ ወጣችሁ፡ ታዩት፡ ዘንድ። ሰውንን፡ ቀጭን፡ ልብስ፡የለበሰውን። እነሆ፡ የክብር፡ የተድላም፡ልብስ፡የለበሱ፡በነገሥታት፡ ቤት፡ናቸው።

፳፮፡ ወይስ፡ለምን፡ወጣችሁ፡ ታዩት፡ዘንድ።ነቢይ ንን፡አዎን፡እላችኋለሁ፡ከነቢይም፡የሚበልጠውን። ዮሐ፡ ፩፡ ፳፱፡፡

፳፯፡ ይህ፡ ነው፡ ስለርሱ፡ የተጻፈው። እነሆ፡ መል ክተኞቼን፡ በፊትህ፡ እልካለሁ፡ መንገድህን፡ በፊት ህ፡የሚጸርግ። መልክ፡ ፫፡ ፩፡፡

፳፰፡ እላችኋለሁና። ከሴት፡ ልጆች፡ በተወለዱ፡ መካከል፡ ከመጥምቁ፡ከዮሐንስ፡ የሚበልጥ፡ነቢይ፡ እንደ፡ ሌለ። ታናሹ፡ግን፡በመንግሥተ፡ ሰማያት፡ እር ሱ፡ ከርሱ፡ ይበልጣል። ም፡ ፩፡ ፲፭፡፡

፳፱፡ ሕዝቡም፡ሁሉ፡ቀራጮችም፡ይህነን፡በሰሙ፡ ጊዜ፡እግዚአብሔርን፡አጸደቁ፡ በዮሐንስ፡ ጥምቀት፡ ተጠምቀዋልና። ማቴ፡ ፳፩፡ ፴፩፡፡

፴፡ ፈሪሳውያን፡ ግን፡ባለ፡ኦሪቶችም፡ የእግዚአብ ሔርን፡ምክር፡ በልባቸው፡ *ናቁ፡ ከርሱ፡አልተጠመቁ ምና። የሐዋ፡ ፲፫፡ ፵፮፡፡

፴፩፡ ጌታም፡ ደግሞ፡ አለ። የዚህን፡ ትውልድ፡ ሰ ዎች፡ በምን፡ እመስላለሁ። በምንስ፡ ይመስላሉ።

፴፪፡በገቢያ፡የተቀመጡን፡ብላቴኖች፡ይመስላሉ። እርሱ፡ በርሳቸው፡ የሚጠሩ፡ እንደሁ፡ ሲሉ። ነፋነላ ችሁ፡ አልዘፈናችሁም። አስለቀስነላችሁ፡ አላለቀሳ ችሁምም።

፴፫፡ መጥምቁ፡ ዮሐንስ፡ መጥቶዋልና፡ እንጀራ፡ ሳይበላ፡ ጸጅም፡ ሳይጠጣ። አላችሁም፡ ይህ፡ ሰይጣ ን፡ አለበት።

፴፬፡ የሰው፡ ልጅ፡ መጣ፡ይበላል፡ ይጠጣልም። አ ላችሁም። እነሆ፡የሚበላ፡ ፀጅም፡ የሚጠጣ፡ ሰው፡ የቀራጮችና፡ የኃጢአተኞች፡ ወዳጅ።

፴፭፡ ጥበብም፡ ተጸደቀች፡ ከልጆችዋ፡ ሁሉ።

፴፮፡ ከፈሪሳውያንም፡ አንድ፡ ለመነው፡ ከርሱ፡ ጋ ራ፡ ይበላ፡ ዘንድ። በፈሪሳዊው፡ ቤትም፡ ገባና፡ ተቀ መጠ። ም፡ ፲፩፡ ፴፯፡፡

፴፯፡ እነሆም፡ ኃጢአተኛ፡ ሴት፡ ባገር፡ ነበረች። በ ፈሪሳዊም፡ ቤት፡ተቀምጦ፡ እንዲበላ፡ባወቀች፡ጊዜ፡ የሽቱ፡ ብርሌ፡ አመጣች። ማቴ፡ ፳፮፡ ፯፡፡

፴፰፡ በግሩ፡ አጠገብም፡ ቀመች፡ በኋላው፡ ኢያለ ቀሰች። በንብዋም፡ እግሩን፡ ታርስ፡ ጀመረች፡ በራስ፡ ጸጉርዋም፡ ታብሳለች። እግሩንም፡ ትስመው፡ ሽቱ ም፡ ትቀባው፡ነበረች። ዮሐ፡ ፲፪፡ ፫፡፡

፴፱፡ ያም፡ ያደመው፡ ፈሪሳዊ፡ ያነን፡ ባየ፡ ጊዜ፡ በ ልቡ፡ ተናገረ፡ እንደሁ፡ ሲል። ይህስ፡ነቢይ፡ በሆነ፡ ይህ ች፡ የዳሰሰችው፡ ሴት፡ ማን፡ እንደ፡ ትም፡እንደሆነች፡ ባወቀ፡ ኃጢአተኛይቱ፡ ናትና። ም፡ ፲፭፡ ፪፡፡

፵፡ የሱስም፡ መለሰ፡ አለው፡ም። ሲሞን፡ ሆይ፡ የ ምነግርህ፡ ነገር፡አለኝ። እርሱም፡ አለ። በል፡ መምህ ር፡ ሆይ።

፵፩፡ የሱስም፡ አለ። ላንድ፡አበዳሪ፡ ሁለት፡ ተበዳ ሮች፡ ነበሩት። ባንዱ፡ አምስት፡ መቶ፡ ድሪም፡ በሁለ ተኛው፡ም፡ አምሳ፡ ነበረበት።

፵፪፡ የሚከፍሉትም፡ ቢያጡ፡ ተወላቸው፡ በሁለ ቱ። በልም፡ማናቸው፡እጅግ፡ይወደ፡ታል። ቆላ፡፪፡፲፫፡፡

፵፫፡ ሲሞንም፡መለሰ፡ አለም፡ እጅግ፡ የተወለቱ፡ ይመስለኛል። እርሱም፡ አለው፡ በውነት፡ ፈረድህ።

፵፬፡ ወደ፡ ሴቲቱም፡ ተመለሰ፡ ሲሞንንም፡ አለ ው፡ ይህችን፡ ሴት፡ ታያለህን። እኔ፡ ወደ፡ ቤትህ፡ ገባ ሁ፡ *ውኃ፡ስንኳ፡ በግሬ፡ ላይ፡አላፈሰስህም። ይህች፡ ግን፡እግሬን፡ በንብዋ፡ አራሰች፡ በራስ፡ ጸጉርዋም፡ አበሰች። *ዘፍ፡ ፲፰፡ ፬፡፡ ዮሐ፡ ፲፫፡ ፭፡፡

፵፭፡ አንተም፡ ስመህ፡ አልተገናኘህኝም። እር ስዋ፡ ግን፡ ከገባሁ፡ እግሬን፡ ከመሳም፡ አላረፈችም።

፵፮፡ አንተ፡ራሴን፡ በዘይት፡ አልቀባኸኝም። ይህ ች፡ ግን፡ እግሬን፡ በሽቱ፡ ቀባች። ማቴ፡ ፳፮፡ ፯፡፡

፵፯፡ ስለዚህ፡እልሃለሁ፡ ብዙው፡ ኃጢአትዋ፡ ተ ሰርዮላታል። እጅግ፡ወደለችና። ጥቂት፡ ግን፡ የሚሰ ረይለት፡ ጥቂት፡ ይወዳል።

፵፰፡ ደግሞም፡ አላት፡ኃጢአትሽ፡ተሰርዮልሻል። ም፡ ፭፡ ፳፡ ፳፩፡፡

፵፱፡ ከርሱ፡ ጋራም፡የተቀመጡ፡ በልባቸው፡ይሉ፡ ጀመረ። ማነው፡ ይህ፡ደግሞ፡ ኃጢአት፡ የሚሰርይ።

፶፡ ሴቲቱንም፡ አላት። ሃይማኖትሽ፡አዳነሽ፡በደህ ና፡ ሒጂ። ም፡ ፰፡ ፵፰፡፡ ማር፡ ፭፡ ፴፬፡፡

## ምዕራፍ፡ ፰፡

፩፡ ከዚያም፡በኋላ፡ሆነ፡እርሱም፡ወደገር፡ወደ፡መ ንደርም፡ ሁሉ፡ይሔድ፡ያስተምርው፡ ነበር፡ የምስራ ችም፡ ይነግር፡ ነበረ፡ስለ፡ እግዚአብሔር፡ መንግሥት፡ ከርሱም፡ጋራ፡አሥራ፡ሁለቱ። *ም፡ ፬፡ ፵፫፡፡ ፯፡ ፲፫፡፡

፪፡ *ሴቶችም፡ ከክፉ፡ አጋንንት፡ የፈወሳቸው፡ ከ ደዌም። እርሳቸው፡ም፡ ማርያም፡መግደላዊት፡የም ትባለው፡ሰባት፡ሰይጣን፡ያወጣላት። *ም፡ ፲፩፡ ፳፯፡፡

፫፡ ዮሐናም፡ የሄሮድስ፡እቃ፡ቤት፡ጠባቂ፡የኩዚ፡

ምሽት። ሱሰናም፡ሌሎቹም፡አያሌዎች፡በከብታቸው፡
ያገለግሉት፡የነበሩ። ማር፡ ፲፭፡ ፵፡ ፵፩፡፡
፬፡ እጅግ፡ ሰዎችም፡ ወደርሱ፡ በተሰበሰቡ፡ ጊዜ፡
ካገርም፡ ሁሉ፡ ወደርሱ፡ የመጡ፡ በምሳሌ፡ አለ።
ማቴ፡ ፲፫፡ ፩፡—፳፫፡፡ ማር፡ ፬፡ ፩፡—፳፭፡፡
፭፡ ዘሪ፡ ወጣ፡ ዘሩን፡ ሊዘራ። እርሱም፡ ሲዘራ፡ ከ
ርሱ፡ በመንገድ፡ ወደቀ፡ተረገጠም፡የሰማይ፡ወፎ.ም፡
በላው።
፮፡ ሌላውም፡ በደንጊያ፡ ላይ፡ ወደቀ፡ በበቀለም፡
ጊዜ፡ ደረቀ፡እርጥበት፡ አልነበረበትምና።
፯፡ ሌላውም፡ በእሾህ፡ መካከል፡ ወደቀ፡ እሾህም፡
ከርሱ፡ ጋራ፡ በቀለና፡ አነቀው።
፰፡ ሌላውም፡ በመልካም፡ ምድር፡ ላይ፡ ወደቀ፡
በበቀለም፡ ጊዜ፡መቶ፡ዕፅፍ፡ አፈራ። ይህነንም፡ባለ፡
ጊዜ፡ ጮኸ። የሚሰማ፡ ጆሮ፡ ያለው፡ ይስማ።
ዘፍ፡ ፳፮፡ ፲፪፡፡
፱፡ ደቀ፡ መዛሙርቱም፡ ጠየቁት፡እንዲህ፡ሲሉ።
ይህ፡ ምሳሌ፡ ምንድር፡ ነው።
፲፡ እርሱም፡ አለ። ለናንተ፡ተሰጠ፡ የእግዚአብሔ
ርን፡የመንግሥቱን፡ ምሥጢር፡ለማወቅ፡ለቀሩት፡ ግ
ን፡ በምሳሌ። ኢያዩ፡ *እንደያዩም፡ ኢየሰሙም፡
እንደያስተውሉም። ኢሳ፡ ፮፡ ፱፡ ፲፡፡
፲፩፡ ምሳሌው፡ ግን፡ ይህ፡ ነው። ዘሩ፡ የእግዚአብ
ሔር፡ ነገር፡ ነው። ፩፡ ጴጥ፡ ፩፡ ፳፫፡፡
፲፪፡ በመንገድም፡ ያሉ፡ እርሳቸው፡ የሚሰሙ፡ ና
ቸው። የዚያን፡ ጊዜም፡ ሰይጣን፡ ይመጣል፡ ከልባቸ
ውም፡ነገሩን፡ይወስዳል፡እንደያምኑና፡እንደይድኑ።
ማር፡ ፬፡ ፲፭፡፡
፲፫፡ በደንጊያ፡ ላይ፡ ግን፡ የተዘሩ፡ እርሳቸውም፡ በ
ሰሙ፡ ጊዜ፡ ነገሩን፡ በደስታ፡ የሚቀበሉ። እሌህም፡
ሥር፡ የላቸውም፡ለጊዜውም፡ ያምናሉ፡ በፈተናም፡
ጊዜ፡ ይክዳሉ። ዘፀአ፡ ፬፡ ፴፩፡፡
፲፬፡ በእሾህም፡ የወደቀ፡ እሌህም፡ የሚሰሙ፡ ናቸ
ው። ካሳብም፡ ከባለጠግነትም፡ ከሕይወት፡ መጣፈ
ጥም፡ የተነሣ፡ ይሔዳሉ፡ ይታነቀሉም፡ ፍሬም፡ አያ
ፈሩም። ፊል፡ ፩፡ ፲፩፡፡
፲፭፡ በመልካም፡ ምድር፡ ግን፡የወደቀ፡ እርሳቸው
ም፡ ነገሩ፡በመልካምና፡ በንጹሕ፡ ልብ፡ ሰምተው፡ ይ
ጠብቁታል፡ በትዕግሥትም፡ ያፈራሉ።
የሐዋ፡ ፲፮፡ ፲፬፡፡ ዕብ፡ ፲፡ ፴፮፡፡
፲፮፡ ማንም፡መብራት፡ አብርቶ፡ በቃ፡ የሚከድን፡
የለም፡ ወይስ፡ ካልጋ፡ በታች፡ የሚያኖር። ነገር፡ ግን፡
በመቅረዝ፡ ያስቀምጠዋል፡ የሚገቡ፡ ሁሉ፡ ብርሃን፡
ያዩ፡ ዘንድ። ማር፡ ፬፡ ፳፩፡—፳፭፡፡ ማቴ፡ ፭፡ ፲፭፡፡
፲፯፡ የተሸሸገ፡ የለምና፡ የተገለጠ፡ የማይሆን። የ
ተሠወረም፡ ሳይታወቅ፡ ወደ፡ ብርሃንም፡ ሳይደርስ፡
የሚቀር። ማቴ፡ ፲፡ ፳፮፡፡
፲፰፡ እንግዲህ፡ እዩ፡ እንዴት፡ ትሰማላችሁ። ያለ
ው፡ ይሰጠዋልና፡ የሌለው፡ ግን፡ ያለው፡ የሚመስለ
ው፡ ከርሱ፡ይወሰዳል። ም፡ ፲፱፡ ፳፮፡፡
፲፱፡ እናቱና፡ ወንድሞቹም፡ ወደርሱ፡ መጡ፡ስለ፡
ሕዝቡም፡ ወደርሱ፡ መድረስ፡ አልተቻላቸውም።
ማቴ፡ ፲፪፡ ፵፮፡—፶፡፡ ማር፡ ፫፡ ፴፩፡—፴፭፡፡
፳፡ ባሮችም፡ነገሩት።እናትህ፡ወንድሞችህም፡ሚ
ያ፡ቁመዋል፡ያዩህም፡ዘንድ፡ይመኞሉ።ም፡ ፯፡ ፵፯፡፡
፳፩፡ እርሱ፡ ግን፡ መልሶ፡ አላቸውም። እናቴ፡ ወን
ድሞቼም፡ እሌህ፡ ናቸው፡ የእግዚአብሔርን፡ ነገር፡
የሚሰሙት፡ የሚያደርጉትም።
፳፪፡ ባንድ፡ ቀንም፡ የሱስ፡ ወደ፡ መርከብ፡ ወጣ፡ እ
ርሱ፡ ደቀ፡ መዛሙርቱም፡ አላቸውም። ኑ፡ ወደ፡ ባሕ
ር፡ ማዶ፡ እንሒድ። ሔዱም። ማቴ፡ ፰፡ ፳፫፡—፳፯፡፡
ማር፡ ፬፡ ፴፭፡—፵፡፡
፳፫፡ እርሳቸውም፡ ሲሰረሩ፡ እርሱ፡ አንቀላፋ።
ባሕሩ፡ ዓውሎ፡ ነፋስ፡ ወረደበት። ውሃም፡ መልተባ
ቸው፡ ነበር፡ እርሳቸውም፡ ተጨነቁ።
፳፬፡ ወደርሱም፡ ደርሰው፡ አስነሡት፡ እንዲህ፡ ሲ
ሉ። መምህር፡ ሆይ፡ መምህር፡ ሆይ፡ አለቅን። እርሱ፡
ግን፡ ተነሣ፡ ነፋሱንም፡ ገሠፀው፡ የውሃውንም፡ ሞገ
ድ። ጉደለም፡ ጸጥም፡ አለ።
፳፭፡ አላቸውም፡ የት፡ አለ፡ ሃይማኖታችሁ። ፈሩ
ም፡ ተደነቁም፡ እንዲህ፡ ሲሉ፡ እርሱ፡ በርሳቸው። እ
ንጃ፡ ይህ፡ ማነው፡ ነፋስን፡ደግሞ፡ ውሃንም፡ያዝልና፡
ይታዘዙታልም። ማቴ፡ ፰፡ ፳፯፡፡
፳፮፡ በመርከብም፡ ወደ፡ ገድራኒን፡ አገር፡ ሰረሩ፡
በገሊላ፡ አንጻር፡ የምትሆን። ማቴ፡ ፰፡ ፳፰፡—፴፬፡፡
ማር፡ ፭፡ ፩፡—፳፡፡
፳፯፡ በምድር፡ ላይም፡ በወጣ፡ ጊዜ፡ አንድ፡ ሰው፡
ካገር፡ተቀበለው፡ ሰይጣናት፡የነበሩት፡ከጅግ፡ዘመን፡
ጀምሮ። ልብስም፡ አይለብስም፡ ነበር፡በቤትም፡ አል
ተቀመጠም፡ ነገር፡ ግን፡ በመቃብር።
፳፰፡ የሱስንም፡ ባየው፡ ጊዜ፡ ጮኸ፡ በፊቱም፡ ወ
ደቀ፡ በታላቅ፡ ቃልም፡ አለ። በኔና፡ ባንተ፡ መካከል፡
ምን፡ አለ፡ የሱስ፡ የልዑል፡የእግዚአብሔር፡ ልጅ፡ ሆ
ይ። እለምንሃለሁ፡እንዳትሣቅየኝ። ፪፡ ጴጥ፡ ፪፡ ፬፡፡
፳፱፡ መንፈስ፡ ርኩስን፡ ያዝ፡ ነበርና፡ ከሰው፡ ይወ
ጣ፡ ዘንድ። ብዙ፡ ጊዜ፡ ይዞት፡ ነበርና። በሰንሰለትና፡
በግር፡ ብረትም፡ታሥሮ፡ይጠበቅ፡ነበር፡እሥራቱንም፡
ቈርጦ፡ ከሰይጣኑ፡ ወደ፡ምድረ፡በዳ፡ ይነዳ፡ ነበር።
ማር፡ ፩፡ ፳፯፡፡
፴፡ የሱስም፡ ጠየቀው፡ እንዴት፡ ሲል። ስምህ፡
ማነው። እርሱም፡ አለው። ሌጌዎን። ብዙ፡ሰይጣና
ት፡ ገብተውበት፡ ነበሩና። ማር፡ ፭፡ ፱፡፡
፴፩፡ ወደርሱም፡ ለመኑ፡ ወደ፡ ጥልቅ፡ በመሔድ፡
እንደያዛቸው። ራእ፡ ፱፡ ፲፩፡፡
፴፪፡ ከዚያም፡ የእጅግ፡እርያ፡ መንጋ፡ ነበረ፡ በተ
ራራ፡ይሰማሩ፡የነበሩ። ለመኑትም፡ያዛቸው፡ ዘንድ፡
ሊገቡባቸው፡ አዘዛቸውም።

፴፫፤ ሰይጣናትም፡ ከሰው፡ ወጡ፡ወደ፡ እርያም፡ ገቡ። መንጋውም፡ ካፋፉ፡ ወደ፡ ውኃው፡ ወደቀ፡ ሠ ጠመም።

፴፬፤ ጠባቂችም፡ የሆነውን፡ ባዩ፡ ጊዜ፡ ሸሸተው፡ ሔደ፡ ባገረና፡ በመንደሩም፡ አወሩ።

፴፭፤ የሆነውንም፡ ያዩ፡ ዘንድ፡ ወጡ፡ ወደ፡ የሱስ ም፡ መጡ፡ ሰይጣናት፡ ከርሱ፡ የወጡትንም፡ ሰው፡ ተቀምጦ፡አገኙት፡ልብሱን፡ለብሶ፡አእምሮውንም፡ ገዝቶ፡ በየሱስ፡ እግር፡ አጠገብ፡ ፈሩም።

፴፮፤ ያዩትም፡ ደግሞ፡ ነገሩዋቸው፡ሰይጣናት፡ የነ በሩት፡ እንዴት፡ ደነ።

፴፯፤ በገድራኒን፡ ዙርያ፡ ያለውም፡ ያገሩ፡ ሰዎች፡ ሁሉ፡ ለመኑት፡ከርሳቸው፡ፈቀቅ፡ይል፡ ዘንድ፡ታላቅ፡ ፍርሃት፡ ደርሰባቸዋልና። እርሱ፡ ግን፡ በመርከቡ፡ ተ ቀመጠና፡ ተመለሰ።

፴፰፤ ከርሱ፡ ሰይጣናት፡የወጡለትም፡ሰው፡ለመ ነው፡ ከርሱ፡ ጋራ፡ ይኖር፡ ዘንድ። የሱስ፡ግን፡ሰደደው፡ እንዲህ፡ ሲል።

፴፱፤ ወደ፡ ቤትህ፡ ተመለስ፡ እግዚአብሔር፡ባደረ ገልህ፡ ሁሉም፡ ንገር። ሔደም፡ ባገሩ፡ ሁሉም፡ አስታ ወቀ፡ የሱስ፡ ያደረገለትን፡ ሁሉ።

፵፤ የሱስም፡ በተመለሰ፡ጊዜ፡ሕዝቡ፡ተቀበሉት፡ ተከማችተው፡ ይጠበቁት፡ ነበረና።

ማቴ፡ ፱፤ ፲፰፤—፳፮፡፡ ማር፡ ፭፤ ፳፩፤—፵፫፡፡

፵፩፤ እነሆም፡ሰው፡ መጣ፡ስሙን፡ ያኢሮስ፡ የሚ ሉት። ያህም፡ የጉባዔ፡ አለቃ፡ ነበር። በየሱስ፡ እግር ም፡ ወደቀ፡ ወደ፡ ቤቱም፡ ይገባ፡ ዘንድ፡ ለመነው።

፵፪፤ አንዲት፡ ልጅ፡ ነበረችውና፡ ለርሱዋ፡ አሥራ፡ ሁለት፡ አመት፡ የሆናት። ይህችም፡ ለሞት፡ ቀርባ፡ ነበረች። እርሱም፡ ከርሱ፡ ጋራ፡ ሲሔድ፡ አሕዛብ፡ ያ ጨንቁት፡ ነበር።

፵፫፤ እነሆም፡ ሴት፡ ነበረች፡ ካሥራ፡ ሁለት፡ አመ ት፡ ጀምሮ፡ ደም፡ የፈሰሳት። ከብትዋንም፡ ሁሉ፡ ለ ፈዋሾች፡ ጨርሳ፡ ነበረች፡ ከማንም፡ ትፈወስ፡ ዘንድ፡ አልተቻላትም።

፵፬፤ ከወደ፡ኋላውም፡ መጣች፡ የልብሱንም፡ ጫ ፍ፡ ደሰሰች። የዚያን፡ጊዜም፡ቀጥ፡የደምዋ፡ጐርፍ።

፵፭፤ የሱስም፡ አለ፡ ማነው፤ የዳሰሰኝ። ሁሉም፡ በካደ፡ ጊዜ፡ ጴጥሮስ፡ አለ፡ ከርሱም፡ ጋራ፡ የነበሩ። መምህር፡ ሆይ፡ ሰዎች፡ ያገፉሃል፡ አንተንም፡ ያጨን ቁሃል፡ ትላለህም፡ ማነው፡ የዳሰሰኝ።

፵፮፤ የሱስም፡ ነገረ፡ አንድ፡ የዳሰሰኝ፡ አለ። አው ቃለሁና፡ ኃይል፡ ከኔ፡ እንደ፡ ወጣ።

፵፯፤ ሴቲቱም፡ ባየች፡ ጊዜ፡ ከርሱ፡ እንዳልተሠወ ረች፡ እያተንቀጠቀጠች፡ መጣች፡ ሰገደችለትም፡ በ ሕዝቡ፡ ሁሉም፡ ፊት፡ ተናገረች፡ በምን፡ ምክንያት፡ እንደ፡ ደሰሰችው፡ በጊዜውም፡ እንደ፡ ተፈወሰች።

፵፰፤ እርሱም፡አላት። እመኝ፡ልጅ፡ሆይ። ኃይማ ኖትሽ፡ አደነሽ። በደኅና፡ ሒጂ። ምዕ፡ ፯፤ ፶፡፡

፵፱፤ እርሱም፡ ሲናገር፡ አንድ፡ ሰው፡ ካለቃው፡ ቤ ት፡ መጣ፡ እንዲህ፡ ሲለው። ልጅህ፡ ፈጽማ፡ ሞተች፡ መምህርን፡ አታድክመው።

፶፤ የሱስ፡ ግን፡ በሰማ፡ ጊዜ፡ መለሰለት፡ እንዲህ፡ ሲል። አትፍራ። እመን፡ ብቻ፡ ትድንማለች።

፶፩፤ ወደ፡ ቤትም፡ ገባ፡ ማንም፡ ከርሱ፡ ጋራ፡ ይገባ፡ ዘንድ፡ አልተወም፡ ከጴጥሮስና፡ ከያዕቆብም፡ ከዮሐ ንስም፡ በቀር፡ ከብላቴናዪቱም፡ አባት፡ ከናትዋም።

፶፪፤ ሁሉም፡ ያለቅሱት፡ ዋይ፡ ይሉዋትም፡ ነበሩ። እርሱ፡ ግን፡ አለ፡ *አታልቅሱ። ብላቴናዪቱ፡ አልሞተ ችም፡ ነገር፡ ግን፡ ተኝታለች። *ምዕ፡ ፯፤ ፲፫፡፡

ዮሐ፡ ፲፩፤ ፲፩፡፡

፶፫፤ ከርሱም፡ የተነሣ፡ ሳቁ፡ እንደ፡ ሞተች፡ ስላ ወቁ።

፶፬፤ እርሱ፡ ግን፡ ሁሉን፡ ወደ፡ ሜደ፡ አስወጣ፡ እ ጅዋንም፡ ይዞ፡ ጮኸ፡እንዲህ፡ ሲል። አንቺ፡ብላቴና፡ ተነሺ። የሐ፡ ፱፤ ፴፡፡

፶፭፤ ነፍስዋም፡ ተመለሰች፡የዚያን፡ጊዜውም፡ ተ ነሣች። አዘዘም፡ የምትበላው፡ ይሰጥዋት፡ ዘንድ።

፶፮፤ አባትና፡ እናትዋም፡ አደነቁ፡ *እርሱ፡ ግን፡ አ ዘዛቸው፡ ለማንም፡ በሆነው፡ እንዳይናገሩ።

*ምዕ፡ ፭፤ ፲፬፡፡ ማር፡ ፯፤ ፴፮፡፡

## ምዕራፍ፡ ፱፤

፩፤ ደግሞም፡ አሥራ፡ ሁለቱን፡ ደቀ፡ መዛሙርቱ ን፡ ጸራ፡ ኃይልም፡ ሥልጣንም፡ ሰጣቸው፡ በሰይጣና ት፡ ሁሉ፡ ላይ፡ ድውያንንም፡ ይፈውሱ፡ ዘንድ።

ማር፡ ፮፤ ፯፤—፲፫፡፡

፪፤ ላካቸውም፡ በእግዚአብሔር፡ መንግሥት፡ ይ ሰብኩ፡ ዘንድ፡ ድውያንንም፡ ይፈውሱ፡ ዘንድ።

ማቴ፡ ፲፤ ፩፤—፲፬፡፡

፫፤ አላቸውም፡ ለመንገድ፡ ምንም፡ አትያዙ። በ ትርም፡ ቢሆን፡ ስንቅም፡ እንጀራም፡ ብርም፡ ቢሆን፡ ሁለት፡ ልብስም፡ አይሁንላችሁ። ምዕ፡ ፳፪፤ ፴፭፡፡

፬፤ በማናቸውም፡ ቤት፡ ብትገቡ፡ ከዚያው፡ ተቀ መጡ፡ ከዚያም፡ ውጡ። ምዕ፡ ፲፤ ፭፤—፯፡፡

፭፤ የማይቀበልዋችሁም፡በዚያች፡አገር፡በወጣች ሁ፡ ትቢያውን፡ ደግሞ፡ ከግራችሁ፡ *አርግፉ፡ በርሳቸ ው፡ ምስክር፡ እንዲሆንባቸው። *ምዕ፡ ፲፤ ፲፩፡፡

የሐዋ፡ ፲፫፤ ፶፩፡፡

፮፤ በወጡም፡ጊዜ፡ኢየመንደሩ፡ ይዞሩ፡ ይሰብኩ፡ ይፈወሱም፡ ነበር፡ በስፍራው፡ ሁሉ።

፯፤ ሄሮድስ፡ ያራተኛውም፡ አለቃ፡ ከርሱ፡ የሚደ ረገው፡ ነገር፡ ሁሉ፡ ሰማ፡ ይቸግረውም፡ ነበር፡ አያሌ፡ ሰዎች፡ ይሉ፡ ነበሩና። ዮሐንስ፡ ከሙታን፡ ተነሣ።

ማቴ፡ ፲፬፤ ፩፤ ፪፡፡

፰፤ አኩሉም፡ ኤልያስ፡ ተገለጠ። ሌሉችም፡ ነቢ ይ፡ ተነሣ፡ ከቀደሙቱ። ማር፡ ፮፤ ፲፬፤—፲፯፡፡

፱፤ ሄሮድስም፡ አለ። እኔ፡ የዮሐንስን፡ ራስ፡ ቊረ

ጥሁ። ይህ፡ መነው፡እኔ፡ እንደ፡ህ፡ያሉ፡የምሰማበት።
*ሊያየውም፡ ይሻ፡ ነበር። *ምዕ፡ ፳፫፡ ፰።
ማር፡ ፮፡ ፴፫።

፲፤ ሐዋርያትም፡በተመለሱ፡ጊዜ፡ ባደረጉት፡ሁሉ፡
ነገሩት። ወሰዳቸውም፡ ወደ፡ ምድረ፡በዳም፡ ቦታ፡ ለ
ብቻው፡ ሔደ፡ ቤተ፡ ሳይዳ፡ ወደምትባል፡ አገር፡ አጠ
ገብ። ማቴ፡ ፲፬፡ ፲፫—፳፩። ማር፡ ፮፡ ፴፡—፵፬።
ዮሐ፡ ፮፡ ፩፡—፲፭።

፲፩፤ አሕዛብም፡ ባወቁ፡ ጊዜ፡ ተከተሉት። እርሱ
ም፡ ተቀበላቸው፡ ስለ፡ እግዚአብሔር፡ መንግሥት
ም፡ነገራቸው፡ መዳንም፡ የሚሹትን፡ ይፈውሳቸው፡
ነበር።

፲፪፤ ቀኑም፡ይመሽ፡ ጀመረ፡አሥራ፡ ሁለቱም፡ መ
ጡና፡ አሉት። ሕዝቡን፡ አሰናብት፡ በዙርያችን፡ወደ
ሉ፡ምንደር፡ይሔዱ፡ወደርሻም፡ያደሩ፡ዘንድ፡የሚ
በሉትንም፡ያገኙ፡ዘንድ።ከዚህ፡በምድረ፡በዳ፡ነንና።

፲፫፤ አላቸውም፡እላንተ፡ስጥዋቸው፡የሚበሉት።
እርሳቸውም፡ አሉ፡ ከኛ፡ ጋራ፡ የለም፡ ካምስት፡ እን
ጀራና፡ ከሁለት፡ ዓሣ፡በቀር። ወይም፡ እንሔድ፡ እን
ደሆን፡ እንጀ፡ እንጀራ፡ እንገዛ፡ ዘንድ፡ ለዚህ፡ ሕዝ
ብ፡ ሁሉ።

፲፬፤ አምስት፡ሺህ፡ሰዎች፡ ያህሉ፡ነበሩና። ለደቀ፡
መዛሙርቱም፡አለ። አስቀምጥዋቸው፡አምሳ፡ከፋ
ላችሁ።

፲፭፤ እንዲህም፡ አደረጉ፡ ሁሉንም፡ አስቀመጡ።

፲፮፤ አምስቱንም፡ እንጀራና፡ ሁለቱን፡ ዓሣ፡ ወሰ
ደ፡ ወደ፡ ሰማይም፡ አየ፡ ባረከም፡ ቈረሰም፡ ለደቀ፡
መዛሙርቱም፡ ሰጠ፡ ለሕዝቡ፡ ያቀርቡ፡ ዘንድ።

፲፯፤ ሁሉም፡ በሉ፡ ጸገቡም። ከርሳቸውም፡ የተረ
ፈውን፡እነሡ፡ከቈራሹ፡ አሥራ፡ ሁለት፡ መሶብ።
፪፡ ነገሥ፡ ፬፡ ፵፬። ዮሐ፡ ፮፡ ፲፪።

፲፰፤ ሆነም፡ እርሱ፡ ሲጸልይ፡ ለብቻው፡ ደቀ፡ መዛ
ሙርቱ፡ከርሱ፡ ጋራ፡ ነበሩ። እንዲህ፡ሲልም፡ጠየቃቸ
ው። ምን፡ ይላሉ፡ ሰዎች፡ እኔ፡ እንደ፡ ሆንሁ።
ማቴ፡ ፲፮፡ ፲፫—፳፮። ማር፡ ፰፡ ፳፯።

፲፱፤ እርሳቸው፡ መለሱ፡ አሉም። ከርሳቸውም፡
የሚል፡ አለ፡ መጥምቁ፡ ዮሐንስ። ሌሎችም፡ ኤልያ
ስ። ሌሎችም፡ ነቢይ፡ ከቀደሙቱ፡ ተነሣ።

፳፤ አላቸው። እላንተስ፡ ምን፡ ትላላችሁ፡ እኔ፡ እ
ንደ፡ ሆንሁ። ጴጥሮስም፡መለሰ፡አለም። አንተ፡ የእ
ግዚአብሔር፡ ክርስቶስ፡ ነህ። ማቴ፡ ፲፮፡ ፲፮።
ዮሐ፡ ፮፡ ፷፱።

፳፩፤ እርሱ፡ ግን፡ ገሠፃቸው፡ ይህንም፡ ለማንም፡
እንደይናገሩ፡ አዘዛቸው።

፳፪፤ እንዲህ፡ ሲል። ለሰው፡ ልጅ፡ ይገባዋል፡ እጅ
ግ፡ መከራ፡ ይቀበል፡ ዘንድ፡ ከሽማግሎችና፡ ከካህና
ትም፡ አለቆች፡ ከጻፎችም፡ይናቅ፡ ይገደልም፡ዘንድ፡
በሦስተኛውም፡ ቀን፡ እንዲ፡ ነሣ። መዝ፡ ፻፲፰፡ ፳፪።
ምዕ፡ ፲፰፡ ፴፪።

፳፫፤ ለሁሉም፡አለ። በኋላዬም፡ሊከተለኝ፡ሰው፡
ቢሻ፡ሰውነቱን፡ ይካድ፡ መስቀሉንም፡ ዕለት፡ ዕለት፡
ይሸከም፡ይከተለኝም።

፳፬፤ *ነፍሱን፡ ማዳን፡ የወደደ፡ ይጥላታልና። ነፍ
ሱንም፡ ስለኔ፡ የጣለ፡ ያድናታል። *ምዕ፡ ፲፯፡ ፴፫።
ማቴ፡ ፲፡ ፴፱። ዮሐ፡ ፲፪፡ ፳፭።

፳፭፤ ለሰው፡ ምን፡ ይረብዋል፡ዓለሙን፡ ሁሉ፡ ቢገ
ዛ፡ ነፍሱን፡ ካጠፋ፡ ካጐደለስ።

፳፮፤ በኔ፡ በነገሬም፡ ያፈረ፡ ሁሉ፡ ይህም፡ የሰው፡
ልጅ፡ ያፈርበታል፡ በክብሩ፡ በአብም፡ በቅዱሳንም፡
መላእክት፡ ክብር፡ በመጣ፡ ጊዜ። ማቴ፡ ፲፡ ፴፫።
፪፡ ጢሞ፡ ፪፡ ፲፪።

፳፯፤ እውነት፡እላችኋለሁ። ከዚህ፡ ከቆሙት፡ ሰ
ዎች፡ አሉ፡ሞትን፡የማይቀምሱት፡የእግዚአብሔር
ን፡ መንግሥት፡ እስኪያዩ፡ ድረስ።

፳፰፤ ከዚህም፡ ነገር፡በኋላ፡ ስምንት፡ ቀን፡በሚያ
ህል፡ጴጥሮስን፡ወሰደ፡ ዮሐንስንም፡ ያዕቆብንም፡ ወ
ደ፡ ተራራም፡ ወጣ፡ ይጸልይ፡ ዘንድ።
ማቴ፡ ፲፯፡ ፩፡—፲፫። ማር፡ ፱፡ ፪፡—፲፫።

፳፱፤ እርሱም፡ ሲጸልይ፡የፊቱ፡መልክ፡ወደ፡ ሌላ፡
መልክ፡ ተለወጠ፤ ልብሱም፡ ነጭ፡ ሆነ፡ አብለጨለ
ጨም።

፴፤ እነሆም፡ ሁለት፡ ሰዎች፡ ከርሱ፡ ጋራ፡ ይናገሩ፡
ነበሩ። እርሳቸውም፡ ሙሴና፡ ኤልያስ።

፴፩፤ በክብር፡ የተገለጡ፡ ስለ፡ መውጣቱም፡ ይና
ገሩ፡ ነበሩ፡ በየሩሳሌም፡ ይፈጽመው፡ ዘንድ፡ ጊዜ፡ ያ
ለው። ቆ፡ ፳፪።

፴፪፤ ጴጥሮስ፡ ግን፡ ከርሱም፡ ጋራ፡ የነበሩት፡ እንቅ
ልፍ፡ ከበዳቸው። በነቁም፡ ጊዜ፡ ድብሩን፡ አዩ፡ ሰዎ
ችንም፡ ከርሱ፡ ጋራ፡ ቆመው፡ የነበሩትን።

፴፫፤ እርሳቸውም፡ ከርሱ፡ ተለይተው፡ በሔዱ፡
ጊዜ፡ ጴጥሮስ፡ የሱስን፡ አለው። መምህር፡ ሆይ። ለ
ኛ፡ መልካም፡ ነው፡ ከዚህ፡ ብንሆን። ሦስት፡ ዳስም፡
እንስራ። አንዱን፡ ላንተ፡ አንዱንም፡ ለሙሴ፡ አንዱ
ንም፡ ለኤልያስ። የሚለውንም፡ አያውቅም፡ ነበር።

፴፬፤ ይህነም፡ ሲናገር፡ ደመና፡ ሠወራቸው። እሊ
ያም፡ ወደ፡ ደመና፡ በገቡ፡ ጊዜ፡ ፈሩ።

፴፭፤ ድምፅም፡ ከደመና፡ መጣ፡ እንዲህ፡ ሲል።
ይህ፡ ነው፡ ልጄ፡ የምወደው፡ እርሱን፡ ስሙት።
ዘዳግ፡ ፲፰፡ ፲፱። ምዕ፡ ፫፡ ፳፪።

፴፮፤ ድምፅም፡ በሆነ፡ ጊዜ፡ የሱስ፡ ብቻው፡ ተገኘ።
እርሳቸውም፡ ዝምአሉ፡ ለማንም፡ አልነገሩም፡ በዚያ
ች፡ ወራት፡ ያዩትን፡ ነገር።

፴፯፤ በመጣውም፡ ቀን፡ ከተራራ፡ በወረዱ፡ ጊዜ፡
ብዙ፡ ሰዎች፡ ተቀበሉት። ማቴ፡ ፲፯፡ ፲፬፡—፳፫።
ማር፡ ፱፡ ፲፬፡—፴፪።

፴፰፤ እነሆም፡ ከሕዝቡ፡ አንድ፡ ሰው፡ ጮኸ፡ እንዲ
ህ፡ ሲል። መምህር፡ ሆይ፡ እለምንሃለሁ፡ ልጄን፡ ታየ
ው፡ ዘንድ። ለኔ፡ አንድ፡ ነውና።

፴፱፡ እነሆም፡ ጋኔን፡ይዞታል፡ድንገትም፡ ይጮኻል፡ አንግርም፡ይጥለዋል። እርሱንም፡ ኢያቀጠቀጠ፡ በ ግድ፡ ከርሱ፡ ይመለሳል።

፵፡ ደቀ፡ መዛሙርትህንም፡ ለመንሁ፡ ያወጡት፡ ዘንድ፡ አልቻሉምም።

፵፩፡ የሱስም፡ መለሰ፡ አለም። አንተ፡ ያላመነ፡ ትውልድ፡ገልበጥባጣም። እስከ፡ መቼ፡ከእንተ፡ጋራ፡ እኖራለሁ፡ እሸከማችሁስ፡ አለሁ። ልጅህን፡ አቅርበ ው፡ ወደዚህ።

፵፪፡ እርሱም፡ ሲመጣ፡ ታገለው፡ ሰይጣኑ፡ አንከ ባለለውም። የሱስም፡ርኩስ፡ መንፈሱን፡ ገሠፀው፡ ብላቴናውንም፡ ፈወሰው፡ *ላባቱም፡ ሰጠው።

*ም፡ ፯፡ ፲፭።

፵፫፡ ሁሉም፡ ተደነቁ፡ ከታላቁ፡ ከእግዚአብሔር፡ ኃይል። እርሳቸውም፡ ሁሉ፡ሲደነቁ፡የሱስ፡ከሰራው፡ ስራ፡ ሁሉ፡ ለደቀ፡መዛሙርቱ፡አለ።

፵፬፡ እላንተ፡ ይህነን፡ ነገር፡ በጆሮቻችሁ፡ አኑሩት። የሰው፡ ልጅ፡ በሰው፡ እጅ፡ ይሰጥ፡ ዘንድ፡ ጊዜ፡ አለ ውና። ቍ፡ ፳፪።

፵፭፡ እርሳቸው፡ ግን፡ ይህነን፡ *ነገር፡ አላስተዋሉ ም፡እንደያስተውልዋትም፡ተሠውራቸው፡ ነበረች። ይፈሩትም፡ ነበር፡ ይህችን፡ ነገር፡ ይጠይቁት፡ ዘንድ።

*ም፡ ፲፰፡ ፴፬።

፵፮፡ አሳብም፡ ገባቸው፡ ከርሳቸው፡ ማናቸው፡ እ ንዲበልጥ። ማቴ፡ ፲፰፡ ፩፡—፭። ማር፡ ፱፡ ፴፫፡—፵።

፵፯፡ የሱስም፡የልባቸውን፡አሳብ፡አይቶ፡ሕፃንን፡ ወስዶ፡ ባጠገቡም፡ አቆመው፡ አላቸውም።

፵፰፡ ማንም፡ ይህነን፡ ሕፃን፡ በስሜ፡ የተቀበለ፡ እኔን፡ ተቀበለኝ። ማንም፡ እኔን፡የተቀበለኝ፡የላከኝ ን፡ተቀበለ። ከሁላችሁ፡ያነሰ፡ እርሱ፡ታላቅ፡ ይሆናል ና። ማቴ፡ ፲፡ ፵። ፲፰፡ ፭።

፵፱፡ ዮሐንስም፡መለሰ፡አለም። መምህር፡ሆይ፡ አንድ፡ሰው፡ አየነ፡ ሰይጣናት፡ ሲያወጣ፡ በስምህ። ከለከልነውም፡ ከኛ፡ጋራ፡ አይከተልምና።

፶፡ የሱስም፡ አለው፡ አትከልክሉት። በኛ፡ *ላይ፡ ያልሆነ፡ ሁሉ፡ ከኛ፡ ጋራ፡ ነውና። *ም፡ ፲፩፡ ፳፫።

ፊል፡ ፩፡ ፲፰።

፶፩፡ የመውጣቱንም፡ ወራት፡ በፈጸመ፡ ጊዜ፡ እር ሱ፡ ፊቱን፡ አቀና፡ ወደ፡የሩሳሌም፡ ለመሔድ።

ማር፡ ፲፡ ፴፪።

፶፪፡ በፊቱም፡መልክተኞች፡ሰደደ። *ሔዱም፡ ወ ደ፡ ሰማራውያንም፡አገር፡ ገቡ፡ ሊያሰናዱለት።

*ም፡ ፲፡ ፩። ዮሐ፡ ፬፡ ፬።

፶፫፡ አልተቀበሉትም፡ፊቱ፡ወደ፡የሩሳሌም፡ የሚ ሔድ፡ ነበርና።

፶፬፡ ደቀ፡ መዛሙርቱም፡ ያዕቆብና፡ ዮሐንስ፡ያነ ን፡ባዩ፡ጊዜ፡ አሉት። አቤቱ፡ ትሻለህን፡ እንል፡ዘንድ፡ እሳት፡ ከሰማይ፡ወርዶ፡ታጠፋቸው፡ዘንድ፡ኤልያስ፡ ደግሞ፡ እንደደረገ። ፪፡ ነገሥ፡ ፩፡ ፲፡ ፲፩።

፶፭፡ እርሱ፡ ግን፡ ተመለሰ፡ተቈጣቸውም፡ እንደ ህ፡ሲል። ከምን፡ነፍስ፡ እንደሆናችሁ፡ አታውቁም።

ሮሜ፡ ፰፡ ፲፭።

፶፮፡ *የሰው፡ ልጅ፡አልመጣምና፡ የሰውን፡ ነፍስ፡ ሊያጠፋ፡ሊያድን፡እንጂ። ወደ፡ሌላ፡አገርም፡ሔደ።

*ዮሐ፡ ፫፡ ፲፯። ፲፪፡ ፵፯።

፶፯፡ እርሳቸውም፡ በመንገድ፡ ሲሔዱ፡ አንድ፡ ሰ ው፡ አለው። ልከተልህን፡ ወደምትሔድበቱ፡ ሁሉ፡ ጌታ፡ ሆይ። ማቴ፡ ፰፡ ፲፱፡—፳፪።

፶፰፡ የሱስም፡ አለው። ለቀበሮች፡ ጕድጓድ፡ ለሰ ማይ፡ ወፎች፡ ዛፍ፡ አላቸው። ለሰው፡ ልጅ፡ ግን፡ ራሱ ን፡ የሚያስጠጋበት፡ ስፍራ፡ የለውም።

፶፱፡ ሌላውንም፡ ተከተለኝ፡ አለው። እርሱ፡ ግን፡ አለ። አቤቱ፡ እዘዘኝ፡ እሔድ፡ ዘንድ፡ አስቀድሜ፡ አ ባቴን፡ ለመቅበር።

፷፡ የሱስም፡አለው።ሙታንን፡ተው፡ሙታናቸው ን፡ ይቅበሩ። አንተስ፡ ሒድ፡ የእግዚአብሔርንም፡ መንግሥት፡ አስተምር።

፷፩፡ ደግሞ፡ ሌላም፡ አለ። አቤቱ፡ *ልከተልህ፡ ነገ ር፡ ግን፡ አስናብተኝ፡ አስቀድሜ፡ ልሒድ፡ የቤቴን፡ ሰ ዎች፡ እሠራ፡ ዘንድ። *፩፡ ነገሥ፡ ፲፱፡ ፳፪፡ ፳፫።

፷፪፡ የሱስም፡አለው። ማንም፡ የለም፡ ማረሻ፡ በጁ፡ ይዞ፡ ወደ፡ ኋላው፡ የሚመለከት፡ ለእግዚአብ ሔር፡ መንግሥት፡ የተዘጋጀ፡ ይሆን፡ ዘንድ።

## ምዕራፍ፡ ፲፡

፩፡ ከዚህም፡ በኋላ፡ ጌታ፡ ሌሎች፡ ሰብዓ፡ ደግሞ፡ ሠራ። *ሁለት፡ ሁለትም፡ አድርጎ፡ በፊቱ፡ ላካቸው፡ እርሱ፡ ወደሚሔድበት፡ አገር፡ ስፍራም፡ ሁሉ።

ማቴ፡ ፲። ማር፡ ፮፡ ፯።

፪፡ አላቸውም፡ መከሩ፡ እጅግ፡ ነው፡ ሰራተኞች፡ ግን፡ ጥቂቶች፡ናቸው። ወደ፡መከሩ፡ጌታ፡ለምኑ፡ለመ ከሩ፡ ሰራተኞች፡ ያወጣ፡ ዘንድ። ዮሐ፡ ፬፡ ፴፭።

ማቴ፡ ፱፡ ፴፯፡ ፴፰።

፫፡ ሒዱ። እነሆ፡ እንደ፡ በግ፡ በተኵላ፡ መካከል፡ እሰዳችኋለሁ።

፬፡ ከረጢት፡ አትያዙ፡ ስንቅም፡ ጫማም። በመን ገድም፡ ለማንም፡ *ሰላም፡ አስጡ።

*፪፡ ነገሥ፡ ፬፡ ፳፱።

፭፡ ወደ፡ ገባችሁበትም፡ ቤት፡ አስቀድማችሁ፡ በ ሉ። ሰላም፡ ለዚህ፡ ቤት።

፮፡ ከዚያም፡ የሰላም፡ ልጅ፡ ቢኖር፡ ሰላማችሁ፡ ያ ድርበታል።ያለዚያም፡ሰላማችሁ፡ይመለስላችኋል።

፯፡ በዚያም፡ ቤት፡ ተቀመጡ፡ በርሳቸውም፡ ዘን ድ፡ ካለው፡ ብሉ፡ ጠጡም። ሰራተኛ፡ዋጋው፡ይገባዋ ልና። ከቤት፡ወደ፡ቤት፡ አትሒዱ። ዘዳግ፡ ፳፬፡ ፲፬።

፰፡ ወደ፡ ማናቸውም፡አገር፡ብትገቡ፡ ቢቀበልዋች ሁም፡ ከቀረበላችሁ፡ ብሉ።

፱፡ በርሷዋም፡ ያሉን፡ ድውያን፡ ፈውሱ፡ በልዋቸውም፡ የእግዚአብሔር፡ መንግሥት፡ ወደላንት፡ ቀረበች።

፲፡ ወደ፡ ማናቸውም፡ አገር፡ ብትገቡ፡ ባይቀበልዋችሁም፡ ወደ፡ አደባባይዋ፡ ውጡ፡ በሉም።

፲፩፡ ካገራችሁ፡ የተጣበቀብነን፡ ትቢያ፡ እናራግፍላችኋለን። ነገር፡ ግን፡ ይህነን፡ እወቁ፡ የእግዚአብሔር፡ መንግሥት፡ ወደላንት፡ እንደ፡ ቀረበች።
የሐዋ፡ ፲፫፡ ፶፩።

፲፪፡ እላችኋለሁ፡ ሶዶም፡ በዚያን፡ ቀን፡ ዕረፍት፡ እንዲሆንላት፡ ከዚያች፡ አገር፡ ይልቅ። ዘፍጥ፡ ፲፱፡ ፳፬።

፲፫፡ ወዮልሽ፡ ኮራዚን፡ ሆይ። ወዮልሽ፡ ቤተ፡ ሰይዳ። በጢሮስና፡ በሲዶናስ፡ ቢሆን፡ በላንት፡ የተደረገው፡ ኃይል፡ ቀድሞ፡ በማቅና፡ ባመድ፡ በተቀመጡ፡ ንስሐም፡ በገቡ። ሕዝ፡ ፳፮፡ ፲፬፡ ፲፭። ዮና፡ ፫፡ ፮።

፲፬፡ ነገር፡ ግን፡ ለጢሮስና፡ ለሲዶና፡ ዕረፍት፡ አላቸው፡ በፍርድ፡ ከላንት፡ ይልቅ።

፲፭፡ አንቺም፡ ቅፍርናሆም፡ ወደ፡ ሰማይ፡ የወጣሽ፡ ወደ፡ ሲኦል፡ ትወርጂለሽ።

፲፮፡ ከላንት፡ የሰማ፡ ከኔ፡ የሰማ፡ ነው። እላንትንም፡ የናቀ፡ እኔን፡ የናቀ፡ ነው። እኔንም፡ የናቀ፡ የላከኝን፡ የናቀ።

፲፯፡ ሰብዓው፡ መለክተኞችም፡ በደስታ፡ ተመለሱ፡ እንዲህ፡ ሲሉ። አቤቱ፡ ሰይጣናትም፡ ደግሞ፡ ይገዙልናል፡ በስምህ።

፲፰፡ አላቸውም። ሰይጣንን፡ አየሁ፡ ከሰማይ፡ ሲወድቅ፡ እንደ፡ መብረቅ። ዮሐ፡ ፲፪፡ ፴፩።
ራእ፡ ፲፪፡ ፰፡ ፱።

፲፱፡ እነሆ፡ ሥልጣን፡ ሰጥቻችኋለሁ፡ እባቡን፡ ትረግጡ፡ ዘንድ፡ ጊንጡንም፡ የጸላትንም፡ ጕልበት፡ ሁሉ። ምንም፡ አይጐዳችሁም። መዝ፡ ፺፩፡ ፲፫።

፳፡ ነገር፡ ግን፡ በዚህ፡ ደስ፡ አይበላችሁ፡ ሰይጣናት፡ እንዲገዙላችሁ። እጅግ፡ ደስ፡ ይበላችሁ፡ እንጂ፡ *ስማችሁ፡ በሰማይ፡ እንደተጻፈ። *ዘፀአ፡ ፴፪፡ ፴፪።
ፊል፡ ፬፡ ፫። ራእ፡ ፫፡ ፭።

፳፩፡ በዚያች፡ ጊዜ፡ የሱስ፡ በልቡ፡ ደስ፡ አለው፡ አለም። አመሰግንሃለሁ፡ አባቴ፡ ሆይ፡ የሰማይና፡ የምድር፡ ጌታ። ይህችን፡ ከጠቢባን፡ ካስተዋዮችም፡ ሠውረሃልና፡ ለሕፃናትም፡ ገልጠሃታልና። አዎን፡ አባት፡ ሆይ። እንዲህ፡ በፊትህ፡ ፈቃድ፡ ሁኖላችና።
ማቴ፡ ፲፩፡ ፳፭—፳፯። ፩፡ ቆሮ፡ ፩፡ ፲፱።
መዝ፡ ፰፡ ፫።

፳፪፡ ሁሉ፡ ካባቴ፡ ተሰጠኝ። አንድም፡ አያውቅም፡ ማንነው፡ ልጅ፡ ካባት፡ በቀር። አባትስ፡ ማነው፡ ከልጅ፡ በቀር። ልጅም፡ የወደደው፡ ይገልጥለት፡ ዘንድ።
ዮሐ፡ ፫፡ ፴፭። ዕብ፡ ፪፡ ፰።

፳፫፡ ወደ፡ ደቀ፡ መዛሙርቱም፡ ተመለስ፡ ለብቻቸውም፡ አለ። እላንተ፡ ያያችሁትን፡ ለምታይ፡ ዓይን፡ ምስጋና፡ ይገባታል። ፩፡ ነገሥ፡ ፲፡ ፰። ዮሐ፡ ፰፡ ፶፮።

፳፬፡ እላችኋለሁና፡ *ብዙ፡ ነቢያት፡ ነገሥታትም፡ እላንት፡ ያያችሁትን፡ ሊያዩ፡ወደዱ፡ አላዩም። እላንት፡ የሰማችሁትንም፡ ይሰሙ፡ ዘንድ፡ አልሰሙም። *፩፡ ጴጥ፡ ፩፡ ፲።

፳፭፡ እነሆም፡ የኦሪት፡ ሰው፡ ሊፈትነው፡ ተነሣ፡ እንዲህም፡ አለው። መምህር፡ ሆይ፡ ምን፡ ላድርግ፡ የዘላለም፡ ሕይወት፡ እወርስ፡ ዘንድ።
ማቴ፡ ፳፪፡ ፴፭—፵። ማር፡ ፲፪፡ ፳፰—፴፬።

፳፮፡ እርሱም፡ አለው። በሕግ፡ የተጻፈ፡ ምንድር፡ ነው። እንዴት፡ ታነባለህ።

፳፯፡ እርሱም፡ መለሰ፡ አለም። እግዚአብሔር፡ አምላክህን፡ ውደድ፡ በፍጹም፡ ልብህ፡ በፍጹም፡ ነፍስህም፡ በፍጹም፡ ኃይልህም፡ በፍጹም፡ አሳብህም፡ ባልንጀራህንም፡ እንደ፡ ነፍስህ። ዘሌዋ፡ ፲፱፡ ፲፰።
ዘዳግ፡ ፮፡ ፭።

፳፰፡ አለውም፡ በውነት፡ መለስህ። ይህነን፡ አድርግ፡ ትድንማለህ። ዘሌዋ፡ ፲፰፡ ፭።

፳፱፡ እርሱ፡ ግን፡ ሰውነቱን፡ ጻድቅ፡ ያደርግ፡ ዘንድ፡ ወደደ፡ የሱስንም፡ አለው። ባልንጀራዬስ፡ ማነው።

፴፡ የሱስም፡ መለሰ፡ አለም። ሰው፡ ነበረ፡ ከየሩሳሌም፡ ወደ፡ የሪኮ፡ የወረደ፡ በወንበዴችም፡ መካከል፡ ወደቀ፡ ገፈፉትም፡ አቈሰሉትም፡ ሔዱም፡ በሕይወትና፡ በሞትም፡ መካከል፡ ተውት።

፴፩፡ ካህንም፡ በዚያች፡ መንገድ፡ ሲወርድ፡ አገኘው፡ አይቶትም፡ አለፈ።

፴፪፡ እንዲሁም፡ ደግሞ፡ የሌዊ፡ ወገን፡ ሰው፡ ወደዚያ፡ ስፍራ፡ መጣ፡ አይቶትም፡ አለፈ።

፴፫፡ ሳምራዊ፡ መንገደኛ፡ ግን፡ አለፈበት፡ ባየውም፡ ጊዜ፡ አዘነለት። ሕዝ፡ ፲፮፡ ፮። ዮሐ፡ ፬፡ ፱።

፴፬፡ ወደርሱም፡ ቀረበ፡ ቍስሉንም፡ አጋጠመለት፡ ዘይትና፡ ጸጅም፡ አፈሰሰበት። ባህያውም፡ ላይ፡ አስቀመጣው፡ የሚበጀውንም፡ ነገር፡ አሰበ። ኢሳ፡ ፩፡ ፮።

፴፭፡ በነገውም፡ ሲወጣ፡ ሁለት፡ ድሪም፡ አወጣ፡ ለመንገደኛ፡ ቤት፡ ጠባቂም፡ ሰጠው፡ አለውም፡ አገልግለው። እጅግም፡ ስለርሱ፡ ብታወጣ፡ በተመለስሁ፡ ጊዜ፡ እሰጥሃለሁ።

፴፮፡ ከለዚህም፡ ከሶስቱ፡ ማናቸው፡ ይመስልሃል፡ በወንበዴች፡ መካከል፡ ለወደቀው፡ ባልንጀራ፡ የሆነው።

፴፯፡ እርሱም፡ አለ፡ ምሕረት፡ያደረገለት። የሱስም፡ አለው። ሒድ፡ አንተም፡ እንዲሁ፡ አድርግ።

፴፰፡ ሲሔዱም፡ እርሱ፡ ወደ፡ አንዲት፡ አገር፡ ገባ። *ሴትም፡ ስምዋን፡ ማርታ፡ የሚሉዋት፡ በቤትዋ፡ ተቀበለችው። *ዮሐ፡ ፲፩፡ ፩። ፲፪፡ ፪፡ ፫።

፴፱፡ ይህችም፡ እኅት፡ ነበረቻት፡ ማርያም፡ የምትባል። በየሱስ፡ እግር፡ አጠገብ፡ ደግሞ፡ የተቀመጠች፡ ነገሩን፡ ትሰማ፡ ዘንድ። ዘዳግ፡ ፴፫፡ ፫።

፵፡ ማርታ፡ ግን፡ በብዙ፡ ማገልገል፡ ትጻር፡ ነበረች። ተነሥታም፡ አለችም። አቤቱ፡ አታስበኝምን፡ እኅቴ፡

ትታኝ፡ብቻዬን፡ እስራለሁና። እንኪያስ፡በላት፡ ታግ
ዘኝ፡ ዘንድ።
፵፩፥ የሱስም፡ መለሰ፡ አላትም። ማርታ፡ ማርታ፡
በብዙ፡ ነገር፡ ትደከሚያለሽ፡ ትታወኪማለሽ።
፵፪፥ አንዲ፡ም፡ ነገር፡ ይበቃል። ማርያም፡ ግን፡ መ
ልካም፡ እድል፡ መረጠች፡ ከርስዋ፡ የማይርቀውን።
ማቴ፡ ፮፥ ፴፫፡፡ መክ፡ ፫፥ ፩፡፡

## ምዕራፍ፡ ፲፩፥

፩፥ እርሱም፡ ሲጸልይ፡ባንድ፡ስፍራ፡በጨረሰ፡ጊዜ፡
ከደቀ፡ መዛሙርቱ፡ አንድ፡አለው። አቤቱ፡ አስተም
ረነ፡ እንጸልይ፡ ዘንድ፡ ዮሐንስ፡ደግሞ፡ ደቀ፡ መዛሙ
ርቱን፡ እንደ፡አስተማረ።
፪፥ አላቸውም፡ ብትጸልዩ፡በሉ። አባታችን፡በሰማ
ያት፡የምትኖር። ስምህ፡ ይቀደስ። መንግሥትህ፡ ት
ምጻ። ፈቃድህ፡ በሰማይ፡ እንደ፡ ሆነች፡ እንዲሁ፡ ት
ሁን፡ በምድር። ማቴ፡ ፮፥ ፱፥—፲፫፡፡
፫፥ የሚበቃነን፡እንጀራችነን፡ ስጠነ፡ ዕለት፡ ዕለት።
፬፥ ኃጢአታችነን፡ ይቅር፡ በልልን። እኛም፡ የበደለ
ነን፡ ሁሉ፡ ይቅር፡ እንደምንል። ወደ፡ ፈተናም፡ አታግ
ባነ፡ ከክፉ፡ አድነነ፡ እንጂ።
፭፥ አላቸውም፡ ማነው፡ ከላንት፡ ወዳጅ፡ ያለው፡
በኩል፡ ሌትስ፡ የሚሔድበት፡ የሚለውስ። ወዳጄ፡
ሆይ፡ ሶስት፡ እንጀራ፡ አበድረኝ።
፮፥ ወዳጅ፡ ከመንገድ፡ መጥቶብኛልና፡ የማቀርብ
ለትም፡ የለኝም።
፯፥ ያም፡ ከውስጥ፡ይመልስለታል፡ ይላልም። አታ
ድክመኝ፡ አሁን፡ ደጂ፡ ተቈልፏል፡ ልጆቼም፡ ከኔ፡
ጋራ፡ ባልጋ፡ ላይ፡ ናቸው፡ አልችልም፡ ተነሥቼ፡ እሰጥ
ህ፡ ዘንድ።
፰፥ እላችኋለሁ። ስለ፡ ወዳጅነቱ፡ ሊሰጠው፡ ባይነ
ሣ፡ *ከመነዘነዙ፡ የተነሣ፡ ይነሣል፡ የሚሻውንም፡ ሁ
ሉ፡ ይሰጠዋል። ም፡ ፲፰፥ ፩፡፡
፱፥ እኔም፡ እላችኋለሁ። ለምኑ፡ ይሰጣችሁማል።
እሹ፡ ታገኙማላችሁ። ደጁ፡ ምቱ፡ ይከፈትላችሁ
ማል።
፲፥ የለመነ፡ ሁሉ፡ ይወስዷልና። የሻም፡ያገኛል። ደ
ጁ፡ የመታም፡ ይከፈትለታል።
፲፩፥ ማንስ፡ አባት፡ ነው፡ እላንት፡ ልጁ፡ እንጀራ፡
ቢለምነው፡ ደንጊያን፡ የሚሰጠው። ዓሣስ፡ ቢለምነ
ው፡ ስላሣው፡ እባብን፡ የሚሰጠው።
፲፪፥ እንቍላልስ፡ ቢለምነው፡ ጊንጥን፡ ይሰጥዋል።
፲፫፥ እንኪያስ፡ እላንት፡ ክፉች፡ ስትሆኑ፡ ለልጆቻ
ችሁ፡ መልካም፡ አሰጣት፡ ትሰጡ፡ ዘንድ፡ ብታውቁ።
እንዴት፡ አብዝቶ፡ አባት፡ በሰማይ፡ያለ፡ መንፈስ፡ ቅ
ዱስን፡ ለሚለምኑት፡ ይሰጣል።
፲፬፥ ሰይጣንንም፡ ያወጣ፡ነበር። ያም፡ ድዳ፡ ነበር።
ሰይጣኑም፡ በወጣ፡ ጊዜ፡ ድዳው፡ ተናገረ። አሕዛብ
ም፡ ተደነቁ። ማቴ፡ ፲፪፥ ፳፪፥—፴፩፥ ፵፫፥—፵፭፡፡

፲፭፥ ሰዎችም፡ ከርሳቸው፡ አሉ። በብዔል፡ ዜቡል፡
በሰይጣናት፡ አለቃ፡ ሰይጣናትን፡ ያወጣል።
ማር፡ ፫፥ ፳፪፥—፳፯፡፡
፲፮፥ ሌሎችም፡ የሚፈትኑት፡ ከሰማይ፡ምልክት፡
ይሹ፡ነበሩ። ማር፡ ፰፥ ፲፩፡፡
፲፯፥ እርሱ፡ ግን፡ አሳባቸውን፡ አወቀ፡ አላቸውም።
እርሱ፡ በርሱ፡ የሚለያይ፡ መንግሥት፡ ሁሉ፡ ይጠፋ
ል። ቤትም፡ በቤት፡ ላይ፡ ቢለይ፡ ይወድቃል።
፲፰፥ ሰይጣንም፡ ደግሞ፡ በራሱ፡ ቢለይ፡ እንዴት፡
ይጸናል፡ ግዛቱ። ትላላችሁና፡ እኔ፡ ሰይጣናትን፡ በብዔ
ል፡ ዜቡል፡ እንደ፡ወጣ።
፲፱፥ እኔስ፡ በብዔል፡ ዜቡል፡ ሰይጣናት፡ የማወጣ፡
ከሆንሁ፡ ልጆቻችሁ፡ በማን፡ ያወጣሉ። ስለዚህም፡
እርሳቸው፡ ፈራጆች፡ ይሆኑባችኋል።
፳፥ እኔ፡ ግን፡ በእግዚአብሔር፡ *ጣት፡ ሰይጣናትን፡
አወጣ፡ እንደ፡ ሆንሁ፡ እንኪዲህ፡ የእግዚአብሔር፡
መንግሥት፡ ወደላንት፡ ደረሰች። *ዘፀአ፡ ፰፥ ፲፱፡፡
፳፩፥ ብርቱ፡ ሰው፡ ጋሻ፡ ጦሩን፡ ለብሶ፡ ቤቱን፡ በጠ
በቀ፡ ጊዜ፡ ከብቱ፡ደህና፡ ይሆናል።
፳፪፥ ከርሱ፡ *የበረታ፡ ግን፡ በመጣና፡ባሸነፈውም፡
ጊዜ፡ ይታመነው፡ የነበረውን፡ ጋሻ፡ ጦሩንም፡ ይወስዳ
ል፡ ኩብቱንም፡ ይካፈላል። *ኢሳ፡ ፶፫፥ ፲፪፡፡
ቈል፡ ፪፥ ፲፭፡፡
፳፫፥ ከኔ፡ ጋራ፡ ያልሆነ፡ እርሱ፡ በኔ፡ ላይ፡ ነው። ከኔ
ም፡ ጋራ፡ የማይሰበስብ፡ እርሱ፡ ይበትናል። ም፡ ፱፥ ፶፡፡
፳፬፥ መንፈስ፡ ርኩስ፡ ከሰው፡ በወጣ፡ ጊዜ፡ ውኃ፡
በሌለበት፡ ስፍራ፡ ይሔዳል፡ ዕረፍት፡ ሲሻ። ባላገኘም፡
ጊዜ፡ ይላል። ወደ፡ ወጣሁበት፡ ቤቴ፡ ልመለስ።
ማቴ፡ ፲፪፥ ፵፬፡፡
፳፭፥ በመጣም፡ ጊዜ፡ ተጸርጎ፡ አጌጦ፡ አገኘው።
፳፮፥ የዚያን፡ ጊዜ፡ ይሔዳል፡ ከርሱ፡ ጋራም፡ ሰባት፡
አጋንንት፡ ሌሎች፡ ይወስዳል፡ ከርሱ፡ የሚከፉ። ይገ
ቡማል፡ ከዚያም፡ ይቀመጣሉ፡ *የዚያ፡ ሰው፡ ኋላኛ
ውም፡ ከፊተኛው፡ የከፋ፡ ይሆናል። *ዮሐ፡ ፭፥ ፲፬፡፡
፪፥ ጴጥ፡ ፪፥ ፳፡፡
፳፯፥ እርሱም፡ ይህነን፡ ሲናገር፡ ሴት፡ ከሕዝቡ፡ ቃ
ልዋን፡ ከፍ፡ አድርጋ፡ ጮኸች፡ አለችውም። ለተሸከ
መህ፡ ማሕፀን፡ *ምስጋና፡ ይገባዋል፡ ለጠባሃቸውም፡
ጡቶች። *ም፡ ፩፥ ፳፰፥ ፵፪፥ ፵፰፡፡
፳፰፥ እርሱ፡ ግን፡ አለ፡ ምስጋናስ፡ የእግዚአብሔር
ን፡ ነገር፡ ለሚሰሙ፡ ለሚጠብቁትም።
ም፡ ፰፥ ፲፭፥—፳፩፡፡
፳፱፥ ሕዝብም፡ በተሰበሰቡ፡ ጊዜ፡ ይል፡ ጀመረ። ይ
ህ፡ ትውልድ፡ ክፉ፡ ነው፡ መልክት፡ ይሻል። ምልክት
ም፡ አይሰጠውም፡ ከነቢዩ፡ ከዮናስ፡ ምልክት፡ በቀር።
ማቴ፡ ፲፪፥ ፴፰፥—፵፪፡፡
፴፥ ዮናስ፡ የነነዌ፡ ሰዎች፡ ምልክት፡ እንደ፡ ሆነ፡ እን
ዲሁ፡ ደግሞ፡ የሰው፡ ልጅ፡ ለዚህ፡ ትውልድ፡ ይሆና
ልና። ዮና፡ ፪፥ ፩፡፡

፴፩፤ የአዜብ፡ ንግሥት፡ በፍርድ፡ ትነሣለች፡ ከዚህ፡ ትውልድ፡ሰዎች፡ጋራ፡ ትፈረድቸውማለች። ከምድር፡ ዳርቻ፡ መጥታለችና፡ የሰሎሞንን፡ ብልሃት፡ ልትሰማ። እነሆም፡ ከሰሎሞን፡የሚበልጥ፡ከዚህ፡ነው። ፩፤ ነገሥ፡ ፲፤ ፩፤

፴፪፤ የነነዌ፡ሰዎች፡ በፍርድ፡ይነሣሉ፡ ከዚህ፡ትውልድ፡ ጋራ፡ ይፈረዲታልም። ከዮናስ፡የሚበልጥ፡ከዚህ፡ ነው። ዮና፡ ፫፤ ፭።

፴፫፤ ማንም፡ መብራት፡ አብርቶ፡በሰውርና፡በንቅብ፡ ታች፡ አያኖረውም፡ በመቅረዝ፡ላይ፡ እንጂ፡ የሚገቡት፡ ብርሃን፡ ያዩ፡ ዘንድ። ም፡ ፭፤ ፲፭፤
ማቴ፡ ፭፤ ፲፭።

፴፬፤ የሥጋ፡መብራቱ፡ዓይን፡ ነው። ዓይንህም፡ጽሩ፡የሆነ፡እንደ፡ሆን፡ሥጋህ፡ሁሉ፡የበራ፡ይሆናል። ዓይንህስ፡ድውይ፡ ከሆነ፡ ሁለንትናህ፡ ጨለማ፡ ይሆናል። ማቴ፡ ፮፡ ፳፪፡ ፳፫።

፴፭፤ እንጊዲህ፡ ተጠበቅ፡ ባንተ፡ ያለው፡ ብርሃን፡ ጨ ለማ፡እንዳይሆንብህ። ዮሐ፡ ፫፤ ፲፱፤

፴፮፤ ሥጋህ፡ ሁሉስ፡ ብርሃን፡ ከሆነ፡ ጥቂት፡ የጨለማ፡ቍራጭም፡ ከሌለበት፡ እርሱ፡ሁሉ፡ የበራ፡ይሆናል፡ መብራት፡ በብርሃኑ፡ እንዲያበራልህ።

፴፯፤ እርሱም፡ ሲናገር፡ፈሪሳዊ፡ ለመነው፡ ከርሱ፡ ዘንድ፡ምሳውን፡ይበላ፡ ዘንድ። ገብቶም፡ ተቀመጠ።

፴፰፤ ፈሪሳዊው፡ ግን፡ባየ፡ጊዜ፡ ተደነቀ፡ ከምሳ፡ በፊት፡እጁን፡ስላልታጠበ። ማቴ፡ ፲፭፤ ፪።

፴፱፤ ጌታም፡አለው። አሁንም፡ እላንት፡ ፈሪሳውያን፡ የጽዋውን፡ የቃውንም፡ ሜደውን፡ ታነጻላችሁ። ውሥጣችሁ፡ ግን፡ መቀማት፡ ክፋትም፡ መልቶ፡ ይኖራል። ማቴ፡ ፳፫።

፵፤ እላንት፡ደናቍርት። የሜደውን፡ የፈጠረ፡ እርሱ፡ ደግሞ፡ የውሥጡን፡ የፈጠረ፡ አይደለምን።

፵፩፤ ነገር፡ግን፡ከላንት፡ዘንድ፡እንደለ፡ መጠን፡ ምጽዋት፡ ስጡ፡ እነሆም፡ ነገር፡ ሁሉ፡ ንጹ፡ ይሆንላችኋል። ፩፤ ጢሞ፡ ፬፤ ፬። ቲቶ፤ ፩፤ ፲፭።

፵፪፤ ነገር፡ግን፡ወዮላችሁ፡እላንት፡ፈሪሳውያን። ካሥር፡ አንድ፡ ታወጣላችሁና፡ እንስላል፡ ጤናደምም፡ የሚበቅለውንም፡ ሁሉ። የእግዚአብሔርንም፡ ፍርድ፡ ፍቅሩንም፡ ትተላለፉላችሁ። ይህነንም፡ ታደርጉት፡ ዘንድ፡ ይገባችሁ፡ ነበር፡ ያነንም፡ ባተውት።

፵፫፤ ወዮላችሁ፡ እላንት፡ ፈሪሳውያን። በመስጊድ፡በላይ፡መቀመጥ፡ ትወዳላችሁና፡ ሰላምታም፡ መስጠት፡ በገቢያ።

፵፬፤ ወዮላችሁ፡ እላንት፡ ጻፎች፡ ፈሪሳውያንም፡ ግብዞች። እንደ፡ተሠወረ፡ መቃብር፡ናችሁና፡ ያሚሔዲበትም፡ ሰዎች፡ አያውቁም።

፵፭፤ ከባለ፡ ኦሪቶችም፡ አንዲ፡ መለሰ፡ አለም። መምህር፡ሆይ፡ይህነን፡ ማለትህ፡እኛንን፡ደግሞ፡ መስደብኽ፡ ነው።

፵፮፤ እርሱም፡አለ። እላንትም፡ደግሞ፡የኦሪት፡ሰዎች፡ወዮላችሁ። ለሰዎች፡ሸክም፡ ታሸክማላችሁና። ከመሸከም፡የሚከብድ። እላንትም፡ባንዲት፡ጻታችሁ፡ ሸክሙን፡ አትነኩም። ኢሳ፡ ፲፤ ፩።

፵፯፤ ወዮላችሁ። የነቢያትኝ፡ መቃብር፡ትሰራላችሁና፡ አባቶቻችሁም፡ ገደልዋቸው።

፵፰፤ እላንትም፡ ትመሰክራላችሁ፡ ባባቶቻችሁም፡ስራ፡ደስ፡ይላችኋል። እርሳቸው፡ገድለዋቸዋልና። እላንትም፡መቃብራቸውን፡ትሰራላችሁ።

፵፱፤ ስለዚህም፡አለች፡የእግዚአብሔር፡ ጥበብ። ወደርሳቸው፡ ነቢያትን፡ እልኳለሁ፡ ሐዋርያትንም። ከርሳቸውም፡ ይገድላሉ፡ ያሳድዋቸዋልም። ማቴ፡ ፲፤ ፲፮። ዮሐ፡ ፲፮፤ ፪።

፶፤ የነቢያት፡ ሁሉ፡ደም፡ ከጥንት፡ ጀምሮ፡ የፈሰሰው፡ ከዚህ፡ ትውልድ፡ ሊፈለግ።

፶፩፤ ከአቤል፡ደም፡ጀምሮ፡እስከ፡ዘካርያስ፡ደም፡ ድረስ፡በመሠዊያውና፡በመቅደስ፡ መካከል፡ የገደሉት። እውነት፡እላችኋለሁ፡ከዚህ፡ ትውልድ፡ እንዲፈለግ። ዘፍ፡ ፬፤ ፰።

፶፪፤ ወዮላችሁ፡እላንት፡የኦሪት፡ሰዎች። የውቀት፡ መክፈቻ፡ወሰዳችኋልና። እላንትም፡ አልገባችሁም፡ የሚገቡትንም፡ ከለከላችሁ። ኢሳ፡ ፶፯፤ ፲፩። ኤር፡ ፪፤ ፰። ፪፤ ጢሞ፡ ፫፤ ፯።

፶፫፤ ይህነንም፡ ሲላቸው፡ ጻፎችና፡ ፈሪሳውያን፡ በጽኑ፡ ያያዙት፡ ነበር፡በብዙም፡ነገር፡ይጠይቁት፡ነበር። መዝ፡ ፵፩፤ ፯፤ ፰።

፶፬፤ ተሸምቀው፡ ካፉም፡ ነገር፡ ሊወስዲ፡ ሹኮው፡ ሊያጸሉት። ም፡ ፳፤ ፳። ዮሐ፡ ፰፤ ፮።

ምዕራፍ፡ ፲፪፤

፩፤ የብዙ፡ብዙ፡አሕዛብ፡በተሰበሰቡም፡ ጊዜ፡ እርሱ፡ በርሳቸው፡ እስኪረጋገጡ፡ ድረስ፡ለደቀ፡ መዛሙርቱ፡አስቀድሞ፡ይል፡ ጀመረ። ተጠበቁ፡ከፈራሳውያን፡ እርሾ፡ እርሱም፡ ግብዝነት። ማቴ፡ ፲፤ ፳፮—፴፫። ፲፮፤ ፮።

፪፤ የተሸሸገ፡ *የለምና፡ ሳይገለጥ፡ የሚቀር፡የተሠወረም፡ ሳይታወቅ። *ም፡ ፬፤ ፳፪። ሮሜ፡ ፪፤ ፲፮።

፫፤ ስለዚህ፡ በጨለማ፡ የተናገራችሁት፡ በብርሃን፡ ይሰማል። በጆሮም፡ ያላችሁት፡ በቤት፡ በሰገነት፡ ላይ፡ ይነገርበታል።

፬፤ እላችሁማልሁ፡ ለላንት፡ ለወዳጆቼ። አትፍሩ፡ ሥጋን፡ ከሚገሉ፡ ከዚያ፡ ወዲያም፡ ከዚያ፡ የሚበልጥ፡የሚያደርጉት፡ የላቸውም።

፭፤ እኔ፡ግን፡ላሳያችሁ፡ የምትፈሩትን። ፍሩ፡ከገደለ፡በኋላ፡ወደ፡ገሃነም፡ለመስደድ፡ ሥልጣን፡ካለው። እውነት፡ እላችኋለሁ፡ ከርሱ፡ ፍሩ።

፮፤ አምስት፡ወፎች፡ በሁለት፡ናስ፡ አይሸጡምን። አንዲም፡ ከርሳቸው፡ በእግዚአብሔር፡ ፊት፡ አይረሳም።

፯፤ ነገር፡ግን፡ደግሞ፡ የራስ፡ *ጸጕራችሁ፡ ሁሉ፡ የተ

ቍጠረ፡ነው።አትፍሩም። ከዐፎች፡እጅግ፡ትበልጣላችሁና። *ምዕ፡ ፳፩፡ ፲፰።

፰፡ እላችሁማለሁ።በሰው፡ፊት፡ያመነብኝ፡ ሁሉ፡ የሰው፡ ልጅም፡ ደግሞ፡ ያምንበታል፡ በእግዚአብሔር፡ በመላእክት፡ ፊት። ማቴ፡ ፲፡ ፴፪። ፳፭፡ ፴፩።

፱፡ በሰው፡ ፊትም፡ የካደኝ፡ በእግዚአብሔር፡ መላእክት፡ ፊት፡ ይካደል። ምዕ፡ ፱፡ ፳፮። ፪፡ ጢሞ፡ ፪፡ ፲፪፡

፲፡ በሰው፡ልጅም፡ላይ፡ ነገር፡ *የሚናገር፡ ሁሉ፡ይሰረይለታል። በመንፈስ፡ቅዱስ፡ግን፡ የሚሳደብ፡ አይሰረይለትም። ማር፡ ፫፡ ፳፰። ፩፡ ዮሐ፡ ፭፡ ፲፮።

፲፩፡ ወደ፡ መስጊድም፡ባቀረብዋችሁ፡ጊዜ፡ ወደለቀቆችም፡ወደ፡ነገሥታትም፡አታስቡ፡ እንዴት፡ ወይስ፡ ምንድር፡እንድትመልሱ፡ ወይም፡ ምን፡ እንድትሉ። ምዕ፡ ፳፩፡ ፲፬። ማር፡ ፲፫፡ ፲፩።

፲፪፡ መንፈስ፡ቅዱስ፡ በዚያች፡ ጊዜ፡ የምትሉትን፡ ያስተምራችኋልና።

፲፫፡ ከሕዝብም፡አንድ፡ ሰው፡ አለው። መምህር፡ ሆይ፡ ወንድሜን፡ በለው፡ ርስቴን፡ እንዲያካፍለኝ።

፲፬፡ እርሱም፡ አለው። አንተ፡ሰው፡ ማን፡ አለቃ፡ ሾመኝ፡ አካፋይስ፡ በላያችሁ።

፲፭፡ አላቸውም ።እዩ፡ከሥሥትም፡ ሁሉ፡ ተጠበቁ።የማንም፡ሕይወት፡በከብቱ፡ብዛት፡ የለውምና። ፩፡ ጢሞ፡ ፮፡ ፱፡ ፲። መዝ፡ ፵፱፡ ፲፮።

፲፮፡ ምሳሌም፡ አላቸው፡ እንዲህ፡ ሲል። አንድ፡ሰው፡ ባለ፡ ጸጋ፡ ምድሩ፡ አማረችለት።

፲፯፡ በልቡም፡ አሰበ፡እንዲህ፡ሲል፡ ምን፡ላድርግ። እህሌን፡የማኖርበት፡ ስፍራ፡ የለኝምና።

፲፰፡ አለም፡ይህነን፡ አደርጋለሁ። ጎተራዬን፡ አፍርሼ፡ ሰፊ፡ አድርጌ፡ እሰራለሁ። ከዚያም፡ እህሌን፡ ሁሉ፡ እከማቻለሁ፡ በረከቴንም። መዝ፡ ፵፱፡ ፯።

፲፱፡ ሰውነቴንም፡እላለሁ። አንቺ፡ሰውነት፡እጅግ፡ በረከት፡አለሽ፡ ለብዙ፡ ዘመን፡ የሚበቃሽ። ዕረፊ።ብዪ። ጠጪ። ደስ፡ይበልሽ።

፳፡ እግዚአብሔር፡ግን፡ አለው።አንተ፡ ሰነፍ፡ በዚች፡ሌት፡ነፍስህን፡ይሽዋታል፤ካንተ፡ሊወስድዋት። ይህም፡ያሰናደኸው፡ለማን፡ይሆናል። መዝ፡ ፶፪፡ ፲፩። ፺፪፡ ፯—፱። ዕብ፡ ፱፡ ፳፯።

፳፩፡ እንዲሁ፡ከብት፡የሚያከማች፡ለነፍሱ፡ነገር፡ ግን፡እርሱ፡ከእግዚአብሔር፡ ዘንድ፡ባለ፡ ጸጋ፡አይደለም። ማቴ፡ ፮፡ ፲፱—፴፫።

፳፪፡ ለደቀ፡ መዛሙርቱም፡ አለ። ስለዚህ፡ እላችኋለሁ፡ለነፍሳችሁ፡አታስቡ፡ በምትበሉት፡ ለሥጋም፡ በምትለብሱት።

፳፫፡ ነፍስ፡ ከመብል፡ ትበልጣለችና፡ ሥጋም ፡ ከልብስ።

፳፬፡ ቍራን ፡ ተመልከቱ ። አይዘሩምና፡ አያጭዱምና ። ክትቻም፡ የለውም ፡ ጎተራ ፡ ሰንኳ ። እግዚአብሔርም ፡ ይመግባቸዋል። እንዴትስ፡ እላንተ፡ ከዐፎች፡ እጅግ፡ ትበልጡ። መዝ፡ ፻፵፯፡ ፱።

፳፭፡ ማነው፡ከላንተ፡አስቦ፡ አንድ፡ ክንድ፡ በቁመቱ፡ላይ፡ ይጨምር፡ ዘንድ፡ የሚችል።

፳፮፡ ታናሽም፡ማድረግ፡ የማትችሉ፡ ከሆናችሁ፡ለምን፡በሌላው፡ታስባላችሁ።

፳፯፡ አበቦችን ፡ ተመልከቱ፡ እንዴት፡ ያድጋሉ። አይደክሙም፡አይፈትሉም።እላችሁማለሁ፡ ሰሎሞን፡ስንኳ፡ በክብሩ፡ ሁሉ፡ከለዚህ፡ እንደንዲቱ፡ አለበሰም።

፳፰፡ ሣሩንም፡ ዛሬ፡ በምድረ ፡ በዳ፡ ያለውን፡ ነገም፡ወደ፡እቶን፡የሚጣል፡እግዚአብሔር፡እንዲህ፡የሚያለብሰው፡ ከሆነ፡ እንዴት፡ እላንተ፡ ትበልጡ፡ እላንተ፡ሃይማኖት፡ያነሳችሁ።

፳፱፡ እላንተም፡ የምትበሉትን ፡ ወይም፡ የምጠጡትን፡አትጠይቁ።በሚያስጨንቅም፡አሳብ፡አትዋለሉ።

፴፡ ይህነን፡ሁሉ፡የዓለም፡አሕዛብ፡ ይሹታልና። እላንተ፡ግን፡ አባታችሁ፡ ያውቃል፡ ይህነን፡ ሁሉ፡ እንድትሹ።

፴፩፡ ነገር፡ ግን፡ የእግዚአብሔርን፡ መንግሥት፡ ፈልጉ። ይህም፡ ሁሉ፡ ይጨመርላችኋል። ምዕ፡ ፲፫፡ ፲፯።

፴፪፡ አትፍሩ፡አንተ፡ታናሽ፡ መንጋ። አባታችሁ፡ ወድዋልና፡መንግሥት፡ ይሰጣችሁ፡ ዘንድ። ምዕ፡ ፳፪፡ ፳፱። ኢሳ፡ ፵፩፡ ፲፬።

፴፫፡ ከብታችሁን፡ሽጡ፡ምጽዋትም፡ስጡ።ለላንተ፡የማያረጅ፡ከረጢት፡አድርጉ፡ መዝገብም፡ በሰማይ፡ የማይጠፋ። ሌባ፡ወደማይደርስበት፡ ነቀዝም፡ የማያጠፋው። ምዕ፡ ፲፰፡ ፳፪። ዕብ፡ ፲፡ ፴፬።

፴፬፡ መዝገባችሁ፡ ወደለበት፡ ከዚያ ፡ ልባችሁ፡ ይሆናልና።

፴፭፡ ወገባችሁ ፡ *የታጠቀ ፡ ይሁን ። † መብራታችሁም፡ የበራ። ማቴ፡ ፳፬፡ ፵፪—፶፩። *ዘፀአ፡ ፲፪፡ ፲፩። †ማቴ፡ ፳፭፡ ፩—፲፫።

፴፮፡ እላንተም፡ጌታቸውን፡የሚጠብቁን፡ሰዎች፡ መስላችሁ፡ከሰርግ፡እስኪመለስ።መጥቶ፡ ደጅም፡በመታ፡ ጊዜ፡ ቶሎ፡ ይከፍቱለት፡ ዘንድ። ፩፡ ጴጥ፡ ፩፡ ፲፫። ራእ፡ ፫፡ ፳።

፴፯፡ ምስጉን፡ናቸው፡ እነዚያ፡ ባሮች፡ ጌታቸው፡በመጣ፡ጊዜ፡ነቅተው፡የሚያገኛቸው። እውነት፡ እላችኋለሁ ። ወገቡን፡ ታጥቀ ፡ እንዲያስቀምጣቸው፡ ተነሥቶም፡ እንዲያገለግላቸው።

፴፰፡ በሁለተኛውም፡ ሰዓት ፡ ቢመጣ ፡ በሶስተኛውም፡ሰዓት፡ቢመጣ፡እንደሁም፡ቢያገኛቸው፡ምስጉን፡ናቸው፡ እለዚያ፡ ባሮች።

፴፱፡ ይህነንም፡እወቁ፡የቤቱ፡ጌታ፡ *ቢያውቅ፡ ሌባ፡ የሚመጣበትን፡ ጊዜ፡ በነቃ፡ ነበር፡ ቤቱንም፡ ሊማስ፡ ባልተወም። *፩፡ ተሰሎ፡ ፭፡ ፪። ዮሐ፡ ፲፫፡ ፲፭።

፵፡ እላንትም፡ደግሞ፡የተዘጋጃችሁ፡ሁኑ።የሰው፡
ልጅ፡ ባልጠረጠራችሁት፡ ቀን፡ ይመጣልና።
ም፡ ፳፬፡ ፵፬፡፡
፵፩፡ ጴጥሮስም፡አለው።አቤቱ፡ለኛን፡ይህነን፡ም
ሳሌ፡ትላለህ፡ወይስ፡ለሁሉ።
፵፪፡ ጌታም፡አለ።ማነው፡ እንኪያ፡ የታመነ፡ መጋ
ቢ፡ ብልሃተኛስ፡ ጌታው፡ በባሮቹ፡ ላይ፡ የሚሾመው፡
ምግባቸውን፡በጊዜው፡ሊሰጣቸው። ፩፡ ቆሮ፡ ፬፡ ፪፡፡
፵፫፡ ምስጋና፡ይገባዋል፡ለዚያ፡ባርያ፡ጌታው፡በመ
ጣ፡ ጊዜ፡ እንደህ፡ ሲያደርግ፡ የሚያገኘው።
፵፬፡ እውነት፡እላችኋለሁ፡በከብቱ፡ ሁሉ፡ ላይ፡እ
ንዲሾመው። ም፡ ፲፱፡ ፲፯፡፡
፵፭፡ ያ፡ባርያ፡ግን፡በልቡ፡ቢል፡ጌታዬ፡አስኪመጣ፡
ይዘገያል።ባሮቹንም፡ሴቶችንም፡ ባሮች፡ ይመታ፡ይጀ
ምራል፡ ይበላልም፡ይጠጣልም፡ ይሰክራልም።
፵፮፡ ይመጣል፡የዚያ፡ባርያ፡ጌታ፡ ባልጠረጠረው፡
ቀን፡ ባላወቃትም፡ ጊዜ ። ከመካከልም ፡ ይሰነጥቀዋ
ል። ፈንታውንም፡ ከማያምኑት፡ ጋራ፡ ያደርጋል።
፵፯፡ ያ፡*ባርያ፡ ግን፡ የጌታውን፡ ፈቃድ፡ የሚያው
ቅ፡ የማያዘጋጅም፡ እንደ፡ ፈቃዱ፡ም፡ የማያደርግ፡እ
ጅግ፡ ይመታል። *ያዕ፡ ፬፡ ፲፯፡፡
፵፰፡ የማያውቅ፡ግን፡መመታት፡የሚገባውንም፡
የሚያደርግ፡ጥቂት፡ይመታል።እጅግም፡የተሰጠው፡
እጅግ፡ይሹበታል። ሆዝ፡ ፹፪፡ ፲፫፡፡ ፩፡ ጢሞ፡ ፯፡ ፲፭፡፡
፵፱፡ በምድር፡ላይ፡እሳት፡ አኖር፡ ዘንድ፡ መጣሁ።
ምንስ፡እሻለሁ፡ ከማንደድዋ፡በቀር።
፶፡ ለኔም፡ የምጠመቃት፡ ጥምቀት፡ አለችኝ። *እ
ንዴትስ፡ እጠበባለሁ፡ እስክትፈጸም፡ ድረስ።
*ማቴ፡ ፳፡ ፳፪፡፡ ፳፮፡ ፴፰፡፡ ዮሐ፡ ፲፪፡ ፳፯፡፡
፶፩፡ ታስባላችሁን ፡ እኔ፡ እንደ፡ መጣሁ ፡ በምድር፡
ላይ፡ሰላም፡እሰጥ፡ዘንድ። እላችኋለሁ። አይደለም፡
ነገር፡ግን፡ መለየት። ማቴ፡ ፲፡ ፴፬፡—፴፮፡፡
፶፪፡ ከዛሬ፡ጀምሮ፡አምስት፡ባንድ፡ ቤት፡ይሆናሉ
፡ተለያይተው፡ ሦስቱ ፡በሁለቱ፡ ላይ፡ ሁለቱም፡ በሦ
ስቱ፡ላይ።
፶፫፡ አባት፡ በልጁ፡ ላይ፡ ይነሣል፡ ልጅም፡ ባባቱ፡ላ
ይ።እናት፡በልጅዋ፡ ልጅም፡ በናትዋ፡ላይ። አማት፡ በ
ምራቷ፡ ምራትም፡ ባማትዋ፡ላይ። ሚክ፡ ፯፡ ፮፡፡
፶፬፡ ደግሞም፡ለሕዝብ፡አለ። *ደመና፡ከምዕራ
ብ፡ ወጥቶ ፡ ባያችሁ፡ጊዜ፡ ለጊዜው ፡ ትላላችሁ ። ዝና
ም፡ይመጣል።እንደሁም፡ይሆናል። *ማቴ፡ ፲፮፡ ፪፡፡
፶፭፡ በአዜብም፡ነፋስ፡በነፈሰ፡ጊዜ፡ ትላላችሁ። ት
ኩሳት፡ ይሆናል። እንደሁም፡ ይሆናል።
፶፮፡ እላንት፡ ግብዞች፡ የምድሩንና፡ የሰማዩን፡ ፊ
ት፡ትመረምሩ፡ዘንድ፡ታውቃላችሁ። ይህነንም፡ዘመ
ን፡እንደ፡ ምን፡አትመረምሩት። ዮሐ፡ ፬፡ ፴፭፡፡
፶፯፡ ነገር፡ግን፡ምነው፡ከነፍሳችሁ፡ በውነት፡ አትፈ
ርዱ።
፶፰፡ በሔድህም፡ጊዜ፡ወደ፡አገር፡ጌታ፡ ከጸላትህ፡
ጋራ፡በመንገድ፡ዝም፡የሚያሰኘው፡ ነገር፡ ስጠው፡ ከ
ርሱ፡ትድን፡ዘንድ፡ አገር፡ ወደሚገዛ፡ እንደይጐትህ፡
ያገሩ፡ ጌታም፡ ለአጋዡ፡ አሳልፎ፡ ይሰጥሃል ። አጋዡ
ም፡በግዞት፡ ያኖርሃል። ዕብ፡ ፲፪፡ ፲፬፡፡
፶፱፡ እልሃለሁ፡ ከዚያ፡ እንደትወጣ ፡ ኋለኛውን፡
ዲናር፡ እስክትሰጥ፡ ድረስ። ማቴ፡ ፭፡ ፳፭፡፡

ምዕራፍ፡ ፲፫፡

፩፡ በዚያም፡ወራት፡ሰዎች፡መጡ፡ነገሩትም፡ ስለ፡
ገሊላውያን፡ ጲላጦስ ፡ ደማቸውን፡ ያደባለቀው፡ ከ
መሥዋዕታቸው ፡ ጋራ።
፪፡ የሱስም፡ መለሰ፡ አላቸውም ። ይመስላችኋል
ን፡እሌህ፡የገሊላ፡ሰዎች፡ ኃጢአተኞች፡ የነበሩ፡ ከገሊ
ላ፡ሰዎች፡ሁሉ፡ ይልቅ። እንደህ፡ያለ፡ መከራ፡ ስላገኛ
ቸው። ዮሐ፡ ፱፡ ፪፡
፫፡ እላችኋለሁ፡አይደለም።ነገር፡ግን፡ንስሐ፡ *ባት
ገቡ፡ሁላችሁ፡እንደሁ፡ትጠፋላችሁ። *መዝ፡ ፯፡ ፲፫፡፡
፬፡ ወይስ፡እለዚያ፡ አሥራ፡ ስምንቱ፡ ግምብ፡ የወ
ደቀባቸው፡በሰሊሆም፡የገደላቸውም።ይመስላችኋ
ልን፡ኃጢአት፡የነበረባቸው፡በየሩሳሌም፡ከነበሩ፡ሰዎ
ች፡ሁሉ፡ይልቅ። ነህም፡ ፫፡ ፲፭፡ ዮሐ፡ ፱፡ ፯፡፡
፭፡ አይደለም፡እላችኋለሁ።ነገር፡ ግን፡ ንስሐ፡ ባት
ገቡ፡ ሁላችሁም፡ እንደሁ፡ ታልቃላችሁ።
የሐዋ፡ ፫፡ ፲፱፡፡
፮፡ ይህነንም፡ምሳሌ፡ አለ። ላንድ፡ሰው፡ በለስ፡ ነበ
ረች፡ በወይኑ፡ ስፍራ፡ የተተከለች። ፍሬም፡ ሊሻባት፡
መጣ፡ አላገኘምም። ኢሳ፡ ፭፡ ፪፡፡ ማቴ፡ ፳፩፡ ፲፱፡፡
፯፡ አታክልት፡ጠባቂውንም፡አለው።እነሆ፡ሦስት፡
አመት፡ መጣሁ፡ ፍሬ፡ልሻ፡ ከዚች፡ በለስ፡ ያላገኘም
ም። ቍረጣት፡ ለምን፡ ምድር፡ ታጠፋለች።
፰፡ እርሱ፡ ግን፡ መለሰ፡ አለም። አቤቱ፡ ይህነን፡አ
መት፡ ደግሞ፡ ተዋት ። ዙርያዋን፡ እስካርስላት፡ ድረ
ስ፡ ፋንድያም፡ እስካፈስላት። ፪፡ ጴጥ፡ ፫፡ ፱ ፲፭፡፡
፱፡ ፍሬም፡ ብታደርግ፡ መልካም፡ ነው። ባታመጣ፡
ግን፡ኋላ፡ ትቈርጣታለህ። ማቴ፡ ፯፡ ፲፱፡
፲፡ እርሱም፡ ሲያስተምር ፡ ባንድ፡ መስጊድ፡ በሰን
በት።
፲፩፡ እነሆ፡ሴት፡ ከዚያ ፡ ነበረች፡ በታመመ፡ መንፈ
ስ፡የተያዘች፡ካሥራ፡ስምንት፡ አመት፡ጀምሮ።ጎባጣ
ም ፡ ነበረች ፡ ትቀናም ፡ ዘንድ ፡ ከቶ፡ አልተቻላትም።
፲፪፡ የሱስም፡አያትና፡ ጸራት፡ አላትም። አንቺ፡ሴ
ት፡ ከደዌሽ፡ ተፈተሻል።
፲፫፡ እጆቹንም፡ *በላይዋ፡ ጫነባት ። የዚያን፡ ጊዜ
ውም፡ ቀናች፡ እግዚአብሔርንም፡ አመሰገነች።
ማር፡ ፯፡ ፴፪፡፡
፲፬፡ የመስጊዱ፡አለቃም፡ኢየተቈጣ፡የሱስ፡በሰን
በት፡ስለ፡ፈወሰ፡መለሰ፡ሕዝቡንም፡አለ።ሰድስት፡ቀ
ን፡አለላችሁ፡ማድረግ፡ የሚገባበት።በርሱ፡ ኑ፡ ተፈወ
ሱም፡በሰንበትም፡ቀን፡ አይደለም። ዘፀአ፡ ፳፡ ፱፡፡

፲፭፡ ጌታም፡መለሰለት፡አለም። አንተ፡ግብዝ። ከ
ላንት፡ኢያንዳንዱ፡በሰንበት፡በሬውን፡ወይስ፡ አህያ
ውን፡ከሠራቱ፡ ይፈታ፡ የለምን፡ ሊያጠጣውስ፡ ይወ
ስደው፡ የለምን። ም፡ ፲፬፡ ፭።

፲፮፡ ይህችም፡እርስዋ፡ደግሞ፡*የአብርሃም፡ልጅ፡
ሰይጣን፡አሥርዋታል፡ እነሆ፡ ካሥራ፡ ስምንት፡ አመ
ት፡ጀምሮ።አይገባምን፡ከዚህ፡እሥራት፡ ትፈታ፡ዘን
ድ፡ በሰንበት፡ ቀን። *ም፡ ፲፱፡ ፱፡

፲፯፡ ይህንንም፡ ባለ፡ ጊዜ፡ በርሱ፡ የተነሡበትን፡ ሁ
ሉ፡አሳፈረ።ሕዝቡም፡ሁሉ፡ደስ፡ይላቸው፡ ነበር፡ ከር
ሱ፡ በሆነችው፡ በተመሰገነችው፡ በማድርጉ፡ ሁሉ።

፲፰፡ ይልም፡ ነበር። የእግዚአብሔር፡ መንግሥት፡
ምን፡ ትመስላለች። በምንስ፡ እመስላታለሁ።
ማቴ፡ ፲፫፡ ፴፩፡—፴፪። ማር፡ ፬፡ ፴—፴፪።

፲፱፡ የሰናፍጭ፡ ቅንጣት፡ ትመስላለች፡ ሰው፡ የወ
ሰደት፡ ባታክልቱም፡ የዘራት። በቀለችም፡ ታላቅ፡
ዛፍም፡ ሆነች፡ የሰማይም፡ ወፎች፡ በጫፎችዋ፡ ተቀ
መጡ።

፳፡ ደግሞም፡ አለ። የእግዚአብሔርን፡ መንግሥ
ት፡በምን፡እመስላለሁ።

፳፩፡ እርሾ፡ትመስላለች፡ሴት፡ የወሰደችው፡በሶስ
ትም፡ መስፈርያ፡ ደቄት፡ ሸሸገችው፡ ሁሉ፡ እስኪመ
ጥ፡ ድረስ። ማቴ፡ ፲፫፡ ፴፫።

፳፪፡ ወደገርም፡ወደ፡መንደርም፡ኢየሔደ፡ ያስተ
ምር፡ነበር። ወደ፡የሩሳሌምም፡ፊቱን፡አቅንቶ፡ነበረ።

፳፫፡ አንድ፡ሰውም፡አለው።አቤቱ፡ ጥቂትን፡ ናቸ
ው፡የሚድኑ። እርሱ፡ግን፡ አላቸው። ማቴ፡ ፯፡ ፲፬።

፳፬፡ ተጋደሉ፡ በጠባብ፡ ደጅ፡ ለመግባት። እላችኋ
ለሁና፡ ብዙ፡ ሰዎች፡ ለመግባት፡ ይሻሉ፡ አይችሉም
ም። ሮሜ፡ ፱፡ ፴፩። ፊል፡ ፫፡ ፲፪።

፳፭፡ የቤቱ፡ ባለ፡ ቤት፡ ተነሥቶ፡ ደጁን፡ በቈለፈ፡
ጊዜ፡በሚደ፡ቁማችሁ፡ትዘጋያላችሁ፡ደጅም፡ ትመታ
ላችሁ፡እንዲህ፡ስትሉ። አቤቱ፡ ክፈትልን። መልሶም፡
ይላችኋል። አላውቃችሁም፡ እላንት፡ የወዴት፡ ናች
ሁ። ማቴ፡ ፳፭፡ ፲፩፡ ፲፪፡

፳፮፡ የዚያን፡ጊዜም፡ትሉ፡ትጀምራላችሁ።በፊት
ህ፡በላን፡ ጠጠንም። ባደባባያችንም፡ አስተማርህ።
ማቴ፡ ፯፡ ፳፪፡ ፳፫።

፳፯፡ ይላልም።እላችኋለሁ፡አላውቃችሁም፡ የወ
ዴት፡ ናችሁ። ከኔ፡ ሒዱ፡ ግፍ፡ የምታደርጉ፡ ሁሉ።
ማቴ፡ ፰፡ ፲፩፡ ፲፪። መዝ፡ ፮፡ ፰።

፳፰፡ ከዚያ፡ልቅሶ፡ይሆናል፡ ጥርስም፡ ማፋጨት።
አብርሃምን፡ ባያችሁ፡ ጊዜ፡ ይስሐቅንም፡ ያዕቆብን
ም፡ነቢያትንም፡ ሁሉ፡ በእግዚአብሔር፡ መንግሥት፡
እላንትም፡ በሚደ፡ ተጥላችሁ።

፳፱፡ ከምሥራቅና፡ከምዕራብም፡ ይመጣሉ፡ከሰ
ሜንም፡ ከደቡብም፡ በእግዚአብሔር፡ ምንግሥት
ም፡ ይቀመጣሉ። ኢሳ፡ ፪፡ ፪፡ ፫። ፰፡ ፬።

፴፡ እነሆም፡ወደ፡ኋላ፡ ከሚሆኑት፡ ወደ፡ ፊት፡ ይ
ሆናሉ።በፊትም፡ከሚሆኑት፡በኋላ። ማቴ፡ ፲፱፡ ፴።

፴፩፡ በዚያም፡ ቀን፡ ከፈሪሳውያን፡ ሰዎች፡ ወደር
ሱ፡መጡ፡እንዲህ፡ ሲሉት። ውጣ፡ ሒድም፡ ከዚህ።
ሄሮድስ፡ሊገድልህ፡ ይሸሃልና። ም፡ ፱፡ ፯።

፴፪፡ አላቸውም። ሒዱ፡ ለዚችም፡ ቀበሮ፡ በልዋ
ት። እነሆ፡እኔ፡ ሰይጣናትን፡ አወጣለሁ፡ ፈውስንም፡
እፈጽማለሁ፡ዛሬና፡ነገ።በሶስተኛውም፡ ቀን፡እፈጸ
ማለሁ።

፴፫፡ ነገር፡ግን፡ይገባኛል፡እሔድ፡ዘንድ፡ዛሬ፡ነገም፡
በሚመጣውም፡ቀን። አይገባምና፡ ነቢይ፡ ይሞት፡ ዘ
ንድ፡ ከየሩሳሌም፡ በሚደ።
ም፡ ፯፡ ፲፮። ዮሐ፡ ፲፩፡ ፱።

፴፬፡ የሩሳሌም፡የሩሳሌም፡ሆይ፡አንቺ፡ነቢያትን፡
ገደይ፡ ወደንች፡ የተላኩትም፡ ወጋሪ፡ ስንተግዜ፡ ወደ
ድሁ፡ ልጆችሽን፡ እሰበስብ፡ ዘንድ። ዶሮ፡ ጫጩቶችዋ
ን፡በክንፍዋ፡ታች፡እንድትሰበስብ፡ እምቢም፡ አላች
ሁ። ማቴ፡ ፳፫፡ ፴፯፡—፴፱።
መዝ፡ ፲፯፡ ፰። ፺፩፡ ፬።

፴፭፡ እነሆ፡ቤታችሁ፡ፈርሶ፡ ይቀርላችኋል። እውነ
ትም፡እላችኋለሁ፡እንደታዩኝ፡ ዘመኑ፡ እስኪመጣ፡
ድረስ፡የምትሉበት። በእግዚአብሔር፡ ስም፡የሚመ
ጣ፡ የተባረከ፡ ነው። መዝ፡ ፷፱፡ ፳፮። ፻፲፰፡ ፳፮።
ኤር፡ ፯፡ ፲፬፡ ፲፭። ሚክ፡ ፫፡ ፲፪።

ምዕራፍ፡ ፲፬፡

፩፡ ከፈሪሳውያንም፡አለቆች፡ ወደንዱ፡ ቤት፡ በሰ
ንበት፡እንጀራ፡ ይበላ፡ ዘንድ፡ በገባ፡ ጊዜ፡ እርሳቸው፡
ያደቡት፡ ነበር። ም፡ ፮፡፮፡—፲። ፲፩፡ ፴፯።

፪፡ እነሆም፡ የተኰደኰደ፡ ሰው፡ ሆዱ፡የተነፋ፡ በ
ፊቱ፡ ነበረ።

፫፡ የሱስም፡ መለሰ፡ ባላ፡ኦሪቶችንና፡ ፈሪሳውያን
ን፡ጠየቀ፡ እንዲህ፡ ሲል። ይገባልን፡ በሰንበት፡ ይፈወ
ስ፡ዘንድ። ማቴ፡ ፲፪፡ ፲፡ ፲፩።

፬፡ እርሳቸው፡ግን፡ ዝም፡አሉ። ወሰደውም፡ ፈወ
ሰውም፡ሰደደውም።

፭፡ መለሰላቸውም፡አለም።ማነው፡ ከላንት፡አህ
ያው፡ወይስ፡በሬው፡በጕድጓድ፡ቢወድቅበት፡የማያ
ነሣው፡ በሰንበት፡ ቀን።
ም፡ ፲፫፡ ፲፭። ዘፀአ፡ ፳፩፡ ፴፫፡

፮፡ በዚህም፡ ይመልሱለት፡ ዘንድ፡ አልቻሉም።

፯፡ ምሳሌም፡ ተናገረ፡ ለተጸሩት፡ የመቀመጫው
ን፡ላይ፡እንዲመርጡ፡ባየ፡ጊዜ፡አላቸውም።
ማቴ፡ ፳፫፡ ፮።

፰፡ ከማንም፡ ወደ፡ ሰርግ፡ በተጸራህ፡ ጊዜ፡ በላይ፡
መቀመጫ፡ አትቀመጥ።ምናልባት፡ አንድ፡ሰው፡ ጸር
ቶ፡ እንደሆን፡ ካንተ፡ የሚበልጥ፡ በክብሩ።
ምሳ ፳፱፡ ፳፫።

፱፡ አንተንም፡እርሱንም፡ የጸራ፡ ይመጣል፡ ይልሃ

ልም።ስፍራውን፡ለዚህ፡ተውለት። የዚያን፡ ጊዜም፡ ታፍር፡ትጀመራለህ፡ዝቅ፡ ያለውንም፡ ስፍራ፡ ትወስ ዳለህ።

፲፤ ነገር፡ ግን፡ በተጸራህ፡ ጊዜ፡ ሒድና፡ ከመጨረሻ ው፡ስፍራ፡ተቀመጥ። ያ፡የጸራህ፡ መጥቶ፡ ዷልህ፡ ዘን ድ።ወዳጄ፡ሆይ፡ወደ፡ላይ፡ከፍ፡በል። የዚያን፡ጊዜ፡ ክ ብር፡ይሆንልሃል፡ ካንተ፡ጋራ፡ በተቀመጡት፡ፊት።

፲፩፤ ራሱን፡ከፍ፡ያደረገ፡ሁሉ፡ ይዋርዷልና። ራሱን ም፡ ያዋረደ፡ ከፍ፡ ይላል። ምሳ፡ ፳፱፡ ፳፫።
ማቴ፡ ፳፫፡ ፲፪።

፲፪፤ ደግሞም፡አለው፡ለጸራው፡ሰው።ምሳ፡ ባደረ ግህ፡ጊዜ፡ወይም፡እራት፡ ወዳጆችህን፡ አትጥራ፡ ወን ድሞችህንም፡ዘመዶችህንም፡ ባለጠጎችንም፡ ጎረቤ ቶችህን።ምናልባት፡ይጸሩሃልና፡ ደግሞ፡ ብድራት፡ ይ ሆንብሃል።

፲፫፤ ነገር፡ግን፡ ምሳ፡ ባደረግህ፡ጊዜ፡ ድኆችን፡ ጥራ፡ ጉንድሾችንም፡ አንካሶችን፡ ዕውሮችን።
ዘዳግ፡ ፲፬፡ ፳፱።

፲፬፤ ምስጋንም፡ ይገባሃል። የሚከፍሉህ፡የላቸው ምና።ዋጋህም፡ይሆናል፡ በጻድቃን፡ *ትንሣኤ።
*ዮሐ፡ ፭፡ ፳፱።

፲፭፤ አንድም፡ከርሱ፡ጋራ፡ ከተቀመጡት፡ ይህነን፡ በሰማ፡ጊዜ፡ አለው። ምስጋና፡ ይገባዋል፡ በእግዚአብ ሔር፡ መንግሥት፡ እንጀራ፡ ለሚበላ።
ም፡ ፲፫፡ ፳፱። መዝ፡ ፴፮፡ ፱።

፲፮፤ እርሱ፡ግን፡አለው።ሰው፡ታላቅ፡ምሳ፡አደረገ፡ ብዙ፡ሰዎችም፡ጸራ። ማቴ፡ ፳፪፡ ፪—፲።

፲፯፤ ባርያውንም፡ ላከ፡ በምሳ፡ጊዜ፡ የተጸሩትን፡ ይል፡ ዘንድ። ኑ፡ አሁን፡ ሁሉ፡ ተዘጋጅቶዋልና።

፲፰፤ ሁሉም፡ ባንድ፡ ይንቁ፡ ጀመሩ። የፊተኛው፡ አለው። ምድር፡ ገዝቻለሁ፡የግድም፡ ያሻኛል፡ ወደር ሱ፡ መውጣት፡ አየው፡ዘንድ። እለምንሃለሁ፡ እንድ ተወኝ።

፲፱፤ ሌላውም፡አለ። አምስት፡ ጥምድ፡ በሮች፡ ገ ዝቻለሁ፡ ልፈትናቸውም፡ እሔዳለሁ። እለምንሃለ ሁ፡ ትተወኝ፡ ዘንድ።

፳፤ ሌላውም፡ አለው። ምሽት፡ አግብቻለሁ፡ ስለ ዚህም፡ መምጣት፡ አይቻለኝም። ፩፡ ቆሮ፡ ፯፡ ፴፫።

፳፩፤ ያም፡ ባርያ፡ በመጣ፡ ጊዜ፡ ይህነን፡ ለጌታው፡ ነገረው። የዚያን፡ ጊዜም፡ ባለቤቱ፡ ተቈጣ፡ ባርያው ንም፡ አለው። ፈጥነህ፡ ወደ፡ አደባባይ፡ ውጣ፡ ወደገ ሩም፡ ገቢያ። ድኆችንም፡ ጉንድሾችንም፡አንካሶችን ም፡ ዕውሮችንም፡ ወደዚህ፡ አግባ።

፳፪፤ ባርያውም፡ አለ። አቤቱ፡ እንዳልኸኝ፡አደረ ግሁ፡ ከዚህም፡ ደግሞ፡ ስፍራ፡ አለ።

፳፫፤ ጌታውም፡ ባርያውን፡ አለ። ወደ፡ መንገድ፡ ወደጥርም፡ ውጣ፡ የግድም፡ በላቸው፡ ይገቡ፡ዘንድ፡ ቤቴ፡ ይመላ፡ ዘንድ። ዘፍ፡ ፲፱፡ ፫።

፳፬፤ እላችኋለሁ፥ ከለዚህ፡ ሰዎች፡ ከተጸሩት፡ አ ንድ፡ ሰንኳ፡ እንጀራዬን፡ እንደይቀምሰው።
ማቴ፡ ፳፩፡ ፵፫።

፳፭፤ ብዙ፡ ሰዎችም፡ ከርሱ፡ ጋራ፡ ይሔዱ፡ ነበሩ። ተመለስም፡ አላቸውም። ም፡ ፲፰፡ ፳፱፡ ፴።
ማቴ፡ ፲፡ ፴፯፡ ፴፰።

፳፮፤ ማንም፡ ወደኔ፡ የሚመጣ፡ አባቱንና፡ እናቱ ንም፡ የማይጸላ፡ ምሽቱንም፡ልጆቹንም፡ወንድሞቹ ንም፡ እኅቶቹንም፡ደግሞ፡ ነፍሱንም፡አይችልም፡ለኔ፡ ደቀ፡ መዝሙር፡ ይሁን፡ ዘንድ።
ዘዳግ፡ ፲፫፡ ፮። ፴፫፡ ፱።

፳፯፤ መስቀሉንም፡ የማይሸከም፡ በኋላዬም፡ የ ማይመጣ፡ ለኔ፡ደቀ፡መዝሙር፡ መሆን፡አይችልም።
ም፡ ፱፡ ፳፫። ማር፡ ፰፡ ፴፬።

፳፰፤ ማነው፡ ከላንት፡ ግምብ፡ መስራት፡ የሚወ ድ፡ አስቀድሞስ፡ የማይቀመጥ፡ የሚፈጅበትንስ፡ የ ማይቈጥር፡ ይጨርሰው፡ዘንድ፡የሚችል፡እንደሆን።

፳፱፤ መሠረት፡ ባደረገ፡ጊዜ፡ መጨረሱን፡ ባይችል፡ ያዩት፡ ሁሉ፡ ይስቁበት፡ እንደይጀምሩ።

፴፤ እንዲህ፡ ሲሉ። ይህ፡ ሰው፡ ሰራ፡ ጀመረ፡ ሊጨ ርሰውም፡ አልተቻለውም።

፴፩፤ ወይስ፡ ማን፡ ንጉሥ፡ ነው፡ ሌላውን፡ ንጉሥ፡ በሰልፍ፡ ለመገናኘት፡ የሚሔድ። አስቀድሞ፡ ተቀ ምጦ፡ የማያስብ፡ በአልፍ፡ ይችላልን፡ በሁለት፡ እል ፍ፡ የሚመጣበትን፡ ያገኘው፡ ዘንድ።

፴፪፤ ወይም፡ከርሱ፡ በሩቅ፡ ሳለ፡ መልክተኞች፡ ይ ልካል፡ለመታረቅም፡ ይለምነዋል። ኢሳ፡ ፵፭፡ ፳፬።

፴፫፤ እንደዚሁም፡ ከላንት፡ ሁላችሁ፡ ከብቱን፡ ሁ ሉ፡ያልተወ፡አይችልም፡ ለኔ፡ ደቀ፡ መዝሙር፡ ይሆ ን፡ ዘንድ። ማቴ፡ ፲፫፡ ፵፬።

፴፬፤ ጨው፡ መልካም፡ ነው። ጨው፡ ግን፡ አልጫ፡ ከሆነ፡ በምን፡ ይጣፈጣል። ማቴ፡ ፭፡ ፲፫።
ማር፡ ፱፡ ፶።

፴፭፤ ለምድርም፡ለእበት፡ መደብም፡አይረባም። ነገር፡ ግን፡ ወደ፡ ሜዳ፡ ይጥሉታል። የሚሰማ፡ ጆሮ፡ ያ ለው፡ ይስማ። ም፡ ፰፡ ፰።

## ምዕራፍ፡ ፲፭፤

፩፤ ወደርሱም፡ ቀረቡ፡ ቀራጮች፡ሁሉ፡ ኃጢአተኞ ችም፡ ከርሱ፡ ሊሰሙ። ም፡ ፭፡ ፳፱፡ ፴።

፪፤ ፈሪሳውያንና፡ ጻፎችም፡አንጐረጐሩ፡እንዲህ፡ ሲሉ። ይህስ፡ ኃጢአተኞችን፡ ይቀበላል፡ ከርሳቸው ም፡ ጋራ፡ ይበላል።

፫፤ ይህነን፡ ምሳሌም፡ ነገራቸው፡ እንዲህ፡ ሲል።
ማቴ፡ ፲፰፡ ፲፪—፲፬።

፬፤ ማን፡ ሰው፡ ከላንት፡ ነው፡ መቶ፡ በግ፡ ያለው። ከርሳቸው፡ አንዱ፡ ቢጠፋ፡ ዘጠና፡ዘጠኙን፡በምድረ፡ በዳ፡ ይተው፡ የለምን፡ ይሔድስ፡ የለምን፡ወደ፡ጠፋ ው፡ እስኪያገኘው፡ ድረስ። ሕዝ፡ ፴፬፡ ፲፩፡ ፲፮።

፭፡ ባገኘውም፡ ጊዜ፡ ደስ፡ ብሎት፡ በጫንቃው፡ ላይ፡ ይሸከመዋል። ኢሳ፡ ፵፡ ፲፩።

፮፡ ወደ፡ ቤትም፡ በመጣ፡ ጊዜ፡ ወዳጆቹንና፡ ጎረቤቶቹን፡ ይጸራል፡ እንደዚህ፡ ሲላቸው። ከኔ፡ ጋራ፡ ደስ፡ ይበላችሁ፡ የጠፋውን፡ በጌን፡ ስላገኘሁ።
፩፡ ጴጥ፡ ፪፡ ፳፭።

፯፡ እላችኋለሁ። እንደሁ፡ ደስታ፡ በሰማይ፡ እንዲሆን፡ ንስሐ፡ በሚገባ፡ ባንድ፡ ኃጢአተኛ፡ ከዘጠና፡ ዘጠኝ፡ ጻድቃን፡ ይልቅ፡ ንስሐ፡ የማይሹ። ም፡ ፭፡ ፴፪።

፰፡ ወይስ፡ ምን፡ ሴት፡ ናት፡ አሥር፡ ድሪም፡ ያላት። አንድ፡ ድሪም፡ ባጠፋች፡ ጊዜ፡ መብራት፡ ታበራ፡ የለችምን፡ ቤቱንም፡ ትጸርጋለች፡ ተግታም፡ ትሻዋለች፡ እስክታገኘው፡ ድረስ።

፱፡ ባገኘችውም፡ ጊዜ፡ ወዳጆችዋን፡ ትጸራለች፡ ጎረቤቶችዋንም፡ እንደዚህ፡ ስትል። ከኔ፡ ጋራ፡ ደስ፡ ይበላችሁ፡ የጠፋኝን፡ ድሪሜን፡ ስላገኘሁ።

፲፡ እንደሁ፡ እላችኋለሁ፡ ደስታ፡ እንዲሆን፡ በእግዚአብሔር፡ *መላእክት፡ ፊት፡ ንስሐ፡ በሚገባ፡ ባንድ፡ ኃጢአተኛ። *ኤፌ፡ ፫፡ ፲።

፲፩፡ አለም። ሰው፡ ሁለት፡ ልጆች፡ ነበሩት።

፲፪፡ ታናሹ፡ ላባቱ፡ አለው። አባቴ፡ ሆይ፡ ከከብቱ፡ የሚደርሰኝን፡ ክፍለህ፡ ስጠኝ። ከብቱንም፡ በመካከላቸው፡ ከፈለ።

፲፫፡ ከጥቂት፡ ቀንም፡ በኋላ፡ ታናሹ፡ ልጁ፡ ሁሉን፡ ሰበሰበ፡ ወደ፡ ሩቅም፡ አገር፡ መንገድ፡ ሔደ። *ከብቱንም፡ በተነ፡ በሳቅ፡ በዋዛም። *ምሳ፡ ፳፱፡ ፫።
፳፫፡ ፳፡ ፳፩።

፲፬፡ ያለውንም፡ ሁሉ፡ በጨረሰ፡ ጊዜ፡ ጽኑ፡ ራብ፡ ሆነ፡ በዚያች፡ አገር፡ እርሱም፡ ይቸ፡ ጀመረ።

፲፭፡ ሔደም፡ ተሰማማም፡ ከዚያች፡ አገር፡ ሰዎች፡ ካንዱ፡ ጋራ። ወደ፡ ግዛቱም፡ ሰደደው፡ እርያ፡ ይጠብቅ፡ ዘንድ።

፲፮፡ ይመኝም፡ ነበር፡ ሆዱን፡ ይመላ፡ ዘንድ፡ እርያ፡ ከሚበላው፡ አሠር። ያነንም፡ የሚሰጠው፡ አልነበረም። መዝ፡ ፲፯፡ ፲፫፡ ፲፬።

፲፯፡ ወደ፡ ልቡናውም፡ ተመለሰና፡ አለ። ስንት፡ ናቸው፡ ያባቴ፡ ባሮች፡ እንጀራ፡ ከርሳቸው፡ የሚተርፍ፡ እኔም፡ በራብ፡ እሞታለሁ። ኢሳ፡ ፵፮፡ ፰።

፲፰፡ ልነሣና፡ *ወዳባቴ፡ ልሒድ፡ ልበለውም። አባቴ፡ ሆይ፡ በሰማይ፡ †በፊትህም፡ በደልሁ።
*ኤር፡ ፫፡ ፲፪። †መዝ፡ ፶፩፡ ፬።

፲፱፡ ደግሞም፡ አይገባኝም፡ ልጅህ፡ እባል፡ ዘንድ። ከባሮችህ፡ እንዳንዱ፡ አድርገኝ።

፳፡ ተነሣና፡ ወዳባቱም፡ መጣ። እርሱም፡ ገና፡ በሩቅ፡ ሳለ፡ አባቱ፡ አየውና፡ አዘነ። ሩጦም፡ ባንገቱ፡ ላይ፡ ወደቀና፡ ሳመው። መዝ፡ ፻፫፡ ፲፫። ያዕ፡ ፬፡ ፰።

፳፩፡ ልጁም፡ አለው። አባቴ፡ ሆይ፡ በሰማይ፡ በፊትህም፡ በደልሁ። ደግሞም፡ አይገባኝም፡ ልጅህ፡ እባል፡ ዘንድ።

፳፪፡ አባቱም፡ ባሮቹን፡ አለ። የቀደመውን፡ ልብስ፡ አምጡና፡ አልብሱት። በጁም፡ ቀለበት፡ አድርጉለት፡ ጫማም፡ በግሩ። ኢሳ፡ ፷፩፡ ፲። ራእ፡ ፫፡ ፲፰።

፳፫፡ ማለፊያ፡ ፍሪዳም፡ አምጡና፡ እረዱ። እንብላም፡ ደስም፡ ይበለን።

፳፬፡ ይህ፡ ልጄ፡ *ሙቶ፡ ነበርና፡ ደህናም፡ ሆነ። ጠፍቶም፡ ነበረ፡ ተገኘም። ደስም፡ ይላቸው፡ ጀመሩ።
*ኤፌ፡ ፪፡ ፩፡ ፭። ፭፡ ፲፬።

፳፭፡ ታላቁ፡ ልጁም፡ በሜዳ፡ ነበረ። በመጣም፡ ወደ፡ ቤትም፡ በቀረበ፡ ጊዜ፡ የልልታ፡ ድምጽ፡ ዘፈንም፡ ሰማ።

፳፮፡ ከብላቴናችም፡ አንዱን፡ በጸራ፡ ጊዜ፡ ጠየቀ፡ ይህ፡ ምንድር፡ ነው፡ ብሎ።

፳፯፡ እርሱም፡ አለው፡ ወንድምህ፡ ስለ፡ መጣ። አባትህም፡ ማለፊያ፡ ፍሪዳ፡ አረደ፡ በደህና፡ መጥትዋልና።

፳፰፡ ተቈጣም፡ ሊገባም፡ አልወደደም። አባቱም፡ ወደርሱ፡ ወጣ፡ ለመነውም።

፳፱፡ እርሱ፡ ግን፡ መለሰ፡ አለውም። እነሆ፡ ስንት፡ አመት፡ አገለግልሃለሁ። አዘዝኸኝንም፡ ከቶ፡ እምቢ፡ ብዬ፡ አላውቅም። ጥቦትም፡ ስንኳ፡ አልሰጠኸኝም፡ ከባልንጀሮቼ፡ ጋራ፡ የምጫወትበት። ቍ፡ ፪።

፴፡ ይህም፡ ልጅህ፡ በመጣ፡ ጊዜ፡ ከብትህን፡ ሁሉ፡ የበላ፡ ከጋለሞቶች፡ ጋራ፡ ማለፊያ፡ ፍሪዳ፡ አረድህለት። ምሳ፡ ፳፱፡ ፫።

፴፩፡ እርሱ፡ ግን፡ አለው። ልጄ፡ ሆይ፡ አንተ፡ ሁልጊዜ፡ ከኔ፡ ጋራ፡ ነህ፡ ለኔም፡ ያለው፡ ሁሉ፡ እርሱ፡ ላንተ፡ ነው።

፴፪፡ ደስ፡ ማለት፡ ግን፡ ሐሤትም፡ ማድረግ፡ ይገባል። ይህ፡ ወንድምህ፡ ሙቶ፡ ነበርና፡ ተመልሶም፡ ሕያው፡ ሁንዋል፡ ጠፍቶም፡ ነበር፡ ተገኝቶዋልና።
ቀለ፡ ፪፡ ፫።

## ምዕራፍ፡ ፲፮፡

፩፡ ደግሞም፡ ለደቀ፡ መዛሙርቱ፡ አለ። ባለ፡ ጸጋ፡ ሰው፡ ነበረ፡ መጋቢም፡ ነበረው። ይህም፡ በርሱ፡ ዘንድ፡ ተከሰሰ፡ ከብቱን፡ እንዲበትን። ም፡ ፲፭፡ ፲፫።

፪፡ ጸራውም፡ አለውም። ባንተ፡ የምሰማው፡ ይህ፡ ምንድር፡ ነው። የመጋቢነትህን፡ ቍጥር፡ ስጠኝ። እንግዲህ፡ መጋቢ፡ ተሆነኝ፡ ዘንድ፡ አትችልምና።

፫፡ መጋቢውም፡ በልቡ፡ አለ። ምን፡ ላድርግ። ጌታዬ፡ መጋቢነቱን፡ ከኔ፡ ይወስዳልና። እርሻም፡ አልችልም፡ መለመንም፡ አፍራለሁ።

፬፡ አወቅሁ፡ የማደርገውን፡ መጋቢነት፡ ቀኔ፡ በወጣ፡ ጊዜ፡ ወደ፡ ቤታቸው፡ እንዲቀበሉኝ።

፭፡ ከጌታውም፡ ባለደች፡ አንድ፡ አንዱን፡ ጸራ። የፊተኛውንም፡ አለው። ምን፡ ያህል፡ አለብህ፡ ለጌታዬ።

፮፡ እርሱም፡ አለው። መቶ፡ ማድጋ፡ ቅባኑግ። አለ

ውም። ደብደቤህን፡ እንካ፡ ቶሎም፡ ተቀመጥ፡ አምሳ፡ ብለህም፡ ጻፍ።

፯፡ ደግሞ፡ ሌላውንም፡ አለ። አንተስ፡ ስንት፡ አለብህ። እርሱም፡ አለ። መቶ፡ ዌን፡ስንዴ። አለውም፡ ደብደቤህን፡ እንካ፡ ሰማንያም፡ ጻፍ።

፰፡ ጌታም፡ የግፍ፡ መጋቢውን፡አመሰገነው፡ በብልሃት፡ አድርጓልና። የዚህ፡ ዓለም፡ልጆች፡ብልሃተኞች፡ ናቸውና፡ *ከብርሃን፡ ልጆች፡ ይልቅ፡በዘመናቸው።

*ኤፌ፡ ፭፡ ፰፡፡ ፩፡ ተሰ፡ ፭፡ ፭፡፡

፱፡ እኔም፡ እላችኋለሁ። ለላንት፡ ወዳጆች፡ ግዙ፡ ከግፍ፡ ከብት።በጎደላችሁ፡ ጊዜ፡ በዘላለም፡ ቤቶች፡ ይቀበልዋችሁ፡ ዘንድ። ኢሳ፡ ፴፰፡ ፲፯፡ ፲፰፡፡

ማቴ፡ ፮፡ ፳፡—፳፱፡፡ ፲፡ ፵፡፡ ፲፱፡ ፳፩፡፡

፲፡ በጥቂት፡ የታመነ፡ደግሞ፡በብዙ፡ የታመነ፡ ይሆናል፡ በጥቂትም፡ ግፍ፡ የሚያደርግ፡ በብዙም፡ ደግሞ፡ ግፈኛ፡ ይሆናል። ም፡ ፲፱፡ ፲፯፡፡

፲፩፡ ባስት፡ከብት፡ካልታመናችሁ፡ማን፡በውነተኛ፡ ያምናችኋል።

፲፪፡ ለላንት፡ባልሆነውም፡ካልታመናችሁ፡ማነው፡ የላንት፡ያለውን፡ የሚሰጣችሁ።

፲፫፡ አንድ፡ሰው፡ ለሁለት፡ ጌታ፡ መገዛት፡ አይችልም። አንዱን፡ ካልጸላ፡ ሁለተኛውንም፡ ካልወደደ። ወይም፡ ላንዱ፡ እሺ፡ ይል፡ ዘንድ፡ ሁለተኛውንም፡ ይንቅ፡ ዘንድ። ለእግዚአብሔርና፡ ለከብት፡ ትገዙ፡ ዘንድ፡ አትችሉም። ማቴ፡ ፮፡ ፳፬፡፡

፲፬፡ ፈሪሳውያንም፡ ደግሞ፡ ይህነን፡ ሁሉ፡ ነገር፡ ይሰሙ፡ ነበሩ። እርሳቸውም፡ ብር፡ ይወዱ፡ ነበሩ። ያፌዙበትም፡ ነበሩ። ማቴ፡ ፳፫፡ ፲፬፡ ፲፭፡፡

፲፭፡ አላቸውም።እላንት፡ ነፍሳችሁን፡ *በሰው፡ ፊት፡ የምታጸድቁ፡ ናችሁ። እግዚአብሔር፡ ግን፡ ልባችሁን፡ †ያውቃል።በሰው፡ፊት፡ ††የሚጓደድ፡በእግዚአብሔር፡ ፊት፡ የተናቀ፡ ይሆናልና። *ም፡ ፲፰፡ ፱፡፡

†መዝ፡ ፯፡ ፲፡፡ ††ምሳ፡ ፮፡ ፲፮፡ ፲፯፡፡

፲፮፡ ኦሪት፡ ነቢያትም፡ እስከ፡ ዮሐንስ፡ ድረስ፡ ነበሩ። ከንጊዲህ፡ ወዲህ፡ ግን፡ በእግዚአብሔር፡ መንግሥት፡ ይነገራል፡ ሰውም፡ ሁሉ፡ ወደርስዋ፡ ይገፋል።

ማቴ፡ ፲፩፡ ፲፪፡ ፲፫፡፡

፲፯፡ ሰማይና፡ ምድርም፡ ያልፉ፡ዘንድ፡ ይቀላል፡ ከኦሪት፡ አንዲት፡ ነቍጣ፡ ክትወድቅ። ማቴ፡ ፭፡ ፲፰፡፡

፲፰፡ ምሽቱን፡ የፈታ፡ ሁሉ፡ ሌላዪቱንም፡ ያገባ፡ እርሱ፡ያመነዝራል። ከባልዋም፡ የተፈታችውን፡ ያገባ፡ ሁሉ፡እርሱ፡ያመነዝራል። ማቴ፡ ፭፡ ፴፪፡፡ ፲፱፡ ፰፡፱፡፡

፲፱፡ ባለ፡ ጸጋ፡ሰው፡ ነበረ። ቀይ፡ሐር፡ ነጭ፡ ሐርም፡ ይለብስ፡ ነበረ፡ ዕለት፡ ዕለትም፡ በጌጹ፡ ደስ፡ ይለው፡ ነበር። ዮሐ፡ ፰፡ ፲፯፡፡ ራእ፡ ፲፰፡ ፲፪፡፡

፳፡ ድኃም፡ ስሙን፡ አልዓዛር፡ የሚሉት፡ ነበረ። በደጁም፡ ወድቆ፡ ነበረ፡ በቍስል፡ ተወርሶ።

፳፩፡ ያምረውም፡ ነበረ፡ሆዱን፡ያጠግብ፡ ዘንድ፡ ከባለ፡ጸጋው፡ ማዕድ፡ከሚወድቀው፡ፍርፋሪ። ደግሞ፡ ውሾችም፡ መጥተው፡ ቍስሉን፡ ይልሱት፡ ነበር።

ማቴ፡ ፲፭፡ ፳፯፡፡

፳፪፡ ጊዜውም፡ ሲደርስ፡ ድኃው፡ ሞተ። መላእክትም፡ ወደ፡ አብርሃም፡ ጭን፡ ወሰዱት።

ማቴ፡ ፰፡ ፲፩፡፡ ዮሐ፡ ፲፫፡ ፳፫፡፡

፳፫፡ ባለ፡ጸጋውም፡ ደግሞ፡ ሞተ፡ ተቀበረም። በሢኦልም፡ ዓይኑን፡ ባነሣ፡ጊዜ፡ እርሱ፡ በሥቃይ፡ሳለ፡ አብርሃምን፡ ከሩቅ፡ አየ፡ አልዓዛርንም፡ በጭኑ።

፳፬፡ እርሱም፡ ጸራ፡ አለም። አባቴ፡ ሆይ፡ አብርሃም፡ ማረኝ። አልዓዛርንም፡ ስደድልኝ፡የጻቱን፡ጫፍ፡ በውኃ፡ነክሮ፡ምላሴን፡ያበርድልኝ፡ዘንድ። በዚህ፡ ነበልባል፡ እሣቀያለሁና። መዝ፡ ፵፱፡ ፲፭፡፡

፳፭፡ አብርሃምም፡አለ። ልጄ፡ሆይ፡ አስብ፡አንተ፡ ተድላህን፡ ፈጽመህ፡ እንደ፡ ተቀበልህ፡በሕይወትህ፡ ሳለህ። አልዓዛርም፡ ደግሞ፡ እንደሁ፡ መከራ። አሁንም፡ እርሱ፡ ደስ፡ ይለዋል፡ አንተም፡ ትሣቀያለህ።

መዝ፡ ፲፯፡ ፲፬፡ ፲፭፡፡ ፵፱፡ ፲፰፡ ፲፱፡፡

፳፮፡ ከዚህም፡ ሁሉ፡በላይ፡ በኛና፡ በላንት፡መካከል፡ ታላቅ፡ ገደል፡ አለ። ከዚህ፡ ወደላንት፡ ማለፍ፡ የሚሹ፡እንዳይችሉ። ከዚያም፡ ያሉ፡ ወደኛ፡ እንደያልፉ።

፳፯፡ አለም። እንኪያስ፡እለምንሃለሁ፡ አባቴ፡ ሆይ፡ ወደአባቴ፡ ቤት፡ ትሰደው፡ ዘንድ።

፳፰፡ አምስት፡ ወንድሞች፡አሉኝና፡ እንዲመሰክርላቸው፡ እርሳቸውም፡ ደግሞ፡ ወደዚህ፡ ሥቃይ፡ ስፍራ፡ እንደይመጡ።

፳፱፡ አብርሃምም፡ አለው። ሙሴ፡ ነቢያትም፡ አሉዋቸው፡እርሳቸውን፡ይስሙ። ኢሳ፡ ፰፡ ፳፡፡

ዮሐ፡ ፭፡ ፴፱፡፡ ፪፡ ጢሞ፡ ፫፡ ፲፯፡፡

፴፡ እርሱም፡ አለ። አይደለም፡ አባቴ፡ ሆይ፡ አብርሃም። ነገር፡ ግን፡ ከሞቱት፡ አንድ፡ ቢሔድባቸው፡ ንስሐ፡ ይገባሉ።

፴፩፡ አብርሃምም፡አለው።ከሙሴና፡ከነቢያትስ፡ ካልሰሙ፡ ከሙታንም፡አንድ፡ ቢነሣ፡ አያምኑትም።

ዮሐ፡ ፲፩፡ ፵፮፡ ፵፯፡፡ ፲፪፡ ፱፡ ፲፡፡

ምዕራፍ፡ ፲፯፡

፩፡ ደቀ፡ መዛሙርቱንም፡ አለ። ማሰናከያ፡ሳይመጣ፡አይቀርም። ነገር፡ግን፡ወዮለት፡ ማሰናከያ፡በርሱ፡ ምክንያት፡ለሚመጣው፡ ሰው።

፪፡ *ይሻለው፡ ነበረ፡ የወፍጮ፡ደንጊያ፡ ባንገቱ፡ አስሮ፡ ወደ፡ ባሕር፡ ቢወድቅ፡ ከለዚህ፡ ከታናኖቹ፡ አንዱን፡ ኪያስት። *ማቴ፡ ፲፰፡ ፯፡፡ ማር፡ ፱፡ ፵፪፡፡

፫፡ ለሰውነታችሁ፡ ተጠበቁ። ወንድምህም፡ቢበድልህ፡ *ተቈጣው። ቢመለስም፡ ይቅር፡በለው።

*ዘሌዋ፡ ፲፱፡ ፲፯፡፡ ማቴ፡ ፲፰፡ ፲፭፡፡

፬፡ በቀንም፡ ሰባት፡ ጊዜ፡ ቢበድልህ። ሰባት፡ ጊዜ

ም፡ በቀን፡ ወደንተ፡ ቢመለስ፡ እንዴህ፡ ቢል። እኔ፡ ተ
መልሻለሁ። ይቅር፡ በለው።
፭፡ ሐዋርያትም፡ጌታን፡ አሉት። ሃይማኖት፡ *አብ
ዛልን። *ማር፡ ፱፡ ፳፬፡፡
፮፡ ጌታም፡ አለ። ሃይማኖትስ፡ *ቢኖራችሁ፡እንደ
ሰናፍጭ፡ ቅንጣት። ይህነን፡ ሾላ፡ ተነቀል፡ ወደ፡ ባሕር
ም፡ ተተከል፡ ትሉት፡ ነበራችሁ። እርስዋም፡ ትታዘዛ
ችሁ፡ ነበረች። *ማቴ፡ ፲፯፡ ፳፡፡ ፳፩፡ ፳፩፡፡
፯፡ ከላንተስ፡ ማነው፡ ባርያ፡ ያለው፡ የሚያርስ፡ የ
ሚጠብቅስ። ከርሻ፡ በተመለሰ፡ ጊዜ፡ ይለዋልን፡ ለጊ
ዜው፡ እለፍና፡ ለራት፡ ተቀመጥ።
፰፡ ነገር፡ ግን፡ ይለው፡የለምን፡ ራቴን፡ አስናዲልኝ።
ወገብህንም፡ታጥቀህ፡አገልግለኝ፡ እስክበላ፡እስክጠ
ጣም፡ ድረስ። ከዚያም፡ በኋላ፡ አንተ፡ ትበላለህ፡ ት
ጠጣማለህ።
፱፡ ወይስ፡ያነን፡ባርያ፡ ያመሰግነዋልን፡ ያዘዘውን፡
ስላደረገ። አይመስለኝም።
፲፡ እንዴሁ፡እላንትም፡ የታዘዛችሁትን፡ ሁሉ፡ ባደ
ረጋችሁ፡ ጊዜ፡ በሉ። እኛ፡ የማንረባ፡ ባሮች፡ ነን። እናደ
ርገው፡ ዘንድ፡ የሚገባንን፡ አደረግነው።
፲፩፡ ወደ፡ የሩሳሌም፡ ሲሔድ፡ *በሰማርያና፡ በገሊ
ላ፡ መካከል፡ አለፈ። ዮሐ፡ ፬፡ ፬፡፡
፲፪፡ እርሱም፡ ወደንዲት፡ አገር፡ ሲገባ፡ተቀበሉት፡
አሥር፡ ሰዎች፡ ለምጻሞች፡ ከሩቅ፡ ቁመው።
፲፫፡ እርሳቸውም፡ *ድምጻቸውን፡ አሰሙ፡ እንዴ
ህ፡ ሲሉ። የሱስ፡ ሆይ፡ መምህር፡ ማረን።
*መዝ፡ ፻፯፡ ፲፱፡፡
፲፬፡ አየም፡ አላቸውም። ሒዱ፡ ራሳችሁንም፡ ለ
ካህናት፡ አስፈትኑ። እርሳቸውም፡ ሲሔዱ፡ ነጹ።
ዘሌዋ፡ ፲፫፡ ፪፡ ፵፭፡ ፵፯፡፡ ፲፬፡ ፪፡፡
፲፭፡ ከርሳቸውም፡ አንዱ፡ እንደ፡ ተፈወሰ፡ ባየ፡ ጊ
ዜ፡ ተመለሰ፡ እግዚአብሔርን፡ በታላቅ፡ ቃል፡ ኢያመ
ሰገነ።
፲፮፡ በግምባሩም፡ ወደቀ፡ ወደግሩ፡ እርሱን፡ ኢያ
መሰገነ። እርሱም፡ ሰምራዊ፡ ነበር።
፲፯፡ የሱስም፡ መለሰ፡ አለም። አሥር፡ የነጹ፡ አይ
ደሉምን። ዘጠኙም፡የታሉ።
፲፰፡ አልተገኙም፡ ሊመለሱ፡ ለእግዚአብሔርም፡
ምስጋና፡ ሊሰጡ፡ ከዚህ፡ ከልዮ፡ ወገን፡ በቀር።
፲፱፡ አለውም፡ተነሣ፡ሒድም፡ *ሃይማኖትህ፡ አዳ
ነህ። *ም፡ ፯፡ ፶፡፡ ፰፡ ፵፰፡፡
፳፡ ፈሪሳውያንም፡ በጠየቁት፡ ጊዜ፡ የእግዚአብ
ሔር፡ መንግሥት፡ መቸ፡ ትመጣለች፡ ብለው። መለ
ሰላቸው፡አለም። በመጠባበቅ፡ አትመጣም፡ *የእግ
ዚአብሔር፡ መንግሥት። *ዮሐ፡ ፲፰፡ ፴፮፡፡
፩፡ቆሮ፡ ፬፡ ፳፡፡
፳፩፡ የሚሉም፡ የለም። እነሆ፡ እርስዋ፡ ከዚህ፡ ና
ት፡ ወይም፡ እነሆ፡ ከዚያ። እነሆ፡ የእግዚአብሔር፡
መንግሥት፡በውሥጣችሁ፡ናትና። *ማቴ፡ ፳፬፡ ፳፫፡፡
ማር፡ ፲፫፡ ፳፩፡፡
፳፪፡ ለደቀ፡ መዛሙርቱም፡አለ። የምትመጣ፡ ቀ
ን፡ አለች፡ የምትመኙባት፡ የሰው፡ልጅን፡ ቀን፡አንዲ
ቱን፡ ታዩ፡ ዘንድ፡ አታዩም።
፳፫፡እላንትንም፡ይልዋችኋል፡*እነሆ፡ከዚህ፡ነው፡
ወይም፡ ከዚያ። አትሒዱ፡ አትከተሉም።
*ም፡ ፳፩፡ ፰፡፡
፳፬፡ እንደ፡ *መብረቅም፡ ከሰማይ፡በታች፡ እንደ
ሚበርቅ፡እስከ፡ ሰማይ፡ ታችም፡እንደሚያበራ፡እን
ዴሁ፡ ይሆናል፡ ደግሞ፡ የሰው፡ ልጅ፡ በቀኑ።
ማቴ፡ ፳፬፡ ፳፯፡፡
፳፭፡ *አስቀድሞ፡ ግን፡ ይገባዋል፡ እጅግ፡ መከራ፡
ይቀበል፡ ዘንድ፡ ከዚህም፡ ትውልድ፡ ይናቅ፡ ዘንድ።
ማቴ፡ ፲፮፡ ፳፩፡፡
፳፮፡ በኖህ፡ ዘመንም፡እንደ፡ሆነ፡እንዴሁ፡ደግሞ፡
በሰው፡ ልጅ፡ ዘመን፡ ይሆናል።
፳፯፡ ይበሉ፡ ይጠጡም፡ ነበር፡ያገቡም፡ ይጋቡም።
*ኖህ፡ ወደ፡ መርከብ፡ እስከሚገባበት፡ ቀን፡ ድረስ።
የጥፋት፡ ውኃም፡ መጣ፡ ሁሉንም፡ አጠፋ።
*ዘፍ፡ ፯፡ ፯፡፡
፳፰፡ እንዴሁም፡ ደግሞ፡ ነበረ፡ በሎጥ፡ ዘመን።
ይበሉ፡ ይጠጡም፡ ነበር፡ ይገዙም፡ ይሸጡም፡ ይተክ
ሉም፡ ይሰሩም።
፳፱፡ ሎጥም፡ ከሮደም፡ በወጣበት፡ ከሰማይ፡ እ
ሳትና፡ዲን፡ *አዘነበ፡ ሁሉንም፡ አጠፋ።
*ዘፍ፡ ፲፱፡ ፲፭፡፡
፴፡ እንዴሁ፡ደግሞ፡ ይሆናል፡ የሰው፡ ልጅ፡ የሚገ
ለጥበት፡ ቀን።
፴፩፡ በዚያ፡ *ቀን፡ በሰገነት፡ ላይ፡ ያለ፡ እቃውም፡
በቤት፡ ሊወስደው፡አይውረድ። እንዴሁም፡ደግሞ፡
ወደ፡ ምድረ፡ በዳም፡ ያለ፡ ወደ፡ ኋላው፡አይመለስ።
ማቴ፡ ፳፬፡ ፲፯፡፡
፴፪፡ የሎጥን፡ ምሽት፡ አሰብዋት።
ዘፍ፡ ፲፱፡ ፳፮፡፡
፴፫፡ ነፍሱን፡ *ማደን፡ የወደደ፡ ይጥላታል። ነፍሱ
ንም፡ የጣለ፡ ያድናታል። *ም፡ ፱፡ ፳፬፡፡ ማቴ፡ ፲፡ ፴፱፡፡
፴፬፡ እላችኋለሁ። በዚያች፡ ሌሊት፡ ሁለቱ፡ ባን
ድ፡ አልጋ፡ ይተኛሉ። አንዱ፡ ይወሰዳል፡ ሁለተኛው
ም፡ ይቀራል። *ማቴ፡ ፳፬፡ ፵፡ ፵፩፡፡
፴፭፡ ሁለት፡ ሴቶች፡ ባንድ፡ ይፈጫሉ። አንዲቱ፡
ትሔዳለች፡ሁለተኛዪቱም፡ ትቀራለች።
፴፮፡ ሁለቱ፡ በሜዳ፡ይሆናሉ። አንዱ፡ ይወሰዳል፡
ሁለተኛውም፡ ይቀራል።
፴፯፡ መለሱም፡አሉትም። ወዴት፡ዘንድ፡አቤቱ።
እርሱ፡አላቸው። *ጥምብ፡ ወዳለበት፡ ስፍራ፡ከዚያ፡
ንሰሮች፡ ይሰበሰባሉ። *ኢዮብ፡ ፴፱፡ ፴፡፡
እንባ፡ ፩፡ ፰፡፡ ማቴ፡ ፳፬፡ ፳፰፡፡

## ምዕራፍ፡ ፲፰፡

፩፡ ደግሞም፡ ምሳሌ፡ አላቸው፡ *ሁለግዜ፡ እንዲ ጸልዩ፡ እንደይታክቱም። *ሮሜ፡ ፲፪፡ ፲፪። ቀል፡ ፬፡ ፪። ፩፡ ተሰ፡ ፭፡ ፲፯።

፪፡ እንዲህ፡ሲል። መኰንን፡ ነበረ፡ ባንዲት፡ አገር፡ እግዚአብሔርን፡ የማይፈራ፡ ሰውንም፡ የማያፍር።

፫፡ በዚያችም፡አገር፡ባልቴት፡ነበረች። ሁለግዜም፡ ትመጣበት፡ ነበረች፡ እንዲህ፡ ስትል። ፍረድልኝ፡ ከባ ለ፡ጋራዬ። ዘፀአ፡ ፳፪፡ ፳፪፡ ፳፫።

፬፡ እርሱም፡ እምቢ፡ አላት፡ አዘገያትም። ከዚያ ም፡ በኋላ፡ በልቡ፡ አለ። ምንም፡ እግዚአብሔርን፡ ባ ልፈራ፡ ሰውንም፡ ባላፍር።

፭፡ ይህች፡ ባልቴት፡ ግን፡ ስለ፡ ነዘነዘችኝ፡ እፈርድላ ታለሁ፡ እንዳታደክመኝ፡ ወደኔም፡ መጥታ፡ እንዳታ ውከኝ። ምዕ፡ ፲፩፡ ፯፡—፱።

፮፡ ጌታም፡አለ። ግፈኛ፡መኰንን፡ያለውን፡ስሙ።

፯፡ እግዚአብሔርን፡ እንኪያ፡ ለርሱ፡ ለተመረጹ ት፡ አይፈርድም፡ ወደርሱ፡ በቀንና፡ በሌት፡ የሚጮ ሁ። ይታገሣቸዋልምን። መዝ፡ ፹፫፡ ፪። ፺፬፡ ፱። ማቴ፡ ፳፬፡ ፳፪። ራእ፡ ፮፡ ፲።

፰፡ እላችኋለሁ፡ ፈጥኖ፡ እንዲፈርድላቸው። ነገር፡ ግን፡ የሰው፡ ልጅ፡ በመጣ፡ ጊዜ፡ እንጃ፡ ሃይማኖትን፡ ያገኛልን፡ በምድር፡ ላይ። ምዕ፡ ፲፯፡ ፳፪። ሮሜ፡ ፲፮፡ ፳።

፱፡ ይህነንም፡ምሳሌ፡ አለ፡ ስለ፡ ሰዎች፡ሰውነታቸ ውን፡ ያምኑት፡ የነበሩ፡ ጻድቃን፡ እንደ፡ ሆኑ፡ ሌሎች ንም፡ የሚንቁ። ምሳ፡ ፴፡ ፲፪።

፲፡ ሁለት፡ ሰዎች፡ ወደ፡ ቤተ፡ መቅደስ፡ ወጡ፡ ሊ ጸልዩ። አንዱ፡ ፈሪሳዊ፡ ሁለተኛውም፡ ቀራጭ። ማቴ፡ ፭፡ ፳፡ ፵፯።

፲፩፡ ፈሪሳዊ፡ ቁሞ፡ ይህነን፡ በልቡ፡ ይጸልይ፡ ነበር። *አቤቱ፡አመሰግንሃለሁ፡ እንደ፡ ሌሎች፡ ሰዎች፡ አይ ደለሁምና። ቀማኞች። ግፈኞች። አመንዝሮች። እን ደዚህም፡ ቀራጭ። *ኢሳ፡ ፶፰፡ ፪። ማቴ፡ ፭፡ ፳።

፲፪፡ በየሳምንቱ፡ ሁለት፡ ጊዜ፡ እጾማለሁ። ከብቴ ን፡ ሁሉ፤ አሥራት፡ አወጣለሁ።

፲፫፡ ቀራጩ፡ ግን፡ ከሩቅ፡ ቁሞ፡ ነበር፡ ወደ፡ ሰማይ ም፡ ዓይኑን፡ ስንኳ፡ ሊያነሣ፡ አይሻም፡ ነበር። ደረቱ ን፡ ይመታ፡ ነበር፡ እንጂ፡ እንዲህ፡ ሲል። አቤቱ፡ ይቀ ር፡ በለኝ፡ እኔን፡ ኃጢአተኛ። መዝ፡ ፶፩፡ ፫።

፲፬፡ እላችኋለሁ፡ይህ፡ወደ፡ቤቱ፡ እንደ፡ ሔደ፡ ነጽ ቶ፡ ከዚያ፡ ይልቅ። *ነፍሱን፡ ከፍ፡ ከፍ፡ ያደርግ፡ሁሉ፡ ይዋርዳልና። ነፍሱንም፡ ዝቅ፡ ዝቅ፡ ያደርግ፡ ከፍ፡ ይ ላል። ኢሳ፡ ፶፯፡ ፪። ማቴ፡ ፳፫፡ ፲፪። ፩፡ ጴጥ፡ ፭፡ ፭።

፲፭፡ ደግሞም፡ *ሕፃናትን፡ ወደርሱ፡ አመጡ፡ ይዳ ሳቸው፡ ዘንድ፡ ደቀ፡ መዛሙርትም፡ አይተው፡ ተቈ ጥዋቸው። *ኢሳ፡ ፵፱፡ ፳፪። ማቴ፡ ፲፱፡ ፲፫፡ ፲፬። ማር፡ ፲፡ ፲፫።

፲፮፡ የሱስ፡ግን፡ ጸራቸው፡ አለም። ተው፡ ሕፃናት፡ ወደኔ፡ ይምጡ፡ አትከልክልዋቸው። እንደለዚህ፡ ላ ሉት፡ ናትና፡ የእግዚአብሔር፡ መንግሥት።

፲፯፡ እውነት፡ እላችኋለሁ። የእግዚአብሔርን፡ መ ንግሥት፡ የማይቀበል፡ እንደ፡ ሕፃን፡ አይገባትም። ማር፡ ፲፡ ፲፭።

፲፰፡ ካለቆችም፡ አንዱ፡ ጠየቀው፡ እንዲህ፡ ሲል። ቸር፡ መምህር፡ ሆይ። ምን፡ ላድርግ፡ የዘላለም፡ ሕይ ወት፡ እወርስ፡ ዘንድ። ማቴ፡ ፲፱፡ ፲፮።

፲፱፡ የሱስም፡ አለው። ለምን፡ ቸር፡ ትለኛለህ። ቸ ር፡ የለም፡ ካንዱ፡ በቀር፡ እርሱም፡ እግዚአብሔር።

፳፡ ትእዛዛቱን፡ ታውቃለህ። *አታመንዝር። አት ግደል። አትስረቅ። ባሰት፡ አትመስክር። አባትህንና፡ እናትህን፡ አክብር። *ዘፀአ፡ ፳፡ ፲፪። ኤፌ፡ ፮፡ ፪።

፳፩፡ እርሱም፡ አለ። ይህነንስ፡ ሁሉ፡ ፈጽሜ፡ ጠበ ቅሁ፡ ከታናሽነቴ፡ጀምሬ።

፳፪፡ የሱስም፡ ይህነን፡ ነገር፡ በሰማ፡ ጊዜ፡ አለው። አንዲት፡ ደግሞ፡ ታጎድላለች። ከብትህን፡ ሁሉ፡ ሽጥ፡ ለ ድኆችም፡ ስጥ፡ በሰማይም፡ *መዝገብ፡ ይሆንልሃል። መጥተህም፡ ተከተለኝ። *ማቴ፡ ፮፡ ፳። ፩፡ ጢሞ፡ ፮፡ ፲፱።

፳፫፡ እርሱ፡ ግን፡ ይህነን፡ በሰማ፡ ጊዜ፡ እጅግ፡ አዘነ፡ እጅግ፡ ባለ፡ ጠጋ፡ ነበረና።

፳፬፡ የሱስም፡ አየ፡ እጅግ፡ እንደዘነ፡ አለም። እን ዴት፡ ይጨንቃል፡ ከብት፡ ላላቸው፡ ወደ፡ እግዚአብ ሔር፡ መንግሥት፡ መግባት።

፳፭፡ የግመል፡ መግባት፡ በመርፌ፡ ጆሮ፡ ይቀላልና፡ ባለ፤ ጠጋ፡ ወደ፡ እግዚአብሔር፡ መንግሥት፡ ኪገባ።

፳፮፡ የሰሙትም፡ አሉ፡ ማን፡ ይችላል፡ ይድን፡ ዘ ንድ።

፳፯፡ እርሱ፡ ግን፡ አለ። *በሰው፡ ዘንድ፡ የማይቻል፡ በ እግዚአብሔር፡ ዘንድ፡ የተቻለ፡ ነው። *ኢዮ፡ ፵፪፡ ፪።

፳፰፡ ጴጥሮስም፡ አለው። እነሆ፡ እኛ፡ ሁሉን፡ ትተ ን፡ ተከተልነህ። ምዕ፡ ፭፡ ፲፩።

፳፱፡ እርሱም፡ አላቸው። እውነት፡ እላችኋለሁ። ማንም፡ ቤትን፡ አልተወም፡ ወላጆችንም፡ ወንድሞ ችንም፡ ምሽትንም፡ ልጆችንም፡ ስለ፡ እግዚአብሔር፡ መንግሥት።

፴፡ ሁለት፡ እጽፍ፡ *አብዝቶ፡ በዚህ፡ ዘመን፡ ለው ጡን፡ ይቀበላል፡ እንጂ። በሚመጣውም፡ ዓለም፡ የዘላለም፡ ሕይወት። ማቴ፡ ፲፱፡ ፳፱። *ኢዮ፡ ፵፪፡ ፲፪።

፴፩፡ አሥራ፡ ሁለቱንም፡ ወሰዳቸው፡ አላቸውም። እነሆ፡ ወደ፡ የሩሳሌም፡ እንወጣለን፡ በነቢያትም፡ የ ተጻፈው፡ ሁሉ፡ በሰው፡ ልጅ፡ ላይ፡ ይፈጸማል። ማቴ፡ ፳፡ ፲፯፡—፲፱። ማር፡ ፲፡ ፴፪፡—፴፬።

፴፪፡ ለአሕዛብ፡ ይሰጣልና። ያፌዙበትማል። ይሰ ደቡማል። ይተፉበትማል። ኢሳ፡ ፶፫፡ ፯። መዝ፡ ፳፪፡ ፯።

፴፫፡ ይገርፉትማል፡ ይገሉትማል። በሶስተኛው
ም፡ ቀን፡ ይነሣል። ዮሐ፡ ፪፡ ፲፱።
፴፬፡ እርሳቸው፡ ግን፡ ምንምን፡ አላወቁም፡ ከዚ
ህ፡ ነገር፡ ይህም፡ ነገር፡ ከርሳቸው፡ ተሠውሮ፡ነበር፡ ያ
ለውንም፡ አያውቁም፡ ነበረ። ማር፡ ፱፡ ፴፪።
፴፭፡ ወደ፡ ዬሪኮም፡ በቀረበ፡ ጊዜ፡ እነሆ፡ ዕውር፡
ተቀምጦ፡ ነበረ፡ በመንገድ፡ ላይ፡ ሲለምን።
ማቴ፡ ፳፡ ፳፱፡—፴፬።
፴፮፡ ሕዝብም፡ ሲያልፍ፡ ሰማ፡ ጠየቀም፡ ይህ፡
ምንድር፡ ነው፡ ብሎ። ማር፡ ፲፡ ፵፮፡—፶፪።
፴፯፡ ነገሩትም፡የሱስ፡የናዝሬቱ፡እንደ፡ያልፍ።
፴፰፡ እርሱም፡ ጮኸ፡ እንደሁ፡ ሲል። የሱስ፡ የዳ
ዊት፡ ልጅ፡ ማረኝ።
፴፱፡ በፊትም፡የነበሩ፡ተቈጡት፡ዝም፡እንዲል።
እርሱ፡ ግን፡ ደግሞ፡ ጮኸት፡ አበዛ። የሱስ፡ ሆይ፡ የዳ
ዊት፡ ልጅ፡ ማረኝ።
፵፡ የሱስም፡ቆመ፡ወደርሱም፡ ያመጡት፡ዘንድ፡
አዘዘ። ወደርሱም፡ በቀረበ፡ጊዜ፡ ጠየቀው።
፵፩፡ እንደሁ፡ ሲል። ምን፡ ተሻለሽ፡ አደርግልህ፡ ዘ
ንድ። እርሱም፡ አለ። አቤቱ፡ አይ፡ ዘንድ።
፵፪፡ የሱስም፡አለው። እይ። *ሃይማኖትህ፡ አዳነ
ህ። ማቴ፡ ፱፡ ፳፪።
፵፫፡ የዚያን፡ጊዜውም፡አየ፡ እግዚአብሔርንም፡
ኢያመሰገነ፡ ተከተለው፡ ሕዝቡም፡ ሁሉ፡ አይተው፡
እግዚአብሔርን፡ አመሰገኑ። መዝ፡ ፻፵፯፡ ፳።

ምዕራፍ፡ ፲፱፡

፩፡ የሱስም፡ ወደ፡ ዬሪኮ፡ በገባ፡ ባለፈባትም፡ጊዜ።
፪፡ እነሆ፡ሰው፡ነበረ፡ ዘኬዎስ፡የሚሉት። ይህም፡
የቀራጮች፡ አለቃ፡ ነበረ። እርሱም፡ ባለጠጋ፡ ነበር።
፫፡ የሱስንም፡ *ሊያይ፡ ይሻ፡ ነበር፡ ማነው፡ እርሱ።
ከሰዎችም፡ ብዛት፡ የተነሣ፡ አይችልም፡ ነበር፡ ቁመ
ቱ፡ አጭር፡ ነበርና። *ዮሐ፡ ፲፪፡ ፳፩።
፬፡ ፈጥኖም፡ በፊት፡ሔደ፡ ወደ፡ ሾላም፡ ወጣ፡ ያየ
ው፡ ዘንድ፡ የሚያልፍባት፡ ነበርና።
፭፡ ወደዚያ፡ ስፍራ፡ በደረሰ፡ ጊዜ፡ የሱስ፡ ተመለ
ከተ፡ አየውም፡ አለውም። ዘኬዎስ፡ ሆይ፡ ፈጥነህ፡
ውረድ። ዛሬ፡ ይገባኛልና፡ በቤትህ፡ እውል፡ ዘንድ።
፮፡ ፈጥኖም፡ ወረደ፡ደስ፡ ብሎትም፡ ተቀበለው።
፯፡ ሁሉም፡ባዩ፡ ጊዜ፡ እንጕረጕሩ፡ እንደሁ፡ሲል።
ወደ፡ ኃጢአተኛ፡ ቤት፡ ገባ፡ ያርፍ፡ ዘንድ።
ም፡ ፲፭፡ ፪።
፰፡ ዘኬዎስም፡ ቆመ፡ጌታንም፡ አለው። እነሆ፡ የ
ኩብቴን፡ እኩሌታውን፡ ጌታ፡ ሆይ፡ ለድኆች፡ እሰጣ
ለሁ። ቀምቼ፡ እንደሆንሁ፡ *አራት፡ እጥፍ፡እከፍላ
ዋለሁ። *ዘፀአ፡ ፳፪፡ ፩፡ ፱። ፩፡ ሳሙ፡ ፲፪፡ ፫።
፱፡ የሱስም፡ አለው። ዛሬ፡ መድኃኒት፡ ሆነ፡ ለዚ
ህ፡ቤት። እርሱም፡ደግሞ፡*የአብርሃም፡ልጅ፡ነውና።
*ም፡ ፲፫፡ ፲፮። ገላት፡ ፫፡ ፯።
፲፡ የሰው፡ ልጅ፡ መጥትዋልና፡ የጠፋውን፡ ይሻ፡ ዘ
ንድ፡ያድነውም፡ ዘንድ። ሕዝ፡ ፴፬፡ ፲፮።
ማቴ፡ ፲፰፡ ፲፩። ፩፡ ጢሞ፡ ፩፡ ፲፭።
፲፩፡ እርሳቸውም፡ ይህነን፡ ሲሰሙ፡ ደግሞ፡ ጨመ
ረ፡ በምሳሌም፡ አላቸው። ወደ፡ የሩሳሌም፡ ቀርቦ፡
ነበርና፡ ይመስላቸውም፡ ነበር፡ የእግዚአብሔር፡መን
ግሥት፡ አሁን፡ ትገለጥ፡ ዘንድ፡ ጊዜ፡ እንደላት።
፲፪፡ አለም። ከበርቴ፡ *ሰው፡ ወደ፡ ሩቅ፡ አገር፡ ሔ
ደ፡ ለራሱ፡ መንግሥት፡ ወስዶ፡ ሊመለስ።
*ማቴ፡ ፳፭፡ ፲፬።
፲፫፡ አሥሩንም፡ ባሮቹን፡ ጸራቸው፡አሥር፡ ቀረጢ
ትም፡ ወርቅ፡ ሰጣቸው፡ አላቸውም። በዚህ፡ ሸጡ፡
ለውጡ፡ እስክመጣ፡ ድረስ።
፲፬፡ ያገሩ፡ *ሰዎች፡ግን፡ይጠሉት፡ነበሩ፡መለክተኛ
ችም፡ በኋላው፡ ላኩበት፡ እንደሁ፡ ሲሉ። ይህ፡ በላያ
ችን፡ ይነግሥብን፡ ዘንድ፡አንወድም። *ዮሐ፡ ፩፡ ፲፩።
፲፭፡ መንግሥትም፡ ወስዶ፡ በተመለሰ፡ ጊዜ፡ እሊ
ያን፡ ባሮች፡ ይጸሩለት፡ ዘንድ፡ አዘዘ፡ ወርቅ፡ የሰጣቸ
ውን፡ ያውቅ፡ ዘንድ፡ ምን፡ ያህል፡ ሸጠ፡ ለወጠ፡ ከር
ሳቸው፡ ኢያንዳንዱ።
፲፮፡ የፊተኛውም፡ መጣ፡ እንደሁ፡ ሲል። ጌታ፡ ሆ
ይ። ቀረጢትህ፡ አሥር፡ ቀረጢት፡ አተረፈ።
፲፯፡ አለውም። *መልካም፡ አደረግህ፡ አንተ፡ መ
ልካም፡ ባርያ። ተበጥቂት፡ የታመንህ፡ ሁነሃልና፡ ሥል
ጣን፡ ይሁንልህ፡ ባሥሩ፡ አገር፡ ላይ።
*ማቴ፡ ፳፭፡ ፳፩። †ሉቃ፡ ፲፮፡ ፲።
፲፰፡ ሁለተኛውም፡ መጣ፡ እንደሁ፡ ሲል። ጌታ፡ ሆ
ይ፡ ቀረጢትህ፡ አምስት፡ ቀረጢት፡ አደረገች።
፲፱፡ ይህነንም፡ ደግሞ፡ አለው። አንተም፡ ባምስ
ቱ፡ አገር፡ ላይ፡ ሁን።
፳፡ ሶስተኛውም፡ መጣ፡ እንደሁ፡ ሲለው። ጌታ፡
ሆይ፡ እነሆ፡ ወርቅህ፡ ከኔ፡ ዘንድ፡ የነበረች፡ በጭርቅ፡
ተጠቅልላ።
፳፩፡ ካንተ፡ ፈርቻለሁና፡ ጽኑ፡ ሰው፡ ስለ፡ ሆንህ።
ያላኖርኸውን፡ትወስዳለህ። ያልዘራኸውንም፡ታጭ
ዳለህ።
፳፪፡ አለውም። *ካፍህ፡ የተነሣ፡ እፈርድብሃለ
ሁ፡ አንተ፡ ክፉ፡ ባርያ። አወቅህ፡ እኔ፡ ጽኑ፡ ሰው፡
እንደ፡ ሆንሁ። ያላኖርሁትን፡ እወስዳለሁ፡ ያልዘራሁ
ትንም፡ አጭዳለሁ። *፪፡ ሳሙ፡ ፩፡ ፲፮።
ማቴ፡ ፲፪፡ ፴፯።
፳፫፡ ምነው፡ ወርቄን፡ ወደ፡ ለዋጮች፡ አላኖርህ፡
እኔም፡ መጥቼ፡ ከትርፉ፡ ጋራ፡ እወስደው፡ ነበርሁ።
፳፬፡ የቆሙቱንም፡ ሰዎች፡ አላቸው። ያነን፡ ቀረ
ጢት. ንሡት፡ አሥር፡ ቀረጢት፡ ላለውም፡ ስጡት።
፳፭፡ አሉትም፡ አቤቱ፡ አሥር፡ ቀረጢት፡ አለው።
፳፮፡ እላችኋለሁና። ያለው፡ ሁሉ፡ ይሰጠዋል። የ
ሌለው፡ ግን፡ ያለውም፡ ይወስደበታል።
*ም፡ ፰፡ ፲፰። ማቴ፡ ፲፫፡ ፲፪።

## ምዕራፍ፡ ፲፰፡

፩፡ ደግሞም፡ ምሳሌ፡ አላቸው፡ *ሁልጊዜ፡ እንዲ
ጸልዩ፡ እንደይታክቱም። *ሮሜ፡ ፲፪፡ ፲፪።
ቆል፡ ፬፡ ፪። ፩፡ ተሰ፡ ፭፡ ፲፯።
፪፡ እንዲህ፡ሲል። መኰንን፡ነበረ፡ ባንዲት፡ አገር፡
እግዚአብሔርን፡ የማይፈራ፡ ሰውንም፡ የማያፍር።
፫፡ በዚያቺም፡አገር፡ባልቴት፡ነበረች። ሁልጊዜም፡
ትመጣበት፡ ነበረች፡ እንዲህ፡ ስትል። ፍረድልኝ፡ ከባ
ለ፡ጋራዬ። ዘፀአ፡ ፳፪፡ ፳፪፡ ፳፫።
፬፡ እርሱም፡ እምቢ፡ አላት፡ አዘገያትም። ከዚያ
ም፡ በኋላ፡ በልቡ፡ አለ። ምንም፡ እግዚአብሔርን፡ ባ
ልፈራ፡ ሰውንም፡ ባላፍር።
፭፡ ይህች፡ ባልቴት፡ ግን፡ ስለ፡ ነዘነዘችኝ፡ እፈርድላ
ታለሁ፡ እንዳታደክመኝ፡ ወደኔም፡ መጥታ፡ እንዳታ
ውከኝ። ም፡ ፲፩፡ ፯—፱።
፮፡ ጌታም፡አለ። ግፈኛ፡መኰንን፡ያለውን፡ስሙ።
፯፡ እግዚአብሔርን፡ እንኪያ፡ ለርሱ፡ ለተመረጹ
ት፡ አይፈርድም፡ ወደርሱ፡ በቀንና፡ በሌት፡ የሚጮ
ሁ። ይታገሣቸዋልምን። መዝ፡ ፹፫፡ ፪።
፺፬፡ ፱። ማቴ፡ ፳፬፡ ፳፪። ራእ፡ ፮፡ ፲።
፰፡ እላችኋለሁ፡ ፈጥኖ፡ እንዲፈርድላቸው። ነገር፡
ግን፡ የሰው፡ ልጅ፡ በመጣ፡ ጊዜ፡ እንጃ፡ ሃይማኖትን፡
ያገኛልን፡ በምድር፡ ላይ። ም፡ ፲፯፡ ፳፪።
ሮሜ፡ ፲፮፡ ፳።
፱፡ ይህነንም፡ምሳሌ፡ አለ፡ ስለ፡ ሰዎች፡ሰውነታቸ
ውን፡ ያምኑት፡ የነበሩ፡ ጻድቃን፡ እንደ፡ ሆኑ፡ ሌሎች
ንም፡ የሚንቁ። ምሳ፡ ፴፡ ፲፪።
፲፡ ሁለት፡ ሰዎች፡ ወደ፡ ቤተ፡ መቅደስ፡ ወጡ፡ ሊ
ጸልዩ። አንዱ፡ ፈሪሳዊ፡ ሁለተኛውም፡ ቀራጭ።
ማቴ፡ ፭፡ ፳፡ ፵፮።
፲፩፡ ፈሪሳዊ፡ ቁሞ፡ ይህነን፡ በልቡ፡ ይጸልይ፡ ነበር።
*አቤቱ፡አመሰግንሃለሁ፡ እንደ፡ ሌሎች፡ ሰዎች፡ አይ
ደለሁምና። ቀማኞች። ግፈኞች። አመንዝሮች። እን
ደዚህም፡ ቀራጭ። *ኢሳ፡ ፶፰፡ ፪። ማቴ፡ ፭፡ ፳።
፲፪፡ በየሳምንቱ፡ ሁለት፡ ጊዜ፡ እጾማለሁ። ከብቴ
ን፡ ሁሉ፤ አሥራት፡ አወጣለሁ።
፲፫፡ ቀራጩ፡ ግን፡ ከሩቅ፡ ቁሞ፡ ነበር፡ ወደ፡ ሰማይ
ም፡ ዓይኑን፡ ሰንኳ፡ ሊያነሣ፡ አይሻም፡ ነበር። ደረቱ
ን፡ ይመታ፡ ነበር፡ እንጂ፡ እንዲህ፡ ሲል። አቤቱ፡ ይቀ
ር፡ በለኝ፡ እኔን፡ ኃጢአተኛ። መዝ፡ ፶፩፡ ፫።
፲፬፡ እላችኋለሁ፡ይህ፡ወደ፡ቤቱ፡ እንደ፡ ሔደ፡ ነጽ
ቶ፡ ከዚያ፡ ይልቅ። *ነፍሱን፡ ከፍ፡ ከፍ፡ ያደረገ፡ሁሉ፡
ይዋረዳልና። ነፍሱንም፡ ዝቅ፡ ዝቅ፡ ያደረገ፡ ከፍ፡ ይ
ላል። ኢሳ፡ ፷፮፡ ፪። ማቴ፡ ፳፫፡ ፲፪። ፩፡ ጴጥ፡ ፭፡ ፭።
፲፭፡ ደግሞም፡ *ሕፃናትን፡ ወደርሱ፡ አመጡ፡ይዳ
ሳቸው፡ ዘንድ፡ ደቀ፡ መዛሙርትም፡ አይተው፡ ተቈ
ጥዋቸው። *ኢሳ፡ ፵፱፡ ፳፪። ማቴ፡ ፲፱፡ ፲፫፡ ፲፬።
ማር፡ ፲፡ ፲፫።

፲፮፡ የሱስ፡ግን፡ ጸራቸው፡ አለም። ተው፡ሕፃናት፡
ወደኔ፡ይምጡ፡ አትከልክልዋቸው። እንደለዚህ፡ ላ
ሉት፡ ናትና፡ የእግዚአብሔር፡ መንግሥት።
፲፯፡ እውነት፡እላችኋለሁ። የእግዚአብሔርን፡መ
ንግሥት፡ የማይቀበል፡ እንደ፡ ሕፃን፡ አይገባባትም።
ማር፡ ፲፡ ፲፭።
፲፰፡ ካለቆችም፡ አንዱ፡ጠየቀው፡ እንዲህ፡ ሲል።
ቸር፡ መምህር፡ ሆይ። ምን፡ ላድርግ፡ የዘላለም፡ ሕይ
ወት፡ አወርስ፡ዘንድ። ማቴ፡ ፲፱፡ ፲፮።
፲፱፡ የሱስም፡ አለው። ለምን፡ቸር፡ ትለኛለህ። ቸ
ር፡ የለም፡ ካንዱ፡ በቀር፡ እርሱም፡ እግዚአብሔር።
፳፡ ትእዛዛቱን፡ ታውቃለህ። *አታመንዝር። አት
ግደል። አትስረቅ። ባሰት፡ አትመስክር። አባትህንና፡
እናትህን፡አክብር። *ዘፀአ፡ ፳፡ ፲፪። ኤፌ፡ ፮፡ ፪።
፳፩፡ እርሱም፡አለ። ይህነንስ፡ ሁሉ፡ ፈጽሜ፡ ጠበ
ቅሁ፡ ከታናሽነቴ፡ ጀምሬ።
፳፪፡ የሱስም፡ ይህነን፡ ነገር፡ በሰማ፡ጊዜ፡ አለው።
አንዲት፡ ደግሞ፡ታሻሃለች። ከብትህን፡ሁሉ፡ ሽጥ፡ ለ
ድኆችም፡ስጥ፡ በሰማይም፡ *መዝገብ፡ ይሆንልሃል።
መጥተህም፡ ተከተለኝ። *ማቴ፡ ፮፡ ፳።
፩፡ ጢሞ፡ ፮፡ ፲፱።
፳፫፡ እርሱ፡ ግን፡ይህነን፡ በሰማ፡ ጊዜ፡አጅግ፡አዘነ፡
እጅግ፡ ባለ፡ ጠጋ፡ ነበረና።
፳፬፡ የሱስም፡ አየ፡ እጅግ፡ እንደዘነ፡ አለም። እን
ዴት፡ ይጨንቃል፡ ከብት፡ ላላቸው፡ ወደ፡ እግዚአብ
ሔር፡ መንግሥት፡ መግባት።
፳፭፡ የግመል፡ መግባት፡ በመርፌ፡ ጆር፡ ይቀላልና፡
ባለ፤ ጠጋ፡ ወደ፡ እግዚአብሔር፡ መንግሥት፡ ኪገባ።
፳፮፡ የሰሙትም፡ አሉ፡ ማን፡ ይችላል፡ ይድን፡ ዘ
ንድ።
፳፯፡ እርሱ፡ግን፡አለ።*በሰው፡ዘንድ፡የማይቻል፡በ
እግዚአብሔር፡ዘንድ፡የተቻለ፡ነው። *ኢዮ፡ ፵፪፡ ፪።
፳፰፡ ጴጥሮስም፡ አለው። እነሆ፡እኛ፡ ሁሉን፡ትተ
ን፡ ተከተልነህ። ም፡ ፭፡ ፲፩።
፳፱፡ እርሱም፡ አላቸው። እውነት፡ እላችኋለሁ።
ማንም፡ ቤትን፡ አልተወም፡ ወላጆችንም፡ ወንድሞ
ችንም፡ ምሽትንም፡ ልጆችንም፡ስለ፡እግዚአብሔር፡
መንግሥት።
፴፡ ሁለት፡ እጽፍ፡ *አብዝቶ፡በዚህ፡ ዘመን፡ ለው
ጡን፡ ይቀበላል፡ እንጂ። በሚመጣውም፡ ዓለም፡
የዘላለም፡ ሕይወት። ማቴ፡ ፲፱፡ ፳፱።
*ኢዮ፡ ፵፪፡ ፲፪።
፴፩፡ አሥራ፡ሁለቱንም፡ወሰደቸው፡አላቸውም።
እነሆ፡ ወደ፡ የሩሳሌም፡ እንወጣለን፡ በነቢያትም፡ የ
ተጻፈው፡ ሁሉ፡ በሰው፡ ልጅ፡ ላይ፡ ይፈጸማል።
ማቴ፡ ፳፡ ፲፯—፲፱። ማር፡ ፲፡ ፴፪—፴፬።
፴፪፡ ለአሕዛብ፡ይሰጣልና። ያፌዙበትማል። ይሰ
ደብማል። ይተፋበትማል። ኢሳ፡ ፶፫፡ ፯።
መዝ፡ ፳፪፡ ፯።

፴፫፡ ይገርፉትማል፡ ይገሉትማል። በሶስተኛውም፡ ቀን፡ ይነሣል። ዮሐ፡ ፪፡ ፲፱።
፴፬፡ እርሳቸው፡ ግን፡ ምንምን፡ አላወቁም፡ ከዚህ፡ ነገር፡ ይህም፡ ነገር፡ ከርሳቸው፡ ተሠውሮ፡ነበር፡ ያለውንም፡ አያውቁም፡ ነበሩ። ማር፡ ፱፡ ፴፪።
፴፭፡ ወደ፡ ዔሪኮም፡ በቀረበ፡ ጊዜ፡ እነሆ፡ ዕውር፡ ተቀምጦ፡ ነበረ፡ በመንገድ፡ ላይ፡ ሲለምን።
ማቴ፡ ፳፡ ፳፱፡—፴፬።
፴፮፡ ሕዝብም፡ ሲያልፍ፡ ሰማ፡ ጠየቀም፡ ይህ፡ ምንድር፡ነው፡ ብሎ። ማር፡ ፲፡ ፵፮፡—፶፪።
፴፯፡ ነገሩትም፡የሱስ፡የናዝሬቱ፡እንዲያልፍ።
፴፰፡ እርሱም፡ ጮኸ፡ እንዲህ፡ ሲል። የሱስ፡ የዳዊት፡ ልጅ፡ ማረኝ።
፴፱፡ በፊትም፡የነበሩ፡ተቈጡት፡ዝም፡እንዲል። እርሱ፡ግን፡ ደግሞ፡ ጮኸት፡ አበዛ። የሱስ፡ ሆይ፡ የዳዊት፡ ልጅ፡ ማረኝ።
፵፡ የሱስም፡ቆመ፡ወደርሱም፡ ያመጡት፡ዘንድ፡ አዘዘ። ወደርሱም፡ በቀረበ፡ጊዜ፡ ጠየቀው።
፵፩፡ እንዲህ፡ ሲል። ምን፡ ተሻለህ፡ አደርግልህ፡ ዘንድ። እርሱም፡ አለ። አቤቱ፡ አይ፡ ዘንድ።
፵፪፡ የሱስም፡አለው። እይ። *ሃይማኖትህ፡ አዳነህ። ማቴ፡ ፱፡ ፳፪።
፵፫፡ የዚያን፡ጊዜውም፡አየ፡ እግዚአብሔርንም፡ ኢያመሰገነ፡ ተከተለው፡ ሕዝቡም፡ ሁሉ፡ አይተው፡ እግዚአብሔርን፡ አመሰገኑ። መዝ፡ ፻፵፮፡ ፳።

ምዕራፍ፡ ፲፱፡

፩፡ የሱስም፡ ወደ፡ ዔሪኮ፡ በገባ፡ ባለፈባትም፡ጊዜ።
፪፡ እነሆ፡ሰው፡ ነበረ፡ ዘኬዎስ፡የሚሉት። ይህም፡ የቀራጮች፡ አለቃ፡ነበረ። እርሱም፡ ባለጠጋ፡ነበር።
፫፡ የሱስንም፡ *ሊያይ፡ ይሻ፡ ነበር፡ ማነው፡ እርሱ። ከሰዎችም፡ ብዛት፡ የተነሣ፡ አይችልም፡ ነበር፡ ቁመቱ፡ አጭር፡ ነበርና። *ዮሐ፡ ፲፪፡ ፳፩።
፬፡ ፈጥኖም፡ በፊት፡ሔደ፡ ወደ፡ ሾላም፡ ወጣ፡ ያየው፡ ዘንድ፡ የሚያልፍባት፡ ነበርና።
፭፡ ወደዚያ፡ ስፍራ፡ በደረሰ፡ ጊዜ፡ የሱስ፡ ተመለከተ፡ አየውም፡ አለውም። ዘኬዎስ፡ ሆይ፡ ፈጥነህ፡ ውረድ። ዛሬ፡ ይገባኛልና፡ በቤትህ፡ እውል፡ ዘንድ።
፮፡ ፈጥኖም፡ ወረደ፡ ደስ፡ ብሎትም፡ ተቀበለው።
፯፡ ሁሉም፡ባዩ፡ ጊዜ፡ አንጐረጐሩ፡ እንዲህ፡ሲል። ወደ፡ ኃጢአተኛ፡ ቤት፡ ገባ፡ ያርፍ፡ ዘንድ።
ም፡ ፲፭፡ ፪።
፰፡ ዘኬዎስም፡ ቆመ፡ጌታንም፡ አለው። እነሆ፡ የከብቴን፡ እኩሌታውን፡ ጌታ፡ ሆይ፡ ለድኆች፡ እሰጣለሁ። ቀምቼ፡ እንደሆንሁ፡ *አራት፡ እጥፍ፡እከፍላለሁ። *ዘፀአ፡ ፳፪፡ ፩፡ ፱። ፩፡ ሳሙ፡ ፲፪፡ ፫።
፱፡ የሱስም፡ አለው። ዛሬ፡ መድኃኒት፡ ሆነ፡ ለዚህ፡ቤት። እርሱም፡ደግሞ፡*የአብርሃም፡ልጅ፡ነውና።
*ም፡ ፲፫፡ ፲፮። ገላት፡ ፫፡ ፯።
፲፡ የሰው፡ ልጅ፡ መጥትዋልና፡ የጠፋውን፡ ይሻ፡ ዘንድ፡ያድነውም፡ ዘንድ። ሕዝ፡ ፴፬፡ ፲፮።
ማቴ፡ ፲፰፡ ፲፩። ፩፡ ጢሞ፡ ፩፡ ፲፭።
፲፩፡ እርሳቸውም፡ ይህነን፡ ሲሰሙ፡ ደግሞ፡ ጨመረ፡ በምሳሌም፡ አላቸው። ወደ፡ የሩሳሌም፡ ቀርቦ፡ ነበርና፡ ይመስላቸውም፡ ነበር፡ የእግዚአብሔር፡መንግሥት፡አሁን፡ ትገለጥ፡ ዘንድ፡ ጊዜ፡ እንደላት።
፲፪፡ አለም። ከበርቴ፡ *ሰው፡ ወደ፡ ሩቅ፡ አገር፡ ሔደ፡ ለራሱ፡ መንግሥት፡ ወስዶ፡ ሊመለስ።
*ማቴ፡ ፳፭፡ ፲፬።
፲፫፡ አሥሩንም፡ ባሮቹን፡ ጸራቸው፡አሥር፡ ቀረጢትም፡ ወርቅ፡ ሰጣቸው፡ አላቸውም። በዚህ፡ ሸጡ፡ ለውጡ፡ እስክመጣ፡ ድረስ።
፲፬፡ ያገሩ፡ *ሰዎች፡ግን፡ይጠሉት፡ነበሩ፡መለክተኞችም፡ በኋላው፡ ላኩበት፡ እንዲህ፡ ሲሉ። ይህ፡ በላያችን፡ ይነግሥብን፡ ዘንድ፡አንወድም። *ዮሐ፡ ፩፡ ፲፩።
፲፭፡ መንግሥትም፡ ወስዶ፡ በተመለሰ፡ ጊዜ፡ እሊያን፡ ባሮች፡ ይጸሩለት፡ ዘንድ፡ አዘዘ፡ ወርቅ፡ የሰጣቸውን፡ ያውቅ፡ ዘንድ፡ ምን፡ ያህል፡ ሸጠ፡ ለወጠ፡ ከርሳቸው፡ ኢያንዳንዱ።
፲፮፡ የፊተኛውም፡ መጣ፡ እንዲህ፡ ሲል። ጌታ፡ ሆይ። ቀረጢትህ፡ አሥር፡ ቀረጢት፡ አተረፈ።
፲፯፡ አለውም። *መልካም፡ አደረግህ፡ አንተ፡ መልካም፡ ባርያ። ተበጥቂት፡ የታመንህ፡ ሁነሃልና፡ ሥልጣን፡ ይሁንልህ፡ ባሥሩ፡ አገር፡ ላይ።
*ማቴ፡ ፳፭፡ ፳፩። †ሉቃ፡ ፲፮፡ ፲።
፲፰፡ ሁለተኛውም፡ መጣ፡እንዲህ፡ ሲል። ጌታ፡ ሆይ፡ ቀረጢትህ፡ አምስት፡ ቀረጢት፡ አደረገች።
፲፱፡ ይህነንም፡ ደግሞ፡ አለው። አንተም፡ ባምስቱ፡ አገር፡ ላይ፡ ሁን።
፳፡ ሶስተኛውም፡ መጣ፡ እንዲህ፡ ሲለው። ጌታ፡ ሆይ፡ እነሆ፡ ወርቅህ፡ ከኔ፡ ዘንድ፡ የነበረች፡ በጭርቅ፡ ተጠቅልላ።
፳፩፡ ካንተ፡ ፈርቻለሁና፡ጽኑ፡ ሰው፡ ስለ፡ ሆንህ። ያላኖርኸውን፡ትወስዳለህ።ያልዘራኸውንም፡ታጭዳለህ።
፳፪፡ አለውም። *ካፍህ፡ የተነሣ፡ እፈርድብሃለሁ፡ አንተ፡ ክፉ፡ ባርያ። አወቅህ፡ እኔ፡ ጽኑ፡ ሰው፡ እንደ፡ ሆንሁ። ያላኖርሁትን፡እወስዳለሁ፡ያልዘራሁትንም፡ አጭዳለሁ። *፪፡ ሳሙ፡ ፩፡ ፲፮።
ማቴ፡ ፲፪፡ ፴፯።
፳፫፡ ምነው፡ ወርቄን፡ ወደ፡ ለዋጮች፡ አላኖርህ፡ እኔም፡ መጥቼ፡ ከትርፉ፡ ጋራ፡ እወስደው፡ ነበርሁ።
፳፬፡ የቆሙቱንም፡ ሰዎች፡ አላቸው። ያነን፡ ቀረጢት. ንሡት፡ አሥር፡ ቀረጢት፡ ላለውም፡ ስጡት።
፳፭፡ አሉትም፡አቤቱ፡ አሥር፡ ቀረጢት፡ አለው።
፳፮፡ እላችኋለሁና። ያለው፡ ሁሉ፡ ይሰጠዋል። የሌለው፡ ግን፡ ያለውም፡ ይወሰድበታል።
*ም፡ ፰፡ ፲፰። ማቴ፡ ፲፫፡ ፲፪።

፳፯፡ እሊያን፡ ጸላቶቼን፡ ግን፡ እነግሥባቸው፡ ዘንድ፡ ያልወደዱትን፡ ወደዚህ፡ አምጡልኝ፡ በፊቴም፡ እረድዋቸው።

፳፰፡ ይህነንም፡ ባለ፡ ጊዜ፡ በፊታቸው፡ ሒደ፡ ወደ፡ *የሩሳሌም፡ ወጣ። *ማር፡ ፲፡ ፴፪።

፳፱፡ ወደ፡ ቤትፋጌም፡ በቀረበ፡ ጊዜ፡ ወደ፡ ቢታንያም፡ ደብረ፡ ዘይት፡ ወደሚባል፡ ተራራ። ሁለት፡ ከደቀ፡ መዛሙርቱ፡ ላከ። ማቴ፡ ፳፩፡ ፩—፱። ዮሐ፡ ፲፪፡ ፲፪—፲፮።

፴፡ እንዲህ፡ ሲል። በፊታችሁ፡ ወደላችው፡ አገር፡ ሒዱ። ወደርስዋም፡ በገባችሁ፡ ጊዜ፡ ያህያ፡ ግልገል፡ የታሠረ፡ ታገኛላችሁ፡ ከሰው፡ ማንም፡ ከቶ፡ ያልተቀመጠበት። ፈታችሁ፡ አምጡት። ማር፡ ፲፩፡ ፪።

፴፩፡ ማንም፡ ቢጠይቃችሁ፡ ለምን፡ ትፈቱታላችሁ፡ ብሎ። እንዲህ፡ በሉት። ጌታ፡ ይሻዋል።

፴፪፡ የተላኩትም፡ በሔዱ፡ ጊዜ፡ አገኙ፡ እንደላቸው።

፴፫፡ እርሳቸውም፡ ግልገሉን፡ ሲፈቱ፡ ጌቶቹ፡ አልዋቸው፡ ግልገሉን፡ ለምን፡ ትፈታላችሁ።

፴፬፡ እርሳቸውም፡ አልዋቸው። ጌታ፡ ይሻዋል። ዮሐ፡ ፲፪፡ ፲፬።

፴፭፡ ወደ፡ የሱስም፡ ይዘውት፡ መጡ፡ በግልገሉም፡ ላይ፡ ልበሳቸውን፡ ጫኑ፡ የሱስንም፡ በርሱ፡ አስቀመጡት።

፴፮፡ እርሱም፡ ሲሔድ፡ ልብሳቸውን፡ በመንገድ፡ አነጸፉ።

፴፯፡ በቀረበም፡ ጊዜ፡ ከደብረ፡ ዘይት፡ በሚያወርደው፡ መንገድ፡ የደቀ፡ መዛሙርቱ፡ ምላ፡ ሁሉ፡ ደስ፡ ይላቸው፡ እግዚአብሔርንም፡ በታላቅ፡ ቃል፡ ያመሰግኑት፡ ጀመሩ፡ ስላዩት፡ ኀይል፡ ሁሉ።

፴፰፡ ኢያሉ፡ የተባረከ፡ ንጉሥ፡ ነው፡ በእግዚአብሔር፡ ስም፡ የሚመጣ። *ሰላም፡ በሰማይ፡ ምስጋናም፡ በአርያም። *ም፡ ፪፡ ፲፬።

፴፱፡ ከፈሪሳውያንም፡ ሰዎች፡ በሕዝቡ፡ መካከል፡ አሉት። መምህር፡ ሆይ፡ ደቀ፡ መዛሙርትህን፡ ተቈጣ።

፵፡ መለሰም፡ አላቸውም። እላችኋለሁ፡ እሌህ፡ ዝም፡ ቢሉ፡ ደንጎች፡ እንዲጮሁ። አንባ፡ ፪፡ ፲፩። ፪፡ ጴጥ፡ ፪፡ ፲፮።

፵፩፡ በቀረበም፡ ጊዜ፡ አገሪቱንም፡ ባየ፡ ጊዜ፡ *አለቀሰላት። *፪፡ ነገሥ፡ ፳፡ ፲፩። ዮሐ፡ ፲፩፡ ፴፮።

፵፪፡ እንዲህ፡ ሲል። ብታውቂስ፡ አንቺ፡ በዚህ፡ በቀንሽ፡ ለሰላምሽ፡ የሚሆነውን፡ ነገር። ዛሬ፡ ግን፡ ካይንሽ፡ ተሠውርዋል። ዘዳግ፡ ፴፪፡ ፳፱። ኢሳ፡ ፶፱፡ ፳።

፵፫፡ ጸላቶችሽ፡ ቅጥር፡ ቀጥረው፡ የሚዞሩሽ፡ ቀን፡ ይመጣብሻልና፡፡ ይከቡሻልም፡ በዚህና፡ በዚያም፡ ያስጨንቁሻል። ኢሳ፡ ፳፱፡ ፫። ሕዝ፡ ፳፩፡ ፳፪።

፵፬፡ ይገለብጡሻልም፡ ልጆችሽንም፡ ባንድ፡ ካንቺ፡ ጋራ። ደንጊያም፡ በደንጊያ፡ ላይ፡ አይተውልሽም። የምሕረትሽን፡ ዘመን፡ አላወቅሽምና። ማቴ፡ ፳፬፡ ፪። ሚካ፡ ፫።

፵፭፡ ወደ፡ መቅደስም፡ በገባ፡ ጊዜ፡ የሚሸጡትን፡ የሚገዙትንም፡ ያወጣ፡ ጀመረ። ማቴ፡ ፳፩፡ ፲፪—፲፮። ማር፡ ፲፩፡ ፲፭—፲፰። ዮሐ፡ ፪፡ ፲፫—፲፮።

፵፮፡ እንዲህ፡ ሲላቸው። ቤቴ፡ የጸሎት፡ ቤት፡ ነው፡ ብሎ፡ ተጽፏዋል። *እላንት፡ ግን፡ የሌቦች፡ ዋሻ፡ አደረጋችሁት። *ኢሳ፡ ፶፮፡ ፯። ኤር፡ ፯፡ ፲፩።

፵፯፡ ሁለግዜም፡ በመቅደስ፡ ያስተምር፡ ነበር። የካህናት፡ አለቆች፡ ግን፡ የሕዝቡም፡ ታላላቆች፡ ይገድሉት፡ ዘንድ፡ ይሹ፡ ነበሩ።

፵፰፡ የሚያደርጉትንም፡ አላገኙም። ሕዝቡ፡ ሁሉ፡ ተንጠልጥሎበት፡ ነበርና፡ ከርሱ፡ ሊሰማ።

ምዕራፍ፡ ፳፡

፩፡ በዚያችም፡ ባንዲቱ፡ ቀን፡ እርሱ፡ ሕዝቡን፡ ሲያስተምር፡ በመቅደስ፡ የምስራችም፡ ሲነግር፡ ተነሡበት፡ የካህናት፡ አለቆች፡ ጻፎችም፡ ከሽማግሎች፡ ጋራ። ማቴ፡ ፳፩፡ ፳፫—፳፯። ማር፡ ፲፩፡ ፳፯—፴፫።

፪፡ ጠየቁትም፡ እንዲህ፡ ሲሉ። ንገረነ፡ በምን፡ ትእዛዝ፡ ይህነን፡ ታደርጋለህ። ወይስ፡ ማነው፡ ይህነን፡ ትእዛዝ፡ የሰጠህ።

፫፡ መለሰም፡ አላቸውም። እኔም፡ እጠይቃችኋለሁ፡ አንዲት፡ ነገር። እላንትም፡ ንገሩኝ።

፬፡ የዮሐንስ፡ ጥምቀት፡ ከሰማይን፡ ነበረች፡ ወይስ፡ ከሰው።

፭፡ እርሳቸው፡ ግን፡ በልባቸው፡ ያስቡ፡ ነበር፡ እንዲህ፡ ሲሉ። ከሰማይ፡ ብንልም፡ ይለናል። ምነው፡ አላመናችሁበት።

፮፡ ከሰውም፡ ብንል፡ ሕዝብ፡ ሁሉ፡ ይወግረናል። አምነዋልና፡ ዮሐንስ፡ ነቢይ፡ እንደ፡ ሆነ።

፯፡ መለሱም፡ እንደያውቁ፡ ከወዴት፡ እንደ፡ ሆነች።

፰፡ የሱስም፡ አላቸው። እኔም፡ አልነግራችሁም፡ በምን፡ ትእዛዝ፡ ይህነን፡ እንደደርግ።

፱፡ ይህነን፡ ምሳሌ፡ ለሕዝቡ፡ ይልው፡ ጀመረ። ሰው፡ የወይን፡ ስፍራ፡ ተከለ፡ ለጠባቆችም፡ ሰጠው፡ መንገድም፡ ሔደ፡ ብዙ፡ ዘመን። ማቴ፡ ፳፩፡ ፴፫—፵፮። ማር፡ ፲፪፡ ፩—፲፪። መዝ፡ ፹፡ ፱። ኢሳ፡ ፭፡ ፩።

፲፡ በጊዜውም፡ ባርያውን፡ ወደ፡ ጠባቆች፡ *ላከ፡ ከወይኑ፡ ፍሬ፡ ሊወስድ። ጠባቆች፡ ግን፡ መቱት፡ እንዲያውም፡ ሰደዱት። *፪፡ ዜና፡ ፴፮፡ ፲፭፡ ፲፮።

፲፩፡ ደግሞም፡ ሌላውን፡ ባርያ፡ ሰደደ። እርሳቸው፡ ግን፡ እርሱን፡ ደግሞ፡ መቱት፡ ናቁትም፡ ባዶውንም፡ ሰደዱት።

፲፪፤ ደግሞም፡ ሦስተኛውን፡ሰደደ። እርሳቸው፡ ግ
ን፡ ደህነን፡ ደግሞ፡ አቍሰሉት፡ ሜደም፡ አወጡት።
፲፫፤ የወይኑ፡ ጌታም፡ አለ። ምን፡ ልሰራ፡ የምወደ
ውን፡ ልጄን፡ ልስደድ። ምን፡ አልባት፡እርሱን፡ ቢያዩ
ት፡ ያፈሩት፡ እንደሆን። ዮሐ፡ ፫፤ ፲፯።
፲፬፤ ጠባቆችም፡ ባዩት፡ ጊዜ፡በልባቸው፡ አሰቡ፡ እ
ንዲህ፡ ሲሉ። ይሀ፡ ነው፡ የሚወርሰው። ኑ፡ እንግደለ
ው፡ ርስቱ፡ ለኛ፡ እንዲሆን። መዝ፡ ፪፤ ፰።
ዕብ፡ ፩፤ ፪።
፲፭፤ ከወይኑም፡ ወደ፡ ሜደ፡ አወጡት፡ ገደሉት
ም። ምንስ፡ ያደርግባቸዋል፡ የወይኑ፡ ባለ፡ ቤት።
፲፮፤ ይመጣል፡ እሊያንም፡ ጠባቆች፡ ያጠፋል። ወ
ይኑንም፡ለሌሎች፡ይስጣል።በሰሙም፡ጊዜ፡አሉ።ይ
ህ፡አይሁን።
፲፯፤ እርሱ፡ግን፡ወደርሳቸው፡ አዮ፡ አለም። ይህ፡ የ
ተጻፈው፡ምንድር፡ነው። አናጾች፡የናቁት፡ ደንጊያ፡ ይ
ህ፡ የማዝን፡ ራስ፡ሆነ። መዝ፡ ፻፲፰፤ ፳፪።
ኢሳ፡ ፰፤ ፲፬።
፲፰፤ በዚያም፡ደንጊያ፡ላይ፡የሚወድቅ፡ሁሉ፡ይቀ
ጠቀጣል።እርሱም፡ የወድቀበትን፡ ሁሉ፡ ይደቍስ
ዋል። ሮሜ፡ ፱፤ ፴፫። ፩፡ጴጥ፡ ፪፤ ፯። ዳን፡ ፪፤ ፵፬።
፲፱፤ የክህናት፡አለቆችም፡ጻፎችም፡በዚያች፡ጊዜ፡
እጃቸውን፡ ይጥሉበት፡ ዘንድ፡ ይሹ፡ ነበሩ። ሕዝቡን
ም፡ፈሩ።አውቀዋልና፡ ይህነን፡ ምሳሌ፡ስለርሳቸው፡
እንደ፡ ተናገረ። ም፡ ፲፱፤ ፵፰።
፳፤ ተጠባበቁትም፡ ሰላዮችንም፡ ላኩ፡ ጻድቃን፡
መስለው፡በነገር፡ሊጸምዱት።ወደ፡ለቆች፡አሳልፎ፡ሊ
ሰጡት፡ ወደ፡ ሹሙም፡ ሥልጣን።
ማቴ፡ ፳፪፤ ፲፭—፳፪። ማር፡ ፲፪፤ ፲፫—፲፯።
፳፩፤ እንዲህም፡ ሲሉ፡ ጠየቁት። መምህር፡ ሆይ፡
አወቅነ፡ በውነት፡ እንድትናገር፡ እንድታስተምርም፡
ለሰው፡ፊትም፡አታደላም፡የእግዚአብሔርን፡መንገ
ድ፡ በውነት፡ ታስተምራለህ፡ እንጂ።
፳፪፤ ይገባናልን፡ለቄሣር፡ግብር፡እንሰጥ፡ዘንድ፡ወ
ይስ፡ አይሆንም።
፳፫፤ እርሱ፡ግን፡ ተንኰላቸውን፡ አወቀ፡ አላቸው
ም። ለምን፡ ትፈታተኑኛላችሁ።
፳፬፤ የግብሩን፡ወርቅ፡ አሳዩኝ። የማነው፡ይህ፡ ሥ
እሉ፡ጽፈቱስ።መለሱም፡ አሉም። የቄሣር።
፳፭፤ እርሱም፡ አላቸው። እንኪያስ፡ የቄሣርን፡
ለቄሣር፡ ስጡ፡ የእግዚአብሔርንም፡ ለእግዚአብ
ሔር። ም፡ ፳፪፤ ፬፤
፳፮፤ በሕዝቡ፡ ፊትም፡ ሊጥሉት፡ አልተቻላቸው
ም።ከምላሹም፡ተደነቁ፡ ዝምም፡አሉ።
፳፯፤ ከሰዱቃውያንም፡ሰዎች፡ወደርሱ፡መጡ፡ የ
ሚሉ፡ትንሣኤ፡የለም። ጠየቁትም፡ እንዲህ፡ ሲሉ።
ማቴ፡ ፳፪፤ ፳፫—፴፫። ማር፡ ፲፪፤ ፲፰—፳፯።
፳፰፤ መምህር፡ ሆይ፡ሙሴ፡ *ጻፈልን። ማንም፡ ወ
ንድሙ፡ ቢሞት፡ ለርሱም፡ ምሽት፡ ያለችው፡ እርሱ
ም፡ቢሞት፡ያለ፡ልጅ፡ወንድሙ፡ ምሽቱን፡ ይውሰድ፡
ለወንድሙም፡ዘር፡ ያስነሣ። ዘዳግ፡ ፳፭፤ ፭።
፳፱፤ ሰባትም፡ ወንድማማች፡ ነበሩ። የፊተኛው፡
ምሽት፡ አገባ፡ ሳይወልድም፡ ሞተ።
፴፤ ሁለተኛውም፡ አገባት። ይህም፡ ሳይወልድ፡
ሞተ።
፴፩፤ ሦስተኛውም፡ወሰዳት። እንዲሁም፡ ሰባቱ።
ልጅን፡ አልተውም፡ ሞቱም።
፴፪፤ ከሁሉም፡በኋላ፡ ሴቲቱ፡ ደግሞ፡ ሞተች።
፴፫፤ እንኪያስ፡በትንሣኤ፡ከርሳቸው፡ለማን፡ም
ሽት፡ ትሆናለች። ሰባቱ፡ ምሽት፡ አድርገዋታልና።
፴፬፤ የሱስም፡መለሰ፡አላቸውም።የዚህ፡ዓለም፡
ልጆች፡ ያገባሉ፡ ይጋባሉም።
፴፭፤ ያነን፡ዓለም፡ግን፡መውረስ፡የሚገባቸው፡ት
ንሣኤም፡ ከሙታን፡ አያገቡም፡ አይጋቡምም።
፩፡ ቆሮ፡ ፲፭፤ ፵፫፤ ፶፫።
፴፮፤ ደግሞ፡ይሞቱ፡ ዘንድ፡አይቻላቸውምና። እ
ንደ፡*መላእክት፡ናቸውና።እርሳቸውም፡†የእግዚአ
ብሔር፡ ልጆች፡ ናቸው፡ የትንሣኤ፡ ልጆች፡ ስለ፡ ሆኑ።
*ሮሜ፡ ፰፤ ፳፫። †፩፡ ዮሐ፡ ፫፤ ፪።
፴፯፤ ሙታን፡እንዲነሡ፡ግን፡በዚያ፡*ሙሴ፡ተናግ
ሮዋል፡ በቍጥቋጦው፡ ባለ፡ጊዜ። እግዚአብሔር፡ የአ
ብርሃም፡ አምላክ። የይስሐቅም፡ አምላክ። የያዕቀ
ብም፡ አምላክ። *ዘፀአ፡ ፫፤ ፮። የሐዋ፡ ፯፤ ፴፪።
፴፰፤ እግዚአብሔር፡የሙታን፡ አምላክ፡ አይደለ
ምና፡ የሕያዋን፡ እንጂ። ሁሉ፡ለርሱ፡ ሕያዋን፡ ናቸ
ውና።
፴፱፤ ከጻፎችም፡ሰዎች፡መለሱ፡ አሉም። መምህ
ር፡ ሆይ፡ መልካም፡ ተናገርህ።
፵፤ ከዚያም፡በኋላ፡አልደፈሩም፡በምንም፡ ይጠ
ይቁት፡ ዘንድ።
፵፩፤ አላቸውም። እንዴት፡ ይላሉ፡ ክርስቶስ፡ የዳ
ዊት፡ ልጅ፡ እንደ፡ ሆነ። ማቴ፡ ፳፪፤ ፵፩—፵፭።
ማር፡ ፲፪፤ ፴፭።
፵፪፤ ዳዊትም፡ራሱ፡በመዝሙራት፡ መጽሐፍ፡አ
ለ። ጌታ፡ ጌታዬን፡ በቀኜ፡ ተቀመጥ፡ አለው።
መዝ፡ ፻፲፤ ፩።
፵፫፤ ጸላቶችህን፡ለእግርህ፡ድኳ፡ አስካደርግልህ፡
ድረስ።
፵፬፤ ዳዊትም፡ጌታ፡ይለዋል።እንዴትስ፡እርሱ፡ል
ጁ፡ ነው።
፵፭፤ ሕዝቡም፡ ሁሉ፡ ሲሰሙ፡ ደቀ፡ መዛሙርቱ
ን፡አለ።
፵፮፤ ከጻፎች፡ተጠበቁ፡በረጅም፡ልብስ፡መሔድ፡
የሚወዱ፡ በገቢያም፡ ሰላም፡ ይወደሉ። በመስጊድ
ም፡በፊት፡መቀመጥ፡የመርፈቂያውንም፡መጀመር
ያ፡ በምሳ። ም፡ ፲፩፤ ፵፫። ማቴ፡ ፳፫፤ ፮።

፵፯፡ የባልቴቶችን ፡ ቤት፡ የሚበሉ ፡ በምክንያት ም፡ጸሎታቸውን፡ ያረዝማሉ። እሌህ፡ታላቅ፡ ፍርድ፡ ይወስዷሉ።
ማር፡ ፲፪፡ ፵፡፡

ምዕራፍ፡ ፳፩፡

፩፡ ተመለከተም፡ ባለ፡ጠጎችንም፡አየ፡ ቍርባናቸ ውን፡ወደ፡መዝገብ፡የሚጥሉን።
፪፡ ነገሥ፡ ፲፪፡ ፱፡፡ ማር፡ ፲፪፡ ፵፩፡ — ፵፬፡፡

፪፡ ደግሞም፡ድኻ፡ባልቴት፡አየ፡ ከዚያ፡ ሁለት፡ ነሓስ፡ስትጥል።

፫፡ አለም።እውነት፡እላችኋለሁ፡ ይህች፡ድኻ፡ ባል ቴት፡ ከሁሉ፡*ይልቅ፡ አብዝታ፡ እንደ፡ ጣለች።
*፪፡ ቆሮ፡ ፰፡ ፲፪፡፡

፬፡ እሌህ፡ሁሉ፡ በእግዚአብሔር፡ መዝገብ፡ ከርኅ ቶቸው፡የተረፈውን፡ጥለዋልና። ይህች፡ግን፡ከነደትዋ፡ ለአደርዋ፡የነበራትን፡ ሁሉ፡ ጣለች፡፡

፭፡ ስዎችም፡ስለ፡ መቅደስ፡ በመልካም፡ ደንጊያ፡ አጌጦ፡እንደ፡ለ፡ስለ፡ ተሰጠለትም፡ ስጦታ፡ ሲናገሩ፡፡
ማቴ፡ ፳፬፡ ፩፡ —፳፩፡፡

፮፡ አለ።ይህ፡የምታዩት፡ዘመን፡ይመጣል፡ የማይ ቀርበት፡ ደንጊያ፡ በደንጊያ ፡ ላይ ፡ ይፈርሳል ፡ እንጂ።
ሚክ፡ ፫፡ ፲፪፡፡

፯፡ ጠየቁትም፡እንዲህ፡ሲሉ። መምህር፡ ሆይ፡ ይ ህ፡መቼ፡ይሆናል።ምልክቱስ፡ ምንድር፡ ነው፡ጊዜው፡ እንደ፡ መጣ፡ ይህ፡ ይሆን፡ ዘንድ።
ም፡ ፲፱፡ ፵፬፡፡

፰፡ እርሱም፡አለ።እዩ፡አትሳቱ። እጅግ፡ ሰዎች፡ በ ስሜ፡ይመጣሉና፡እንዲህ፡ ሲሉ። እኔ፡እንደ፡ ሆንሁ። ወራቱም፡ ቀርብዋል። በኋላቸውም፡ አትሒዱ።
ም፡ ፲፯፡ ፳፫፡፡

፱፡ ሰልፍና፡ ሁከትም፡ በሰማችሁ፡ጊዜ፡ አትፍሩ። ይህ፡በፊት፡ይሆን፡ዘንድ፡ይገባልና።ነገር፡ግን፡ፍጻሜ፡ አሁን፡ አይሆንም።

፲፡ የዚያን፡ጊዜ፡አላቸው። ሕዝብ፡ በሕዝብ፡ ላይ፡ ይነሣል፡ መንግሥትም፡ በመንግሥት፡ላይ።

፲፩፡ ታላቅም፡የምድር፡ መናወጥ፡በያገሩ፡ ትሆናለ ች፡ራብም፡በሽታም።ፍርሃትም፡ታላቅም፡ ምልክት፡ ከሰማይ።
ኢዮ፡ ፫፡ ፫፡፡

፲፪፡ ከዚህ፡ሁሉም፡አስቀድሞ፡ እጃቸውን፡ በላያ ችሁ፡ ይጥላሉ። ያሳድዋችኋልም፡ ወደ፡ መስጊድም፡ ወደ፡ እሥራትም፡ ይወስድዋችኋል። ወደ፡ ነገሥታት ም፡ ወደ፡ ሹማምትም፡ ያደርስዋችኋል፡ ስለ፡ ስሜ።
ም፡ ፲፪፡ ፲፩፡፡ ማር፡ ፲፫፡ ፱፡፡ የሐዋ፡ ፲፪፡ ፩፡ ፬፡፡

፲፫፡ ምስክርም፡ ይሆንላችኋል። ፊል፡ ፩፡ ፲፱፡፡

፲፬፡ አሁንም፡በልባችሁ፡አኑሩት፡አስቀድማችሁ፡ እንደታስቡ፡ በምትሉት።
ማቴ፡ ፲፡ ፲፱፡፡

፲፭፡ እኔ፡አፍና፡ጥበብ፡ እሰጣችኋለሁና፡ ቦደረኞቻ ችሁ፡ሁሉ፡ከርሰዋ፡ጋራ፡መጣላትና፡መቋቋም፡ የማ ይችሉትን።
የሐዋ፡ ፯፡ ፲፡፡

፲፮፡ የምትሰጡበትም፡ጊዜ፡አላችሁ፡ካባቶች፡ደግ

፲፯፡ ከሁሉም ፡ የተጸላችሁ፡ ትሆናላችሁ ፡ ስለ፡ስ ሜ።
ማቴ፡ ፲፡ ፳፩፡ ፳፪፡፡

፲፰፡ ከራሳችሁም፡ አንዲት፡ ጸጕር ፡ አትጠፋም።
ም፡ ፲፪፡ ፯፡፡

፲፱፡ በትዕግሥታችሁ፡ ነፍሳችሁን፡ ትገዛላችሁ።
፪፡ ዜና፡ ፲፭፡ ፯፡፡ ዕብ፡ ፲፡ ፴፮፡፡

፳፡ የሩሳሌምም፡በጭፍራ፡ተከባ፡ባያችሁ፡ጊዜ፡የ ዚያን፡ጊዜ፡እወቁ፡ጥፋትዋ፡እንደ፡ደረሰ።
ዳን፡ ፱፡ ፳፯፡፡

፳፩፡ የዚያን፡ጊዜ፡በይሁዳ፡ያሉ፡ ወደ፡ተራራ፡ ይሸ ሹ። በመካከልዋም፡ ያሉ፡ ወጥተው፡ ይበሩ። በምድ ረ፡ በዳም፡ ያሉ፡ አይግቡዋትም።
ማቴ፡ ፳፬፡ ፲፭፡፡

፳፪፡ ይህ፡*የበቀል፡ጊዜ፡ነውና፡የተጻፈው፡ሁሉ፡ይ ፈጸም፡ ዘንድ።
*ኤር፡ ፭፡ ፳፱፡፡

፳፫፡ ወዮላቸው ፡ ግን፡ ለርጉዞች ፡ ለሚያጠቡም፡ በዚያች፡ወራት።ጽኑ፡መከራ፡ ይሆናልና፡ በምድር፡ ላ ይ፡ቍጣም፡ በዚህ፡ሕዝብ።

፳፬፡ በሰይፍ፡ አፍም፡ ይወድቃሉ፡ ወደ፡አሕዛብ፡ ሁሉም፡ይማርካሉ።የሩሳሌምም፡ከአሕዛብ፡ የተረ ገጠች፡ ትሆናለች ፡ *የአሕዛብ፡ ዘመን፡ እስክትፈጸ ም፡ ድረስ።
*ሮሜ፡ ፲፩፡ ፳፭፡፡ ራእ፡ ፲፩፡ ፪፡፡
ዘዳግ፡ ፳፰፡ ፷፬፡፡

፳፭፡ ምልክትም፡*በጸሓይ፡ይሆናል፡ በጨረቃም፡ በከዋክብትም። በምድርም፡ላይ፡ የአሕዛብ፡ ጭንቀ ት፡በፍርሃት፡ †ከባሕሩ፡ መበጣበጥ ፡ የተነሣ፡ ከሞገ ዱም።
*ኢሳ፡ ፲፫፡ ፲፡፡ † መዝ፡ ፵፮፡ ፬፡፡

፳፮፡ የሰዎችም ፡ ነፍስ፡ ትደክማለች፡ *ከፍርሃት፡ የተነሣ፡በዓለሙም፡ላይ፡ የሚመጣውን፡ ከመመል ከት፡ የተነሣ። የሰማዮች፡ ኃይል፡ ትናወጣለችና።
ኢሳ፡ ፰፡ ፯፡፡ሕዝ፡ ፳፬፡ ፳፫፡፡

፳፯፡ የዚያን፡ጊዜም፡የሰው፡ ልጅ፡ በደመና፡ ሲመ ጣ፡ ያያሉ፡ ከታላቅ፡ ኃይል፡ ከመስጋናም ፡ ጋራ።
ዳን፡ ፯፡ ፲፫፡፡ ራእ፡ ፩፡ ፯፡፡

፳፰፡ ይህች፡ ትሆንም፡ ዘንድ፡ በጀመረች፡ ጊዜ፡ ወ ደ፡ላይ፡እዩ፡*ራሳችሁንም፡ አንሡ። ደህንነታችሁ፡ ቀ ርብዋልና።
ሮሜ፡ ፰፡ ፳፩፡ ፳፫፡፡ ፊል፡ ፬፡ ፬፡ ፭፡፡

፳፱፡ ምሳሌም፡አላቸው።እዩ፡ወደ፡በለስ፡ወደ፡ሁ ሉም፡ዛፍ።
ማቴ፡ ፳፬፡ ፴፪፡፡

፴፡ በለመለመች ፡ ጊዜ፡ ታያላችሁ፡ ከሰውነታችሁ ም፡ታውቃላችሁ፡በጋ፡ እንደ፡ ቀረበ።

፴፩፡ እንዲሁ፡እላንትም፡ደግሞ፡ ይህችን፡ ሁና፡ባ ያችሁ፡ጊዜ፡እወቁ፡የእግዚአብሔር፡መንግሥት፡እን ደ፡ ቀረበች።

፴፪፡ እውነት፡እላችኋለሁ፡ ይህ፡ ትውልድ፡ እንዲ ያልፍ፡ ሁሉ፡ እስኪሆን፡ ድረስ።

፴፫፡ ሰማይና ፡ ምድር፡ ያልፋሉ፡ ነገሬ፡ ግን፡ አያል ፍም።
ም፡ ፲፮፡ ፲፯፡፡ ኢሳ፡ ፶፩፡ ፮፡፡

፴፬፡ በነፍሳችሁ፡ግን፡ተጠንቀቁ፡ ልባችሁ፡ በሥሥ

ም፡ከወንድሞችም፡ከዘመዶችም፡ከወዳጆችም፡ከ
ላንትም፡ ይገላሉ። ሚክ፡ ፯፥ ፮።
ት፡ በስካርም፡ እንዳይደነድን፡ ስለ፡ አደርም፡ በማሰ
ብ። ያም፡ ቀን፡ ድንገት፡ እንዳይደርስባችሁ።
ሮሜ፡ ፲፫፥ ፲፫። ፩፥ ጴጥ፡ ፬፥ ፯፥ ፰። ገላት፡ ፭፥ ፳፩።
፴፭፥ እንደ፡ወጥመድ፡ይደርሳልና፡በምድር፡ፊት፡
በተቀመጠው፡ ሁሉ፡ ላይ። ፩፥ ተሰ፡ ፭፥ ፳፩።
፴፮፥ ስለዚህ፡ትጉ፡ሁለግዜም፡ጸልዩ፡ከዚህ፡ሁሉ፡
ነገር፡መሸሸት፡እንዲገባችሁ፡ ይሆን፡ ዘንድ፡ ጊዜ፡ ካለ
ው። በሰው፡ ልጅ፡ ፊትም፡ መቆም። ኤር፡ ፮፥ ፲፫።
፩፥ ተሰ፡ ፭፥ ፮። ፪፥ ጴጥ፡ ፫፥ ፲፩።
፩፥ ዮሐ፡ ፪፥ ፳፰። ም፡ ፱፥ ፲፯።
፴፯፥ በቀንም፡በመቅደስ፡ያስተምር፡ ነበር፡ በሌት
ም፡ወደ፡ተራራ፡ወጥቶ፡ ይቀመጥ፡ ነበር፡ *ደብረ፡ ዘይ
ት፡ ወደሚባለው። *ዮሐ፡ ፰፥ ፩፥ ፪።
፴፰፥ ሕዝብም፡ ሁሉ፡ ወደርሱ፡ ይማልዱ፡ ነበር፡
በመቅደስ፡ ከርሱ፡ ይሰሙ፡ ዘንድ።

ምዕራፍ፡ ፳፪።

፩፥ በዓለ፡ ናእትም፡ ቀረበ፡ ፋሲካ፡ የሚባለው።
ማቴ፡ ፳፮፥ ፩፥—፭።
፪፥ የካህናት፡ አለቆችም፡ ጻፎችም፡ እንደምን፡ ያ
ጠፉት፡ ዘንድ፡ ይሹ፡ ነበሩ። ሕዝቡን፡ ይፈሩ፡ ነበሩና።
መዝ፡ ፪፥ ፪። ዮሐ፡ ፲፩፥ ፵፯።
፫፥ ሰይጣንም፡በይሁዳ፡ገባ፡ አስቆሮታዊ፡የሚባለ
ው፡ ካሥራ፡ ሁለቱ፡ ቍጥር፡ የነበረው።
ማቴ፡ ፳፮፥ ፲፬፥ ፲፮።
፬፥ ሔደም፡ለካህናትም፡አለቆች፡ለታላላቆች ጋ፡
ነገረ፡ እንዴት፡ ያሲዛቸው፡ ዘንድ።
፭፥ ደስም፡አላቸው፡ከርሱም፡ጋራ፡ ተሰማሙ፡ ብ
ር፡ይሰጡት፡ ዘንድ።
፮፥ ተስፋም፡ ሰጣቸው። ምቹም፡ ጊዜ፡ ይሻ፡ ነበረ፡
ያሲዛቸው፡ ዘንድ፡ ያለ፡ ሽብርት።
፯፥ በዓለ፡ናእትም፡መጣ፡ *ፋሲካ፡ይታረድበት፡ዘ
ንድ፡ ይገባ፡ የነበረው። *ዘፀአ፡ ፲፪፥ ፲፰፥—፳።
፰፥ ጴጥሮስንና፡ ዮሐንስም፡ ላከ፡ እንዲህ፡ ሲላቸ
ው። ሒዱ፡ ፋሲካንም፡ ለኛ፡ አዘጋጁ፡ እንበላ፡ ዘንድ።
፱፥ እርሳቸውም፡ አሉት። ወዴት፡ ትሻለህ፡ እናሰ
ናዳ፡ ዘንድ።
፲፥ እርሱም፡ አላቸው። እነሆ፡ ወደ፡ ገር፡ በገባችሁ፡ ጊ
ዜ፡ ማድጋ፡ ውኃ፡ የተሸከመ፡ ሰው፡ ያገኛችኋል። ወደ
ሚገባው፡ ቤት፡ ተከተሉት።
፲፩፥ ለቤቱም፡ጌታ፡ በሉት። መምህር፡ ይልሃል። ወ
ዴት፡ነው፡የዕረፍት፡ ሰፍራ፡ ፋሲካን፡ የምበላበት፡ ከ
ደቀ፡መዛሙርቴ፡ጋራ።
፲፪፥ ያም፡ታላቅ፡ቤት፡ ንጡሥ፡ ያሳያችኋል፡ የተነጸ
ፈ። ከዚያ፡ አስናዱ። ማር፡ ፲፬፥ ፲፭።
፲፫፥ ሒደውም፡ *አገኙ፡ እንዳላቸው። ፋሲካንም፡
አዘጋጁ። *ም፡ ፲፱፥ ፴፪።
፲፬፥ ጊዜውም፡ በደረሰ፡ ጊዜ፡ ለመብል፡ ተቀመጠ፡
ከርሱም፡ ጋራ፡ አሥራ፡ ሁለቱ፡ ሐዋርያት።
፲፭፥ አላቸውም። መውደድን፡ ወደድሁ፡ ይህነን፡ ፋ
ሲካ፡ ከላንት፡ ጋራ፡ እበላ፡ ዘንድ፡ ከሕማሜ፡ በፊት።
፲፮፥ እላችኋለሁና፡ ይህነን፡ ደግሞ፡ እንዳልበላ፡ እስ
ኪፈጸም፡ ድረስ፡ በእግዚአብሔር፡ መንግሥት።
ም፡ ፲፫፥ ፳፱።
፲፯፥ ጽዋም፡ ተቀበለ፡ አመሰገነም፡ አለም። ይህነ
ን፡ እንኩ፡ በመካከላችሁም፡ ተካፈሉት።
፲፰፥ *እላችኋለሁና፡ ከወይኑ፡ ፍሬ፡ እንዳልጠጣ፡
የእግዚአብሔር፡ መንግሥት፡ እስክትመጣ፡ ድረስ።
*ማቴ፡ ፳፮፥ ፳፱።
፲፱፥ እንጀራም፡ ወስደ፡ አመሰገነም፡ ቈረሰም፡ ሰ
ጣቸውም፡ እንዲህ፡ ሲል። ይህ፡ ነው፡ ሥጋዬ፡ ስለላን
ት፡ የሚሰጠው። ይህነን፡ አድርጉት፡ ለመታሰቤ።
፩፥ ቆሮ፡ ፲፩፥ ፳፫።
፳፥ ደግሞም፡ እንዲሁ፡ ጽዋውን፡ ከእራት፡ በኋላ፡
እንዲህ፡ ሲል። ይህ፡ ጽዋ፡ አዲስ፡ ሥርዓት፡ ነው፡ በደ
ሜ፡ ስለላንት፡ የሚፈሰው። ዘፀአ፡ ፳፬፥ ፰።
ዕብ፡ ፲፪፥ ፰፥ ፳፪፥
፳፩፥ ነገር፡ ግን፡ እነሆ፡ አሳልፎ፡ የሚሰጠኝ፡ እጁ፡ ከ
ኔ፡ ጋራ፡ ነው፡ በማዕድ። መዝ፡ ፵፩፥ ፲።
፳፪፥ የሰው፡ ልጅም፡ ይሔዳል፡ እንደ፡ ተጻፈ። ነገር፡
ግን፡ ወዮለት፡ ለዚያ፡ ሰው፡ አሳልፎ፡ ለሚሰጠው።
፳፫፥ እርሱ፡ በርሳቸውም፡ ይጠያየቁ፡ ጀመሩ፡ እን
ጂ፡ ከርሳቸው፡ ይህነን፡ ያደርገው፡ ዘንድ፡ ያለው፡ ማ
ነው።
፳፬፥ በመካከላቸውም፡ ደግሞ፡ ክርክር፡ ነበረ፡ ከር
ሳቸው፡ ማናቸው፡ ታላቅ፡ እንደ፡ ሆነ፡ የሚመስለው።
ም፡ ፱፥ ፵፮።
፳፭፥ እርሱ፡ ግን፡ አላቸው። የአሕዛብ፡ ነገሥታት፡
እርሳቸውን፡ ይገዙዋቸዋል። የነገሡባቸውም፡ ቸርነ
ት፡ አድራጎች፡ ይባላሉ። ማቴ፡ ፳፥ ፳፭፥ ፳፮።
ማር፡ ፲፥ ፵፪።
፳፮፥ እላንት፡ ግን፡ እንዲህ፡ አይደለም። ነገር፡ ግን፡
ከላንት፡ ታላቁ፡ እንደ፡ ታናሽ፡ ይሁን፡ አለቃውም፡ እን
ደ፡ ሎሌ። ፊል፡ ፪፥ ፫። ፩፥ ጴጥ፡ ፭፥ ፫፥ ፭፥ ፮።
፳፯፥ ማናቸውም፡ ይበልጥ። ተቀምጦ፡ የሚበላ
ውን፡ ወይስ፡ ቁሞ፡ የሚያገለግለው። ተቀምጦ፡ የሚ
በላው፡ አይደለምን። እኔ፡ ግን፡ በመካከላችሁ፡ እንደ፡
ሎሌ፡ ነኝ። ዮሐ፡ ፲፫፥ ፬፥—፲፬።
፳፰፥ ነገር፡ ግን፡ እላንት፡ ናችሁ፡ ከኔ፡ ጋራ፡ በመከራ
ዬ፡ የታገሣችሁ። ም፡ ፲፰፥ ፳፰።
፳፱፥ እኔም፡ መንግሥትን፡ አዘጋጅላችኋለሁ፡ አባ
ቴ፡ ለኔ፡ እንደዘጋጀት። ራእ፡ ፫፥ ፳፩።
፴፥ ትበሉ፡ ትጠጡም፡ ዘንድ፡ በማዕዴ፡ በመንግሥ
ቴ። ባሥራ፡ ሁለቱም፡ ዙፋን፡ ትቀመጡ፡ ዘንድ፡ ባሥ
ራ፡ ሁለቱም፡ በእሥራኤል፡ ነገድ፡ ትፈርዱ፡ ዘንድ።
ማቴ፡ ፲፱፥ ፳፰፥

፴፩፡ ጌታም፡አለ።ሲሞን፡ሲሞን።እነሆ፡ሰይጣን፡ በላንት፡ ተመኘ፡ ሊነፋችሁ፡ እንደ፡ ስንዴ።
ማቴ፡ ፳፮፡ ፴፩፡—፴፭። አሞ፡ ፱፡ ፱፡፡ ፩፡ጴጥ፡ ፭፡ ፰፡

፴፪፡ እኔ፡ግን፡ ስላንት፡*ለመንሁ፡ ሃይማኖትህ፡እንዳይጐድል። †አንተም፡ በተመለስህ፡ ጊዜ፡ ወንድሞችህን፡ አጽና።
*ዮሐ፡ ፲፯፡ ፲፩፡ ፲፭፡ ፳፡፡
†መዝ፡ ፶፩፡ ፲፫፡፡

፴፫፡ እርሱም፡ አለው። አቤቱ፡ እኔ፡ የተዘጋጀሁ፡ ነኝ፡ካንተ፡ጋራ፡ወደ፡እሥራት፡ወደ፡ሞትም፡እሔድ፡ ዘንድ።
ዮሐ፡ ፲፫፡ ፴፯፡፡

፴፬፡ እርሱም፡አለ፡እልሃለሁ፡ጴጥሮስ፡ሆይ።ዛሬ፡ ዶሮ፡ እንደይጮህ፡ ሶስት፡ጊዜ፡ እስክትክደኝ፡ ድረስ፡ እንደታውቀኝ።

፴፭፡ አላቸውም። በላክኋችሁ፡ ጊዜ፡ ያለ፡ ከረጢት፡ያለ፡ስንቅም፡ያለ፡ጫማም፡አንዳች፡ጎደላችሁን። እርሳቸውም፡አሉ። አንዳች፡ ሰንኳ።
ም፡ ፱፡ ፫፡፡

፴፮፡ አላቸውም፡ዛሬ፡ግን፡ከረጢት፡ያለው፡ይውሰድ።እንዲሁም፡ስንቅ።ሰይፍ፡የሌለው፡ልብሱን፡ይሽጥና፡ ሰይፍ፡ ይግዛ።

፴፯፡ እላችኋለሁና፡ይህ፡ የተጻፈው፡ ደግሞ፡ ይፈጸምበኝ፡ዘንድ፡ ይገባል። *ከኃጢአተኞች፡ ጋራ፡ ተቈጠረ፡ተብሎ።ስለኔ፡ የተጻፈው፡ ፍጻሜ፡ አለውና።
*ኢሳ፡ ፶፫፡ ፲፪፡

፴፰፡ እርሳቸውም፡አሉ። አቤቱ፡እነሆ፡ ከዚህ፡ ሁለት፡ሰይፎች፡ አሉ። እርሱም፡ አላቸው፡ ይበቃል።
ማቴ፡ ፳፮፡ ፴፮፡—፵፮፡፡

፴፱፡ ወጥቶም፡ሔደ፡እንደ፡ ልማዱ፡ ወደ፡ ደብረ፡ ዘይት። ደቀ፡ መዛሙርቱም፡ ደግሞ፡ ተከተሉት።
ማር፡ ፲፬፡ ፴፪፡—፵፪፡፡

፵፡ ወደ፡ቦታም፡በደረሰ፡ጊዜ፡ አላቸው። ጸልዩ፡ ወደ፡ መከራ፡ እንዳትገቡ።

፵፩፡ እርሱም፡ከርሳቸው፡ ራቀ፡ የድንጊያ፡ ውርወራ፡ያህል። በጕልበቱም፡ ተንበረከከና፡ ጸለየ።

፵፪፡ እንዲህ፡ ሲል። አባቴ፡ ሆይ። ብትወድስ፡ ከኔ፡ ትለፍ፡ይህቺ፡ ጽዋ።ነገር፡ ግን፡ ፈቃዴ፡ አይደለም። ፈቃድህ፡ ትሁን፡ እንጂ።

፵፫፡ ከሰማይም፡ መልአክ፡ ለርሱ፡ ታየው፡ ሊያጸናው።
፩፡ ነገሥ፡ ፲፱፡ ፭፡

፵፬፡ እጅግም፡ተጋደለ፡በጽኑም፡ጻር፡ ይጸልይ፡ ነበር። ወዙም፡ እንደ፡ ደም፡ ነጠብጣብ፡ በምድር፡ ላይ፡ ወረደ።
መዝ፡ ፲፰፡ ፭፡ ፯፡፡ ዮሐ፡ ፲፰፡ ፲፰፡
ዕብ፡ ፬፡ ፲፬፡ ፲፭፡

፵፭፡ ከጸሎትም፡ተነሥቶ፡ወደ፡ደቀ፡መዛሙርቱ፡ መጣ፡ከኃዘንም፡ የተነሣ፡ ተኝተው፡ አገኛቸው።

፵፮፡ አላቸውም። ለምን፡ ትተኛላችሁ። ተነሡና፡ ጸልዩ፡ ወደ፡ መከራ፡ እንዳትገቡ።

፵፯፡ እርሱም፡ ሲናገር፡ ሰዎች፡ መጡ። ይሁዳም፡ የሚባለው፡ ካሥራ፡ ሁለቱ፡አንዱ፡በፊታቸው፡ይሔድ፡ ነበረ። ወደ፡ የሱስም፡ ቀረበ፡ ሳመውም።
ማቴ፡ ፳፮፡ ፵፯፡—፶፯፡፡

፵፰፡ የሱስ፡ግን፡አለው።ይሁዳ፡ሆይ፡ በመሳምን፡ የሰውን፡ ልጅ፡ አሳልፈህ፡ ትሰጣለህ።
ማር፡ ፲፬፡ ፵፫፡—፶፡፡ ዮሐ፡ ፲፰፡ ፫፡—፲፬፡፡

፵፱፡ ከርሱም፡ጋራ፡የነበረት፡ የሚሆነውን፡ ባዩ፡ ጊዜ፡ አሉት። አቤቱ፡ በሰይፍ፡ እንምታን።

፶፡ ከርሳቸውም፡አንዱ፡የካህናቱን፡ አለቃ፡ባርያ፡ መታ፡ ቀኝ፡ ጆሮውንም፡ ቈረጠው።

፶፩፡ የሱስም፡መለሰ፡አለም። አሁንስ፡ተው። ጆሮውንም፡ ደሶ፡አዳነው።

፶፪፡ የሱስም፡አለ፡ወደርሱ፡ለመጡት፡ለካህናት፡ አለቆች፡ለመቅደስም፡አዛዦች፡ ለሽማግሌቾም።በሌባ፡ ላይ፡ እንድትወጡን፡ ከሰይፍና፡ በበትር፡ ወጣችሁ።

፶፫፡ ሁለግዜ፡ከላንት፡ጋራ፡ ነበርሁ፡ በመቅደስ፡ *እጆቻችሁንም፡አልዘረጋችሁብኝም። ነገር፡ግን፡ ይህች፡ ጊዜያችሁ፡ ናት፡ የጨለማውም፡ ሥልጣን።
*ዮሐ፡ ፯፡ ፴፡፡ ፰፡ ፳፡፡

፶፬፡ ወሰዱትም፡ ይዘውትም፡ መጡ፡ ወደ፡ ካህናት፡አለቃ፡ቤትም፡አገቡት።ጴጥሮስ፡ ግን፡ከሩቅ፡ ይከተለው፡ ነበር።
ማቴ፡ ፳፮፡ ፶፰፡—፸፭፡፡

፶፭፡ እሳትም፡በአደራሽ፡ መካከል፡ ባነደዱ፡ ባንድም፡ በተቀመጡ፡ ጊዜ፡ ጴጥሮስ፡ ተቀመጠ፡ በመካከላቸው።
ዮሐ፡ ፲፰፡ ፲፭፡ ፳፯፡፡

፶፮፡ አንዲት፡ባርያም፡ አየችው፡ በእሳቱ፡ ተቀምጦ፡አስተዋለችውም፡አለችም።ይህ፡ደግሞ፡ ከርሱ፡ ጋራ፡ ነበረ።

፶፯፡ እርሱ፡ ግን፡ ካደው፡ እንዲህ፡ ሲል። አንቺ፡ ሴት፡ አላውቀውም።

፶፰፡ ጥቂትም፡ቈይቶ፡ሌላው፡ አየው፡ አለም።አንተም፡ደግሞ፡ከርሳቸው፡ወገን፡ነህ።ጴጥሮስም፡አለው። አንተ፡ሰው፡እኔ፡ አይደለሁም።

፶፱፡ ካንድ፡ሰዓትም፡ በኋላ፡ ሌላው፡ ነገር፡ አጸናበት፡ እንዲህ፡ ሲል። በውነት፡ ይህ፡ደግሞ፡ ከርሱ፡ጋራ፡ ነበረ።እርሱ፡ ደግሞ፡ ገሊላዊ፡ ነውና።

፷፡ ጴጥሮስም፡አለ።አንተ፡ሰው፡የምትለውን፡ አላውቅም። በዚያን፡ ጊዜም፡ እርሱ፡ ሲናገር፡ ዶሮ፡ ጮኸ።

፷፩፡ ጌታም፡ተመልሶ፡ጴጥሮስን፡አየው። ጴጥሮስም፡የጌታን፡ነገር፡አሰበ፡እንደለው። ዶሮ፡ ሳይጮህ፡ ሶስት፡ ጊዜ፡ ትካደኛለህ።
ቍ ፴፬፡

፷፪፡ ጴጥሮስም፡ሜደ፡ ወጣ፡ መራራ፡ ልቅሶም፡ አለቀሰ።

፷፫፡ የሱስንም፡የያዙት፡ ሰዎች፡ ያፊዙበት፡ ይመቱትም፡ ነበሩ።
ማር፡ ፲፬፡ ፷፭፡፡

፷፬፡ ሸፍነውም፡ ፊቱን፡ ይጸፉት፡ ነበሩ፡ እንዲህ፡ ሲሉም፡ ይጠይቁት፡ ነበር። ንገረን፡ ማነው፡ የመታህ።

፷፭፤ ሌላም፡ እጅግ፡ ነገር፡ ይሉት፡ ነበር፡ ኢየሰደ
ቡት።
፷፮፤ ቀንም፡ በሆነ፡ ጊዜ፡ ተከማቹ፡ የካህናቱ፡ አለ
ቆች፡የሕዝቡም፡ሽማግሌዎች፡ጻፎችም፡ወደ፡ሸንጎቸ
ውም፡ አመጡት።
፷፯፤ እንዲህ፡ ሲሉ። አንተ፡ ክርስቶስ፡ እንደ፡ ሆን
ህ፡ ንገረን። አላቸውም። ብነግራችሁም፡ አታምኑ
ኝም።
፷፰፤ ደግሞም፡ብጠይቃችሁ፡ አትመልሱልኝም፡
አተውኝምም።
፷፱፤ ከዛሬ፡ጀምሮ፡የሰው፡ልጅ፡በእግዚአብሔር፡
በኃይሉ፡ቀኝ፡የሚቀመጥ፡ ይሆናል። ማር፡ ፲፬፡ ፷፪፡፡
፸፤ ሁሉም፡አሉ።እንኪያስ፡አንተ፡የእግዚአብሔ
ር፡ልጅ፡ነህ።እርሱም፡አላቸው። እላንተ፡ ትላላችሁ።
እኔ፡ እንደ፡ ሆንሁ።
፸፩፤ እርሳቸውም፡አሉ።ምን፡ እንሻለን፡ ወደ፡ ም
ስክሮች። እኛ፡ ካፉ፡ ሰምተናልና።

ምዕራፍ፡ ፳፫፤

፩፤ ወገኖቻቸውም፡ሁሉ፡ተነሡ፡ ወደ፡ጲላጦስም፡
አመጡት። ማቴ፡ ፳፯፡፡ ማር፡ ፲፭፡፡
ዮሐ፡ ፲፰፡፡ ፫፡ ፲፱፡፡
፪፤ ያጣሉትም፡ጀመሩ፡እንዲህ፡ሲሉ። ይህነን፡አገ
ኘነ፡ ወገኖቻችንን፡ ሲገለብጥ።ግብርም፡*ለቄሣር፡እንደ
ይሰጥ፡ ይከለክላል። ክርስቶስ፡ንጉሥም፡ እንደ፡ ሆነ፡
ይናገራል። *ምዕ፡ ፳፡ ፳፭፡፡
፫፤ ጲላጦስም፡ጠየቀው፡ እንዲህ፡ ሲል። አንተን፡
ነህ፡ የአይሁድ፡ ንጉሥ። እርሱም፡ መለሰለት፡ እንደ
ህ፡ሲል። አንተ፡ አልህ።
፬፤ ጲላጦስ፡ግን፡ለካህናት፡አለቆች፡ ለተከማቹት
ም፡ አለ። በዚህ፡ ሰው፡ አንዲት፡ ምክንያት፡ አላገኘ
ሁም።
፭፤ እርሳቸው፡ግን፡ይጸኑ፡ ነበር፡ እንዲህ፡ ሲሉ። ሕ
ዝቡን፡ ያወካል፡ ኢያስተማረ፡ በይሁዳ፡ ሁሉ፡ ከገሊ
ላ፡ ጀምሮ፡ እስከዚህ፡ ድረስ።
፮፤ ጲላጦስ፡ግን፡ገሊላን፡በሰማ፡ጊዜ፡ጠየቀ፡ የገሊ
ላ፡ሰው፡ እንደ፡ ሆነ፡ ብሎ።
፯፤ ከሄሮድስ፡ግዛትም፡እንደ፡ሆነ፡ ባወቀ፡ ጊዜ፡ ወ
ደ፡*ሄሮድስ፡ሰደደው፡እርሱም፡ ደግሞ፡ በዚያች፡ ወ
ራት፡ በየሩሳሌም፡ ነበርና። *ምዕ፡ ፫፡ ፩፡፡
፰፤ ሄሮድስም፡የሱስን፡ ባየ፡ ጊዜ፡ እጅግ፡ደስ፡ አለ
ው፡ከብዙ፡ዘመን፡ጀምሮ፡*ያየው፡ዘንድ፡ ይመኝ፡ነበ
ርና። እጅግ፡ነገር፡ከርሱ፡ስለ፡ሰማ።ተስፋም፡ያደርግ፡
ነበረ፡እርሱ፡የሚያደርጋትን፡ተአምራት፡ያይ፡ዘንደ።
*ምዕ፡ ፱፡ ፱፡፡
፱፤ እጅግም፡ነገር፡ጠየቀው። እርሱ፡ ግን፡ ምንም፡
አልመለሰለትም።
፲፤ የካህናትም፡አለቆች፡ ጻፎችም፡ ቆሙ፡ እጅግ፡
ያጣሉትም፡ ነበሩ።
፲፩፤ ሄሮድስም፡ አቃለለው፡ ከሠራዊቱ፡ ጋራ፡ አፌ
ዙበትም። የሚያበለጨልጭ፡ ልብስም፡ አለበሰው፡
መልሶም፡ ወደ፡ ጲላጦስ፡ ሰደደው።
፲፪፤ ጲላጦስና፡ሄሮድስም፡በዚያ፡ ቀን፡ እርሱ፡ በር
ሳቸው፡ወዳጆች፡ሆኑ። ቀድሞ፡በመካከላቸው፡ጥል፡
ነበርና። የሐዋ፡ ፬፡ ፳፯፡፡
፲፫፤ ጲላጦስ፡ግን፡የካህናቱን፡ታላላቆች፡ጸራ፡የሕ
ዝቡንም፡ አለቆች።
፲፬፤ አላቸውም።ይህነን፡ሰው፡ ወደኔ፡ አመጣችሁ
ት፡ሕዝቡን፡እንዲመልስ።በፊታችሁም፡ እነሆ፡መረ
መርሁት፡ በዚህም፡ ሰው፡ ምክንያት፡ አላገኘሁበት
ም፡ በምታጣሉት፡ ነገር፡ ሁሉ። ቍ፡ ፪፡ ፬፡ ፭፡፡
፲፭፤ ሄሮድስ፡ ስንኳ። ወደርሱ፡ ሰድጀችሁ፡ ነበርሁ
ና፡እነሆም፡ ያደረገው፡ ነገር፡ የለም፡ ሞት፡ የሚገባ
በት።
፲፮፤ እኔም፡ቀጥቼ፡ልሰደደው። ዮሐ፡ ፲፱፡ ፩፡፡
፲፯፤ ልማድ፡ ነበረው፡ ግን፡ በየበዓሉ፡ አንድ፡ ሰው፡
ይተውላቸው፡ ዘንድ።
፲፰፤ ሕዝቡም፡ሁሉ፡ጮሁ፡ እንዲህ፡ ሲሉ። ይህን፡
አስነሣው፡ በርባንንም፡ ተውልን። የሐዋ፡ ፫፡ ፲፬፡፡
፲፱፤ ያም፡በግዘት፡ነበረ፡ሰላደረገው፡ነገር፡በሁከት፡
ነፍስ፡በመግደልም፡ባገር።
፳፤ ጲላጦስም፡ደግሞ፡ተናገረቸው፡የሱስንም፡ሊ
ተው፡ወደደ።
፳፩፤ እርሳቸው፡ግን፡ ጮሁ፡ እንዲህ፡ ሲሉ። ስቀለ
ው፡ ስቀለው።
፳፪፤ እርሱም፡ሶስተኛ፡አላቸው።ይህ፡ምን፡ ክፉ፡
አደረገ። ሞት፡ የሚገባው፡ ምክንያት፡ አላገኘሁበት
ም። ልቅጣውና፡ ልተወው።
፳፫፤ እርሳቸው፡ግን፡ የግድ፡ አሉት፡ በታላቅ፡ ቃል፡
ኢየጮሁ፡ ይሰቀለውም፡ ዘንድ፡ ለመኑት። ቃላቸው
ም፡ በረታ፡ የካህናት፡ አለቆችም፡ ቃል።
፳፬፤ ጲላጦስም፡ፈረደ፡ልመናቸው፡ይሆንላቸው፡
ዘንድ።
፳፭፤ ያነንም፡ በሁከትና፡ በመግደል፡ በግዘት፡ ተቀ
ምጦ፡የነበረውን፡ተወላቸው፡ የለመኑትን። የሱስን፡
ግን፡ ለፈቃዳቸው፡ አሳልፎ፡ ሰጣቸው።
፳፮፤ እርሳቸውም፡ ይዘውት፡ ሲሔዱ፡ አንድ፡ ሰ
ው፡ያዙ፡*ሲሞን፡ ቀሬናዊ፡ የሚሉት፡ ከሜዳ፡ ሲመ
ጣ። መስቀሉንም፡ በላዩ፡ ጫኑበት፡ ይሸከመው፡ ዘን
ድ፡ከየሱስ፡ በኋላ። ማቴ፡ ፳፯፡ ፴፪፡፡
ማር፡ ፲፭፡ ፳፩፡፡
፳፯፤ ከሕዝቡም፡እጅግ፡ሰዎች፡ይከተሉት፡ነበሩ፡
ሴቶችም።እርሳቸው፡ደግሞ፡ያልቅሱለት፡ ዋይ፡ይሉ
ትም፡ የነበሩት።
፳፰፤ የሱስም፡ ወደርሳቸው፡ ተመለሰ፡ አለም።
እላንተ፡ የየሩሳሌም፡ ልጆች፡ ለኔ፡ አታልቅሱልኝ። ነገ
ር፡ግን፡ስለ፡ራሳችሁ፡አልቅሱ፡ ስለ፡ ልጆቻችሁም።
፳፱፤ እነኋት፡ቀን፡ትመጣለችና፡የሚሉባት።ለመ

ካዮች፡ምስጋና፡ይገባቸዋል፡ላልወለደም፡ማሕፀን፡ላላጠባም፡ ጡት። ማቴ፡ ፳፬፡ ፲፱፡፡

፴፡ የዚያን፡ጊዜ፡ይጀምራሉ፡ተራሮችን፡ ይሉ፡ ዘንድ። በላያችን፡ ውደቁ። ኮረፍቶችንም፡ ድፈኑ። ሆሴ፡ ፲፡ ፰፡፡ ራእ፡ ፮፡ ፲፮፡፡

፴፩፡ በርጥብ፡ እንጨት፡ እንደህ፡ የሚያደርጉ፡ ከሆኑ፡ በደረቀውስ፡ እንዴት፡ ይሆን። ፩፡ ጴጥ፡ ፬፡ ፲፯፡ ፲፰፡፡

፴፪፡ ደግሞ፡ ሌሎችን ፡ ሁለት ፡ ክፉ፡ አድራጎችን፡ አመጡ፡ከርሱ፡ጋራ፡ይሰቀሉ፡ዘንድ። ዮሐ፡ ፲፱፡ ፲፰፡፡

፴፫፡ ወደ፡ቦታም፡ ቀራንዮ፡ ወደሚሉት፡ በመጡ፡ ጊዜ፡ከዚያ፡ ሰቀሉት፡ ክፉ፡ አድራጎችንም። አንዱን፡ በቀኙ፡ ሁለተኛውንም፡ በግራው።

፴፬፡ የሱስ፡ግን፡አለ።*አባቴ፡ሆይ፡ሰረይላቸው።የሚያደርጉትን፡አያውቁምና። ልብሱንም፡ ተካፈሉ፡ ዕፃም፡ ተጣጣሉበት። *ማቴ፡ ፭፡ ፵፬፡፡ ኢሳ፡ ፶፫፡ ፲፪፡፡ መዝ፡ ፳፪፡ ፲፰፡፡

፴፭፡ ሕዝብም፡ቁሞ፡ ያይ፡ ነበር፡ አለቆችም፡ ደግሞ፡ያፈዙበት፡ነበሩ፡ከርሳቸው፡ ጋራ፡ እንደህ፡ ሲሉ። ሌሎችን፡አድንዋልና፡ራሱንም፡ያድን። እርሱ፡ ክርስቶስ፡እግዚአብሔር፡ የመረጠው፡ ከሆነ።

፴፮፡ ጭፍራውም፡ደግሞ፡ያፈዙበት፡ ነበር፡ወደርሱም፡ ቀርበው፡ መጸጸ፡ አመጡለት፡ ኢያሉ።

፴፯፡ አንተስ፡የአይሁድ፡ንጉሥ፡እንደ፡ ሆንህ፡ራስህን፡አድን።

፴፰፡ ደግሞም፡ጽፈት፡በላዩ፡ተጽፎበት፡ነበረ፡በፅርዕ፡በሮሚ ም፡በዕብራይስጥም፡ፊደላት፡የሚል። ይህ፡ነው፡ የአይሁድ፡ ንጉሥ።

፴፱፡ ክፉ፡ካደረጉትም፡አንዱ፡ ከርሱ፡ ጋራ፡ ከተሰቀሉት፡ይሰድበው፡ነበረ፡ እንደህ፡ ሲል። አንተስ፡ ክርስቶስ፡ አንደ፡ ሆንህ፡ ራስህን፡ አድን፡ እኛንም።

፵፡ ሁለተኛው፡ ግን፡ መለሰ፡ ተቈጣውም፡ እንደህ፡ ሲል። አንተ፡ እግዚአብሔርን ፡ አትፈራምን፡ አንተ፡ በንደዚህ፡ ያለ፡ ኵነኔ፡ ሳለህ።

፵፩፡ እኛስ፡ በውነት፡ ፍዳችነን፡ እንደ፡ ድርጎታችነን፡ መጠን፡ የሚገባነውን፡ ተቀበልነ። ይህ፡ ግን፡ አንዲቹ፡ክፉ፡ አልሰራም።

፵፪፡ የሱስንም፡አለው። አስበኝ፡ አቤቱ፡ በመንግሥትህ፡ በመጣህ፡ ጊዜ። ነህም፡ ፲፫፡ ፴፩፡፡ ማቴ፡ ፲፮፡ ፳፰፡፡

፵፫፡ የሱስም፡ አለው ። በውነት፡ እልሃለሁ፡ ዛሬ፡ ከኔ፡ ጋራ፡ በገነት፡ እንድትሆን።

፵፬፡ ስድስት፡ ሰዓትም ፡ ጊዜ ፡ ነበረ ። ጨለማም፡ ሆነ፡በምድር፡ሁሉ፡ላይ፡እስከ፡ ዘጠኝ፡ ሰዓት፡ ድረስ። ፊል፡ ፩፡ ፳፩፡፡

፵፭፡ ጸሐይም ፡ ጨለመች ። የመቅደስም፡ መጋረጃ፡ ከመካከሉ ፡ ተከፈለ። ማቴ፡ ፳፯፡ ፶፩፡፡

፵፮፡ የሱስም፡በታላቅ፡ቃል፡ጮኸ፡ አለም።አባቴ፡ ሆይ፡*በጅህ፡ ነፍሴን፡ አደራ፡ እሰጣለሁ። ይህነንም፡ ባለ፡ጊዜ፡ ነፍሱን፡ ሰጠ። *መዝ፡ ፴፩፡ ፮፡፡ የሐዋ፡ ፯፡ ፶፰፡፡

፵፯፡ የመቶው፡አለቃ፡ግን፡ የሆነውን፡ባየ፡ ጊዜ፡ እግዚአብሔርን፡ አመሰገነ፡ እንደህ፡ ሲል። በውነት፡ ይህ፡ ሰው፡ ጻድቅ፡ ኑሮዋል።

፵፰፡ ተከማችተውም፡ የነበሩት፡ ሰዎች፡ ሁሉ፡ ይህነን፡ለማየት፡የሆነውን፡ባዩ፡ጊዜ፡ተመለሱ፡ ደረታቸውን፡ኢየመቱ።

፵፱፡ የሚያውቁትም፡ሁሉ፡ ርቀው፡ ቁመው፡ ነበሩ። *ሴቶችም፡ ከገሊላ፡ ይከተሉት፡ የነበሩ፡ ከርሱ፡ጋራ፡ ይህነንም፡ ያዩ፡ነበሩ። *ምዕ፡ ፰፡ ፪፡፡

፶፡ እነሆም፡ አንድ፡ ሰው፡ ስሙን፡ ዮሴፍ፡ የሚሉት፡ምክር፡የሚያውቅ፡ቸር፡ሰው፡ ጻድቅም።

፶፩፡ ይህም፡ለምክራቸው፡ለስራቸውም፡ የተገበረ፡አልነበረም። አገሩም፡ አሪማቲያ፡ ነበረች፡ የአይሁድ፡አገር። *እርሱም፡ደግሞ፡ የእግዚአብሔርን፡ መንግሥት፡ ተሰፋ፡ ያደርግ፡ ነበር። *ምዕ፡ ፪፡ ፳፭፡—፴፰፡፡

፶፪፡ ይህ፡ወደ፡ ጲላጦስ፡ መጣ፡ የየሱስንም፡ ሥጋ፡ ለመነው።

፶፫፡ አወረደውም፡ በበፍታም ፡ ከፈነው ፡ በተጸረበ፡መቃብርም፡አኖረው፡ ማንም፡ ገና፡ ያልገባበት።

፶፬፡ ዓርብ ፡ ቀንም ፡ ነበር ። የሰንበትም ፡ አጥቢያ፡ ነበር። ዮሐ፡ ፲፱፡ ፴፩፡ ፵፪፡፡

፶፭፡ ደግሞም፡ሴቶች፡ከርሱ፡ጋራ፡ከገሊላ፡የመጡት፡ተከተሉት፡መቃብሩንም፡አዩ፡እንዴትም፡እንደ፡ ተጨመረ፡ ሥጋው። ቍ፡ ፵፱፡፡

፶፮፡ ተመለሱም፡ሽቱና፡ ሰብርም፡ አዘጋጁ። በሰንበትም፡ቀሩ፡ *እንደ፡ሕጉ። *ዘፀአ፡ ፳፡ ፲፡፡

## ምዕራፍ፡ ፳፬፡

፩፡ ከሰንበታቱም፡ በመጀመርያ፡ ቀን፡እጅግ፡ማለደ፡ወደ፡ መቃብር፡ መጡ፡ ያዘገጁትን፡ ሽቱ፡ ተሸክመው።ከርሳቸውም፡ ጋራ፡ ደግሞ፡ ሌሎች። ማቴ፡ ፳፰፡ ፩፡—፰፡፡

፪፡ ደንጊያውንም ፡ አገኙት ፡ ከመቃብር፡ ተፈንቅሎ። ማር፡ ፲፮፡ ፩፡—፰፡፡ ዮሐ፡ ፳፡ ፩፡—፲፡፡

፫፡ ገቡም፡ የየሱስንም፡ የጌታን፡ ሥጋ፡ አላገኙም።

፬፡ እርሳቸውም፡ከዚህ፡ሲያደንቁ።እነሆ፡ሁለት፡ ሰዎች፡ በፊታቸው፡ ቆሙ፡ በሚበርቅ፡ ልብስ።

፭፡ በፈሩም፡ጊዜ፡ ፊታቸውንም፡ወደ፡ ምድር፡ ዝቅ፡ባደረጉ፡ጊዜ፡ አልዋቸው።ለምን፡ ሕያውን፡ ትሻላችሁ፡ ከሙታን፡ ጋራ።

፮፡ እርሱ፡ከዚህ፡የለም፡ነገር፡ግን፡ተነሣ።አስቡ፡እንደ፡ ነገራችሁ ፡እርሱ፡ ገና፡ በገሊላ፡ ሳለ።

፯፡ እንደህ፡ሲል። *የሰው፡ልጅ፡ይገባዋል፡ በኃጥኣን፡እጅ፡ይሰጥ፡ዘንድ፡ይሰቀልም፡ዘንድ።በሦስተኛውም፡ ቀን፡ ይነሣ፡ ዘንድ። *ማቴ፡ ፲፯፡ ፳፪፡፡

፰፡ ነገሩንም፡ አሰቡ።

፱፤ ከመቃብርም፡ተመለሱ፡ ይህንንም፡ ሁሉ፡ ነገር፡ ለአሥራ፡ አንዱ፡ ነገሩ፡ ለቀሩትም፡ ሁሉ።

፲፤ *ማርያም፡መግደላዊትና፡ዮሐናም፡ነበሩ፡ማርያምም፡ የያዕቆብ፡ እናት፡ የቀሩትም፡ ከርሳቸው፡ ጋራ፡የነበሩት፡ ይህነን፡ ለሐዋርያት፡ ያልዋቸው። *ም፡ ፲፮፤ ፩፤ ፫፤፤

፲፩፤ ነገራቸውም፡ እንደ፡ ተረት፡ መሰላቸው፡ አላመንዋቸውምም።

፲፪፤ ጴጥሮስ፡ግን፡ተነሣ፡ወደ፡መቃብርም፡አፈጠነ፡ ዝቅም፡ አለ፡ በፍታውንም፡ ብቻውን፡ ተቀምጦ፡ አየ።ሔደም፡በልቡ፡ኢየተደነቀ፡ ከሆነው፡ የተነሣ።

፲፫፤ እነሆም፡ ሁለት፡ሰዎች፡ ከርሳቸው፡ በዚያ፡ ቀን፡ወደገር፡ይሔዱ፡ነበሩ፡ ከየሩሳሌም፡ስድሳ፡ ምዕራፍ፡ የራቀች። ስምዋን፡ ኤማኡስ፡ የሚልዋት።

፲፬፤ እርሳቸውም፡ ይጫወቱ፡ነበሩ፡እርሱ፡ በርሳቸው፡ስለዚህ፡ስለ፡ ሆነው፡ ነገር፡ ሁሉ።

፲፭፤ እርሳቸውም፡*ሲጫወቱ፡ ሲጠያየቁም፡ የሱስ፡ራሱ፡ወደርሳቸው፡ቀረበ፡ከርሳቸውም፡ጋራ፡ ይሔድ፡ ነበረ። *ማቴ፡ ፲፰፤ ፳፤፤

፲፮፤ ዓይኖቻቸው፡ ግን፡ ተከልክሎ፡ ነበር፡ እንዳያውቁት።

፲፯፤ አላቸውም። ምንድር፡ ነው፡ ይህ፡ ነገር፡ እላንት፡በላንት፡ የምትናገሩት፡ እላንት፡ ስትሔዱ፡ ኢያዘናችሁ።

፲፰፤ ከርሳቸውም፡ አንዱ፡ መለሰ፡ ስሙን፡ ቀለዮጳ፡የሚሉት፡አለውም። አንተን፡ ብቻህ፡እንግዳ፡ነህ፡ በየሩሳሌም። አታውቅምም፡ የነበረባትን፡ በዚህ፡ ወራት።

፲፱፤ አላቸውም፡እርሱ፡ምንድር፡ ነው። እርሳቸውም፡አሉት።የየሱስ፡የናዝሬቱ፡ነገር። *ነቢይ፡ ሰው፡ የነበረው፡ብርቱ፡በማድረግም፡በቃልም፡በእግዚአብሔር፡ ፊት፡ በሕዝቡም፡ ሁሉ። *ማቴ፡ ፳፩፤ ፲፩፤፤ የሐዋ፡ ፪፤ ፳፪፤፤

፳፤ እንደትስ፡ የካህናት፡ ታላላቆች፡ አለቆቻችንም፡ለሞት፡ ፍርድ፡ አሳልፈው፡ ሰጡት፡ ሰቀሉትም።

፳፩፤ እኛ፡ግን፡ተስፋ፡እናደርግ፡ነበር፡እርሱ፡እንደ፡ሆነ፡የሚመጣው፡እሥራኤልን፡*ያድን፡ዘንድ። ነገር፡ ግን፡ከዚህ፡ሁሉ፡ጋራ፡ለርሱ፡ዛሬ፡ ሦስት፡ቀኑ፡ ነው፡ ይህ፡ ከሆነ። *የሐዋ፡ ፩፤ ፮፤፤

፳፪፤ ደግሞም፡ሴቶች፡ከኛ፡አስደነቁነ፡ ወደ፡ መቃብር፡ ማልደው፡ ነበሩና። ቍ፡ ፱፤፤

፳፫፤ ሥጋውንም፡ ባላገኙት፡ ጊዜ፡ እንደህ፡ ሲሉ፡ መጡ፡የመላእክት፡መልክ፡ደግሞም፡እንዳዩ፡ የተናገሩ፡ሕያው፡ እንደ፡ ሆነ።

፳፬፤ ከኛም፡ሰዎች፡ወደ፡መቃብር፡ሔዱ፡እንደሁም፡አገኙ፡ ሴቶች፡ ደግሞ፡ እንደ፡ ተናገሩ። እርሱን፡ ግን፡ አላዩትም።

፳፭፤ እርሱም፡ አላቸው። እላንት፡ ያላስተዋላችሁ፡ ልባችሁም፡ የደነደነ፡ ከማመን፡ ነቢያት፡ በተናገሩበት፡ ሁሉ። ቍ፡ ፵፬፤

፳፮፤ ለክርስቶስ፡ ይገባው፡የለምን፡ ይህነን፡ መከራ፡ ይቀበል፡ ዘንድ፡ ወደ፡ ክብሩም፡ ይገባ፡ዘንድ። ፩፤ ጴጥ፡ ፩፤ ፲፩፤፤ ዕብ፡ ፪፤ ፱፤፤

፳፯፤ ከሙሴም፡ጀመረ፡ከነቢያትም፡ሁሉ፡ ይተረጕምላቸውም፡ነበረ፡ በመጽሐፉ፡ ሁሉ፡ ስለርሱ፡ የተጻፈውን፡ ነገር። ዘዳግ፡ ፲፰፤ ፲፭፤፤ መዝ፡ ፳፪፤፤ ኢሳ፡ ፶፫፤፤

፳፰፤ ይሔዱባትም፡ወደ፡ ነበሩባት፡ አገር፡ ደረሱ። እርሱም፡ወደ፡መራቅ፡ ይሔድ፡ ዘንድ፡ አለ።

፳፱፤ የግድም፡አሉት፡ እንዲህ፡ሲሉ። ከኛ፡ጋራ፡ እደር።መሸተዋልና፡ቀኑም፡ዘነበለ።ከርሳቸውም፡ጋራ፡ ለማደር፡ ገባ። ም፡ ፲፬፤ ፳፫፤፤

፴፤ ከርሳቸውም፡ጋራ፡ በተቀመጠ፡ ጊዜ፡ እንጀራ፡ ያዘ፡ ባረከም፡ ቈረሰም፡ ሰጣቸውም። ም፡ ፳፪፤ ፲፱፤፤ ዮሐ፡ ፳፩፤ ፲፫፤፤

፴፩፤ ዓይኖቻቸውም፡ ተከፈተ፡አወቁትም። እርሱ፡ ግን፡ ከርሳቸው፡ ጠፋ። ቍ፡ ፲፮፤ ፴፭፤፤

፴፪፤ እንዲም፡ባልንጀራውን፡አለው። ልባችን፡ ሲቃጠልብን፡የነበረው፡አይደለምን፡በመንገድ፡ ይነግረነ፡በነበረ፡ጊዜ፡መጽሐፍስ፡ በተረጐመልነ፡ ጊዜ።

፴፫፤ በዚያችም፡ጊዜ፡ተነሡ፡ ወደ፡ የሩሳሌምም፡ ተመለሱ። አሥራ፡አንዱንም፡ ተከማችተው፡አገኙ፡ ከርሳቸውም፡ ጋራ፡ የነበሩትን።

፴፬፤ እንዲህ፡ሲሉ።ጌታ፡በውነት፡ተነሣ፡ለሲሞንም፡ ታየ። ፩፤ ቆሮ፡ ፲፭፤ ፬፤ ፭፤፤

፴፭፤ እርሳቸውም፡ ነገሩ፡በመንገድ፡የሆነውን። እንደ፡ ምንስ፡ አወቁት፡እንጀራ፡ በቈረሰ፡ ጊዜ።

፴፮፤ እርሳቸውም፡ይህነን፡ሲናገሩ፡ እርሱ፡ የሱስ፡ በመካከላቸው፡ ቆመ። አላቸውም። ሰላም፡ ለላንት፡ነው።

፴፯፤ እርሳቸው፡ግን፡ፈሩ፡ደነገጡም፡ *ነፍስም፡ያዩ፡ ይመስላቸው፡ ነበረ። *ማቴ፡ ፲፬፤ ፳፮፤፤

፴፰፤ አላቸውም። ምን፡ ሁናችሁ፡ ትደነግጣላችሁ። ለምንስ፡ አሳብ፡ በልባችሁ፡ ይወጣል፡ይገባል።

፴፱፤ እጆችንና፡እግሬን፡እዩ፡ እኔ፡ነኝና። ይሱኝ። እዩም። ነፍስ፡ሥጋና፡አጥንት፡የለውምና፡እንድታዩ፡ለኔ፡ እንደለኝ።

፵፤ ይህነንም፡ባለ፡ጊዜ፡ እጁንና፡ እግሩን፡ አሳያቸው። መዝ፡ ፳፪፤ ፲፯፤፤

፵፩፤ እርሳቸውም፡ገና፡አላመኑም፡ከደስታ፡ የተነሣ፡ይደነቁም፡ነበሩ። አላቸውም። ከዚህ፡ አንዳች፡ አላችሁን፡ የሚበላ።

፵፪፤ እርሳቸውም፡ከተጠበሰው፡ *ዓሣ፡ የተከፈለ፡ ሰጡት። ከማር፡ ወለላም። *ዮሐ፡ ፳፩፤ ፲፤፤

፵፫፤ ተቀበለም፡ በፊታቸውም፡ በላ። ዘፍ፡ ፲፰፤ ፰፤

፵፬፤ አላቸውም።ይህ፡ነገር፡የነገርኋችሁ፡ነው፡ከላ

ንት፡ጋራ፡ሳለሁ።ይጨረስ፡ ዘንድ፡ እንዲገባ፡ በሙሴ፡
ኦሪት፡በነቢያትም፡በመዝሙርም፡ስለኔ፡የተጻፈው፡
ሁሉ። መዝሙራት። ፲፮፥ ፳፪፥ ፵፥ ፵፩፥ ፷፰፥
፷፱፥ ፸፪፥ ፻፲፥ ፻፲፰።
፵፭፤ የዚያን፡ጊዜ፡አእምሮዋቸውን፡ ገለጸ፡ መጽ
ሐፉን፡ያስተውሉ፡ ዘንድ። የሐዋ፡ ፲፯፥ ፫።
፵፮፤ አላቸውም።እንደሁ፡ተጻፈ፡እንደህም፡ይገ
ባ፡ነበር፡ክርስቶስ፡መከራ፡እንዲቀበል፡ ከሙታንም፡
እንዲነሣ፡ በሶስተኛው፡ ቀን። መዝ፡ ፳፪፥ ፫።
ኢሳ፡ ፶፫፥ ፭።
፵፯፤ በስሙም፡ይሰበክ፡ዘንድ፡ በንስሐ፡ ኃጢአት
ም፡በማስተስረይ፡ በአሕዛብ፡ ሁሉ፡ ከየሩሳሌም፡ ጀ
ምሮ። ኢሳ፡ ፪፥ ፫። ማቴ፡ ፳፬፥ ፲፬። የሐዋ፡ ፪፥ ፴፰።
፵፰፤ እላንትም፡ በዚህ፡ ምስክሮች፡ ናችሁ።
፵፱፤ እኔም፡*እነሆ፡ ያባቴን፡ ተስፋ፡ እልክላችኋለ
ሁ።እላንት፡ግን፡ በየሩሳሌም፡ ከተማ፡ ተቀመጡ፡ ኃ
ይል፡ እስክትለብሱ፡ ድረስ፡ከላይ።
ዮሐ፡ ፲፭፥ ፳፮። ፲፮፥ ፯። የሐዋ፡ ፩፥ ፬።
፶፤ ወደ፡ሜደም፡አወጣቸው፡እስከ፡ ቢታንያ፡ድረ
ስ።እጁንም፡ዘረጋና፡ ባረካቸው። ዘሌዋ፡ ፱፥ ፳፪።
፶፩፤ እርሱም፡ሲባርካቸው፡ከርሳቸው፡ራቀ፡ወደ፡
ሰማይም፡ ወጣ። *የሐዋ፡ ፩፥ ፱፥—፲፫።
፶፪፤ እርሳቸውም፡ሰገዱለት። ወደ፡የሩሳሌም፡ ተ
መለሱ፡ በታላቅ፡ ደስታ።
፶፫፤ ሁልጊዜም ፡ በመቅደስ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ያ
መሰግኑ፡ ይገርኩም፡ ነበረ። አሜን።

ተፈጸመ ፡ የሉቃስ ፡ ወንጌል።

---

# የ ዮ ሐ ን ስ ፡ ወ ን ጌ ል ።



---

# የጌታችን ፡ የየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ቅዱስ ፡ ወንጌል ፡ እንደ ፡ ጻፈው፡ ቅዱስ ፡ ዮሐንስ ።

## ምዕራፍ፡ ፩፡

፩፡ አስቀድሞ፡ *ቃል፡ነበረ።ቃልም፡በእግዚአብሔር፡ ዘንድ፡ ነበረ። እግዚአብሔርም፡ ቃል፡ ነበረ። *ም፡ ፲፯፡ ፭። ዘፍጥ፡ ፩፡ ፩—፫። ፩፡ ዮሐ፡ ፩፡ ፩፡ ፪።

፪፡ ይህ ፡ አስቀድሞ ፡ *በእግዚአብሔር ፡ ዘንድ፡ ነበረ። *ምሳ፡ ፰፡ ፳፪።

፫፡ ሁሉ፡ በርሱ፡ሆነ፡ *ያለርሱም፡ አልሆነም፡ ምንም፡ ከሆነው፡ ሁሉ። መዝ፡ ፴፫፡ ፮። ቆላ፡ ፩፡ ፲፮። ዕብ፡ ፩፡ ፪። ፲፩፡ ፫።

፬፡ ሕይወት፡*በርሱ፡ነበረች።ሕይወትም፡*የሰው፡ ብርሃን፡ ነበረች። *ም፡ ፭፡ ፳፮። ፲፩፡ ፳፭። ም፡ ፰፡ ፲፪።

፭፡ ብርሃንም፡ በጨለማ፡ *ያበራል። ጨለማም፡አላገኘውም። *መዝ፡ ፴፮፡ ፲። ም፡ ፫፡ ፲፱። ፱፡ ፭።

፮፡ ሰው፡ነበረ፡ከእግዚአብሔር፡የተላከ፡ስሙም፡ ዮሐንስ። ም፡ ፫፡ ፲፡ ፳፮፡ ፴፩።

፯፡ ይህ፡ ለምስክር፡ መጣ፡ ለብርሃን፡ *ሊመሰክር፡ ሁሉ፡ በርሱ፡ ያምን፡ ዘንድ። *ም፡ ፭፡ ፴፫።

፰፡ እርሱ፡ብርሃን፡አልነበረም፡ነገር፡ግን፡ተላከ፡ *ለብርሃን፡ ሊመሰክር። *ም፡ ፫፡ ፳፰።

፱፡ እውነተኛ፡ብርሃን፡ነበረ፡ለሰው፡ ሁሉ፡የሚያበራ፡ወደ፡ ዓለም፡ ለሚመጣው። ም፡ ፲፪፡ ፵፮። ኢሳ፡ ፰፡ ፩።

፲፡ በዓለም፡ነበረ፡ዓለሙም፡በርሱ፡ሆነ፡ዓለምም፡ አላወቀውም።

፲፩፡ ወደ፡ወገኖቹ፡መጣ፡ወገኖቹም፡አልተቀበሉትም*። *ዘፀ፡ ፲፱፡ ፭። መዝ፡ ፳፱፡ ፱።

፲፪፡ ለተቀበሉት ፡ ሁሉ ፡ ግን፡ ሥልጣን፡ ሰጣቸው፡ የእግዚአብሔር፡ልጆች፡ይሆኑ፡ዘንድ፡በስሙ፡የሚያምኑ*። *ሆሴ፡ ፩፡ ፲። ፩፡ዮሐ፡ ፫፡ ፩።

፲፫፡ ከደም፡ወገን፡ያይደሉ፡ከሥጋ፡ ፈቃድም፡ ከሰውም፡ መውደድ ፡ ነገር ፡ ግን፡ ከእግዚአብሔር፡ ተወለዱ*። *ም፡ ፫፡ ፫። ፩፡ ዮሐ፡ ፫፡ ፱። ያዕ፡ ፩፡ ፲፰።

፲፬፡ ቃልም፡ሥጋ፡ሆነ፡ *በኛም፡አደረ። ክብሩንም፡ አየነ፡አንድ፡እንደ፡ መሆኑ፡ ክብር፡ከአብ፡†ጸጋ፡እውነትም፡ **የመላበት። *ኢሳ፡ ፯፡ ፲፬። ፱፡ ፮። ፩፡ ጢሞ፡ ፫፡ ፲፮። ኢሳ፡ ፶፯፡ ፲፭። ም፡ ፪፡ ፲፩። †ቍ፡ ፲፰። ** መዝ፡ ፹፱፡ ፪፡ ፫፡ ፲፭፡ ፳፮።

፲፭፡ ዮሐንስ፡ *ስለርሱ፡ መሰከረ፡ ጮኸም፡ እንዲህ፡ሲል። ይህ፡ ነው፡ ያልሁት። ከኔ፡ በኋላ፡ የሚመጣው፡እርሱ፡በፊቴ፡ ሆነ። ከኔ፡በፊት፡ ነበርና። *ማቴ፡ ፫፡ ፲፩።

፲፮፡ ከሙላቱም፡እኛ፡ሁላችን፡ወሰድነ፡ጸጋም፡በጸጋ፡ፈንታ። ም፡ ፫፡ ፴፬። ቆላ፡ ፩፡ ፲፱። ሮሜ፡ ፩፡ ፲፯።

፲፯፡ ኦሪት፡ *በሙሴ፡ተሰጥዋልና፡ ጸጋ፡ ግን፡ እውነትም፡ በየሱስ፡ ክርስቶስ፡ ሆነ። *ዘፀ፡ ፳፡ ፩። ሮሜ፡ ፲፡ ፬። ፲፭፡ ፰፡ ፱።

፲፰፡ እግዚአብሔርን፡ከቶ፡*ያየው፡የለም።አንድ፡ ልጁ፡ ባባቱ፡ ጭን፡ ያለ፡እርሱ፡ ተናገረበት። *፩፡ ዮሐ፡ ፬፡ ፲፪። ማቴ፡ ፲፩፡ ፳፯።

፲፱፡ ይህ፡ነው፡የዮሐንስ፡ምስክር፡አይሁድ፡ ከየሩሳሌም፡ ካህናትን፡ ሌዋውያንንም፡ በላኩበት፡ጊዜ፡ ይጠይቁት፡ ዘንድ። አንተ፡ ማነህ። ም፡ ፭፡ ፴፫።

፳፡ እውነትም፡ተናገረ፡አልካደምም፡በነገሩም፡ጸና፡ እኔ፡ ክርስቶስ፡ አይደለሁም ፡ ብሎ።

፳፩፡ ጠየቁትም። እንኪያስ፡ማነህ። ኤልያስን፡*ነህ።አለም።አይደለሁም። አንተ፡ †ነቢይን፡ነህ። መለሰም፡የለም። *ማቴ፡ ፲፯፡ ፲—፲፪። †ዘዳግ፡ ፲፰፡ ፲፭።

፳፪፡ አሉትም፡እንኪያስ፡ ማነህ፡አንተ። ለላኩን፡ ምላሽ፡እንመልስ፡ዘንድ። ምን፡ትላለህ፡ ስለ፡ ራስህ።

፳፫፡ አለም። እኔ፡ *አዋጅ፡ነጋሪ፡ነኝ፡በምድረ፡በዳ፡ የሚጮህ። የእግዚአብሔርን፡መንገድ፡አቅኑ። ነቢዩ፡ ኢሳይያስ፡ እንደ፡ ተናገረ። *ኢሳ፡ ፵፡ ፫።

፳፬፡ የተላኩትም፡ ከፈሪሳውያን፡ ነበሩ። ማር፡ ፯፡ ፫።

፳፭፡ ጠየቁትም፡አሉትም። እንኪያ፡ለምን፡ታጠምቃለህ፡ ክርስቶስ፡ ያይደለህ፡ ከሆንህ፡ ኤልያስም፡ ነቢዩም።

፳፮፡ ዮሐንስም፡ መለሰላቸው፡ እንዲህ፡ ሲል። እኔ፡በውኃ፡አጠምቃለሁ።በመካከላችሁ፡ግን፡ ቁሞዋል፡ የማታውቁት። ማቴ፡ ፫፡ ፲፩።

፳፯፡ ይህ፡እርሱ፡ነው፡በኋላዬ፡የሚመጣው። እርሱም፡በፊቴ፡ሆነ።እኔ፡የማይገባኝ፡ የጫማውን፡ሲር፡ እፈታ፡ ዘንድ። ም፡ ፫፡ ፳፮። መልክ፡ ፬፡ ፩።

፳፰፡ ይህ፡ሁሉ፡ሆነ፡በቤታበራ፡ በዮርዳኖስ፡ ማዶ፡ ዮሐንስ፡ ያጠምቅበት፡ ወደ፡ ነበረው። ም፡ ፲፡ ፵።

፳፱፡ በነገውም፡ዮሐንስ፡የሱስን፡አየ፡ ወደርሱ፡ሲመጣ፡አለም። እነሆ፡ የእግዚአብሔር፡ በግ፡ የዓለምን፡ኃጢአት፡ የሚያስወግድ*። *ኢሳ፡ ፶፫፡ ፯። ፩፡ ዮሐ፡ ፪፡ ፪።

፴፡ ይህ፡ነው፡እኔ፡ ስለርሱ፡ ያልሁት። ሰው፡ እንዲመጣ፡ በኋላዬ፡ እርሱም፡ በፊቴ፡ ነበር። ቍ፡ ፲፭።

፴፩፡ እኔም፡የማውቀው፡አልነበርሁም።ነገር፡ግን፡ ለእሥራኤል፡ሊገለጥ፡ስለዚህ፡እኔ፡መጣሁ፡ በውኃ፡ ሳጠምቅ።

፴፪፡ ዮሐንስም፡መሰከረ፡እንዲህ፡ ሲል። እኔ፡ መንፈስ፡ አየሁ፡ ከሰማይ፡ ሲወርድ፡ እንደ፡ ርግብ፡ ሲቀመጥበትም። ማቴ፡ ፫፡ ፲፮።

፴፫፡ እኔም፡የማውቀው፡አልነበርሁም፡ነገር፡ግን፡ የላከኝ፡በውኃ፡አጠምቅ፡ ዘንድ፡እርሱ፡ አለኝ። የምታየው፡ መንፈስ፡ ወርዶ፡ ሲቀመጥበት፡ እርሱ፡ነው፡ በመንፈስ፡ *ቅዱስ፡ የሚያጠምቅ።

*ኢዮ፡ ፫፡ ፩። የሐዋ፡ ፩፡ ፭።

፴፬፡ እኔም፡አየሁ፡ መሰከርሁም፡ ይህ፡ የእግዚአብሔር፡ልጅ፡እንደ፡ ሆነ።

፴፭፡ በነገውም፡ደግሞ፡ ዮሐንስ፡ቁሞ፡ ነበር፡ ሁለትም፡ ከደቀ፡ መዛሙርቱ። ቍ፡ ፵።

፴፮፡ የሱስንም፡ሲያልፍ፡ተመለከተው፡ አለም። እነሆ፡ የእግዚአብሔር፡ *በግ። *ቍ፡ ፳፱።

፴፯፡ ሁለቱም፡ደቀ፡መዛሙርት፡ነገሩን፡ ሰሙ፡ የሱስንም፡ ተከተሉት።

፴፰፡ የሱስም፡ ተመልሶ፡ ሲከተሉትም፡ አይቶ፡ አላቸው።

፴፱፡ ምን፡ትሻላችሁ። እርሳቸውም፡አሉት።ረቢ፡ (ትርጓሜውም፡መምህር፡ሆይ)። ወዴት፡ትኖራለህ።

፵፡ አላቸው።ኑና፡እዩ። መጡም፡ አዩም፡ ወዴት፡ እንዲኖር።ያነንም፡ቀን፡በርሱ፡ ዘንድ፡ ተቀመጡ። አሥር፡ሰዓትም፡ያህል፡ነበረ። ቍ፡ ፵፯። ራእ፡ ፯፡ ፩።

፵፩፡ አንዲም፡ከሁለቱ፡ከዮሐንስ፡ ሰምተው፡ ከተከተሉት፡እንድርያስ፡ ነበረ፡ የሲሞን፡ ጴጥሮስ፡ *ወንድም። *ማቴ፡ ፬፡ ፲፰።

፵፪፡ ይህ፡በመጀመርያ፡ሲሞንን፡ወንድሙን፡አገኘ፡ አለውም። መሢሐን፡አገኘነ፡(ትርጓሜውም፡ቅቡእ፡ነው)። መዝ፡ ፪፡ ፪። ዳን፡ ፱፡ ፳፭፡ ፳፮።

፵፫፡ ወደ፡ የሱስም፡ ይዞት፡ መጣ። የሱስም፡ ባየው፡ጊዜ፡አለ።አንተ፡ሲሞን፡ ነህ፡ የዮና፡ ልጅ፡ አንተ፡ ኬፋ፡ ትባላለህ፡ (ትርጓሜውም፡ ሕንፃ)።

ማቴ፡ ፲፮፡ ፲፰።

፵፬፡ በነገውም፡ እኻ፡ የሱስ፡ ወደ፡ ገሊላ፡ መውጣት፡ ፊልጶስንም፡ አገኘ፡ አለውም። ተከተለኝ።

፵፭፡ ፊልጶስም፡ ከቤተ፡ ሰይዳ፡ ነበር፡ ከእንድርያስና፡ ከጴጥሮስ፡ አገር። ም፡ ፲፪፡ ፳፩።

፵፮፡ ፊልጶስ፡ ናትናኤልን፡ አገኘው፡ አለውም። ሙሴ፡በኦሪት፡ስለርሱ፡የጻፈለቱን፡ነቢያትም፡ አገኘነው። እርሱም፡ የሱስ፡ የዮሴፍ፡ ልጅ፡የናዝሬቱ።

ዘዳግ፡ ፲፰፡ ፲፰። ኢሳ፡ ፯፡ ፲፬። ፶፫፡ ፪።
ኤር፡ ፳፫፡ ፭። ሕዝ፡ ፴፬፡ ፳፫።

፵፯፡ ናትናኤልም፡አለው።ከናዝሬቱ፡መልካም፡ ነገር፡ይወጣ፡ዘንድ፡ይቻላልን።ፊልጶስ፡አለው። መጥተህ፡እይ። ም፡ ፯፡ ፵፩፡ ፵፪።

፵፰፡ የሱስ፡ናትናኤልን፡አየ፡ወደርሱ፡ ሲመጣ፡ ስለርሱም፡አለ።እነሆ፡የእሥራኤል፡ወገን፡ሰው፡በውነት፡ተንኰል፡የሌለበት።

፵፱፡ ናትናኤልም፡ አለው። ከወዴት፡ ታውቀኛለህ።መለሰ፡የሱስ፡አለውም።ፊልጶስ፡ ሳይጠራህ፡ አንተም፡በበለስ፡ታች፡ሳለህ፡አየሁህ። ም፡ ፬፡ ፲፯፡ ፳፱።

፶፡ ናትናኤል፡መለሰ፡አለም። ረቢ፡ አንተ፡ ነህ፡ የእግዚአብሔር፡ ልጅ።አንተ፡ነህ፡ የእሥራኤል፡ ንጉሥ። ም፡ ፮፡ ፲፮። መዝ፡ ፪፡ ፯። ማቴ፡ ፲፬፡ ፴፫። ፲፮፡ ፲፮።

፶፩፡ የሱስም፡መለሰ፡ አለውም። እኔ፡ በበለስ፡ ታች፡አየሁህ፡ስላልሁህን፡አመንህ። ከዚህ፡የበለጠ፡ ታያለህ። ም፡ ፳፡ ፳፱።

፶፪፡ አለውም።እውነት፡እላችኋለሁ፡ ከዚህ፡ በኋላ፡ ሰማዮች፡ ተከፍተው፡ *እንድታዩ፡ የእግዚአብሔርም፡ †መላእክት፡ በሰው፡ ልጅ፡ላይ፡ሲወጡና፡ ሲወርዱ። *ም፡ ፫፡ ፲፫። ማቴ፡ ፫፡ ፲፮። †ዘፍ፡ ፳፰፡ ፲፪።

## ምዕራፍ፡ ፪፡

፩፡ በሦስተኛውም፡ቀን፡ሰርግ፡ነበረ፡በቃና፡በገሊላ፡ የየሱስም፡ እናት፡ ከዚያ፡ ነበረች።

፪፡ የሱስም፡ ደቀ፡ መዛሙርቱም፡ ተጸሩ፡ ወደ፡ ሰርግ።

፫፡ ጸጁ፡ም፡ባለቀ፡ጊዜ፡የየሱስ፡እናት፡አለችው።ጸጅ፡የላቸውም።

፬፡ የሱስም፡አላት።ካንች፡ጋራ፡ምን፡አለኝ፡አንች፡ *ሴት። †ጊዜዬ፡ ገና፡አልደረሰም። *ም፡ ፲፱፡ ፳፮።
†ም፡ ፯፡ ፮፡ ፴።

፭፡ እናቱም፡ ላገልጋዮች፡ አለች። የሚላችሁን፡ ሁሉ፡አድርጉ።

፮፡ ከዚያም፡ ስድስት፡ የድንጊያ፡ ጋኖች፡ ተቀምጠው፡ነበሩ፡*አይሁድ፡ እንዲያነጹ፡ መጠን። ከርሳቸውም፡ ኢያንዳንዱ፡ ሁለት፡ ማድጋ፡ ወይም፡ ሦስት፡ ያነሣ፡ነበር። *ማር፡ ፯፡ ፫። ዝኍል፡ ፴፩፡ ፳፫።

፯፡ የሱስም፡ አላቸው፡ጋኖችን፡ውኃ፡ሙልዋቸው። እስከ፡ላይ፡ድረስም፡መልዋቸው።

፰፡ አላቸውም። ቅድዋቸው፡ እንጊዲህ፡ ለመርፈቂያው፡ አለቃም፡ ስጡት። አደረሱም።

፱፡ የምርፋቁም፡አለቃ፡ያነን፡ውኃ፡በቀመሰ፡ጊዜ፡ ጸጅ፡ሁኖ፡የተለወጠውን።ከወዴትም፡እንደ፡መጣ፡ አላወቀም፡አገልጋዮች፡ግን፡ ውኃ፡ የመሉት፡ ያውቁ፡ ነበር። የምርፋቁ፡ አለቃ፡ ሙሽራውን፡ ጸራ።

፲፡ አለውም።ሰው፡ሁሉ፡አሰቀድሞ፡መልካም፡ጸጅ፡ያመጣል፡*በሰከሩም፡ጊዜ፡ከዚያ፡ ወዲያ፡ የተዋረደውን።አንተ፡ግን፡መልካሙን፡ ጸጅ፡እስካሁን፡ጠበቅህ። *መዝ፡ ፴፮፡ ፱። ሐጌ፡ ፩፡ ፮።

፲፩፡ ይህች፡ ናት፡የተአምራት፡ መጀመርያ፡ የሱስ፡ በቃና፡ገሊላ፡ያደረጋት። *ክብሩንም፡ገለጠ፡ደቀ፡መዛሙርቱም፡ †አመኑበት።

*ም፡ ፩፡ ፲፬። †ም፡ ፩፡ ፵፩—፵፱።

፲፪፡ ከዚህ፡በኋላ፡ ወደ፡ ቅፍርናሆም፡ ወረደ፡ እርሱ፡እናቱም፡ ወንድሞቹም፡ደቀ፡ መዛሙርቱም። ከዚያም፡ ተቀመጡ፡ ጥቂት፡ ቀን፡ ብዙም፡ አይደለም። ም፡ ፯፡ ፫።

፲፫፣ የአይሁድም፡ *ፋሲካ፡ ቀርቦ፡ነበረ፡ የሱስም፡
ወደ፡የሩሳሌም፡ ወጣ። *ዘፀ፡ ፴፬፣ ፳፫፡፡
፲፬፣ በመቅደስም፡ላም፡የሚሸጡ፡ አገኘ፡ በግም፡
ርግብም፡ ለዋጮችም፡ ተቀምጠው።
ማቴ፡ ፳፩፣ ፲፪፣—፲፮፡፡ ማር፡ ፲፩፣ ፲፭፣—፲፯፡፡
ሉቃ፡ ፲፱፣ ፵፭፣ ፵፮፡፡
፲፭፣ የገመድም፡አለንጋ፡አደረገ፡ሁሉንም፡ከመቅ
ደስ፡አወጣ፡ላሙንም፡ በጉንም። የለዋጮችንም፡ ወ
ርቅ፡ በተነ፡ ሰደቃቸውንም፡ ገለበጠ።
፲፮፣ ርግብ፡ሻጮችንም፡ አላቸው። ይህነን፡ ከዚህ፡
አንሡ።ያባቴን፡ቤት፡የመሸጥ፡ የመለወጥ፡ቤት፡አታ
ድርጉ። ሉቃ፡ ፪፣ ፵፱፡፡
፲፯፣ ደቀ፡መዛሙርቱም፡ አሰቡ፡ ተጽፏ፡ እንደ ለ።
የቤትህ፡ ቅናት፡ በላችኝ። መዝ፡ ፷፱፣ ፲፡፡
፲፰፣ አይሁድም፡ መለሱ፡ አሉትም። ምን፡ *ምል
ክት፡ ታሳየናለህ፡ ይህነን፡ ትሰራ፡ ዘንድ።
*ማቴ፡ ፲፪፣ ፴፰፣
፲፱፣ የሱስም፡ መለሰ፡ አላቸውም። ይህነን፡ *መቅ
ደስ፡ አፍርሱት፡ እኔም፡ በሦስት፡ ቀን፡ አስነሣዋለሁ።
*ማቴ፡ ፳፮፣ ፷፩፡፡
፳፣ አይሁድም፡አሉት።ባርባ፡ ስድስት፡ አመት፡ ተ
ሰራ፡ ይህ፡ መቅደስ ። አንተን፡ በሦስት ፡ ቀን፡ ታነሣዋ
ለህ።
፳፩፣ እርሱ፡ ግን፡ አለ፡ ስለ፡ ሥጋው፡ መቅደስ።
ማቴ፡ ፳፯፣ ፵፡፡ ቆላ፡ ፪፣ ፱፡፡ ዕብ፡ ፲፣ ፳፡፡
፳፪፣ ከሙታንም፡በተነሣ፡ጊዜ፡ ደቀ፡መዛሙርቱ፡
አሰቡ፡ ይህነን፡ ይላቸው፡ እንደ ፡ ነበረ ። *በመጽሐፍ
ም፡አመኑ፡ በነገርም፡ የሱስ፡ ይናገራት፡ በነበረው።
*መዝ፡ ፲፮፣ ፲፡፡
፳፫፣ በየሩሳሌምም፡ሳለ፡ በፋሲካ፡ በበዓሉ፡ ቀን፡
ብዙ፡ሰዎች፡በስሙ፡አመኑ፡ የሚያደርጋትን፡ ተአም
ራት፡ ባዩ፡ጊዜ።
፳፬፣ የሱስ፡ ግን፡ አያምናቸውም፡ ነበረ፡ ሁሉን፡ያ
ውቅ፡ነበርና። ም፡ ፰፣ ፩፣ ፪፡፡
፳፭፣ አይሻምም፡ነበረ፡ማንም፡በሰው፡ይመሰክር
ለት፡ዘንድ። እርሱ፡በሰው፡ ያለውን፡ ያውቅ፡ ነበርና።
ማር፡ ፪፣ ፰፡፡ ፩፣ ሳሙ፡ ፲፮፣ ፯፡፡ ምሳ፡ ፳፬፣ ፲፪፣

## ምዕራፍ፡ ፫፣

፩፣ ከፈሪሳውያን፡አንድ፡ሰው፡ነበረ፡ ስሙም፡ ኒቆ
ዲሞስ፡የአይሁድ፡ አለቃ። ም፡ ፯፣ ፶፡፡ ፲፱፣ ፴፱፡፡
፪፣ ይህ፡ወደ፡የሱስ፡መጣ፡በሌት፡አለውም። ረቢ፡
አኛ፡አናውቃለን፡ከእግዚአብሔር፡ዘንድ፡ እንደ፡ መ
ጣህ፡መምህር፡ ሁነህ። አንድም፡ የሚችል፡ የለምና፡
ተአምራት፡ያደርግ፡ዘንድ፡አንተ፡የምታደርጋትን፡ እ
ግዚአብሔር፡ ከርሱ፡ ጋራ፡ ካለ፡በቀር።
ም፡ ፱፣ ፴፫፡፡ የሐዋ፡ ፲፣ ፴፰፡፡
፫፣ የሱስም፡ መለሰ፡ አለውም ። እውነት፡ እልሃለ
ሁ። ማንም፡ከላይ፡ ካልተወለደ ፡ የእግዚአብሔርን፡
መንግሥት፡ያይ፡ ዘንድ፡ አይችልም።
፩፣ ጴጥ፡ ፩፡ ፳፫፡፡
፬፣ ኒቆዲሞስም፡አለው።እንዴት፡ይችላል፡ሰው፡
ይወለድ፡ዘንድ፡እርሱም፡ሸማግሌ። ወደናቱ፡ማሕፀ
ን፡ ተመልሶ፡ ሁለተኛ፡ ይወለድ፡ ዘንድ፡ ይችላልን።
፭፣ የሱስም፡መለሰ፡እውነት፡እውነት፡እልሃለሁ።
ማንም፡*ከውኃና፡ከመንፈስ፡ካልተወለደ፡ወደ፡እግ
ዚአብሔር ፡ መንግሥት ፡ ይገባ ፡ ዘንድ ፡ አይችልም።
*ሕዝ፡ ፴፮፣ ፳፭፣ ፳፯፡፡ ኤፌ፡ ፭፣ ፳፮፡፡ ቲቶ፡ ፫፣ ፭፡፡
፮፣ *ከሥጋ፡ የተወለደው ፡ ሥጋ፡ ነው ። ከመንፈስ
ም፡ የተወለደ፡ መንፈስ፡ ነው። *ዘፍ፡ ፭፣ ፫፡፡
መዝ፡ ፶፩፣ ፭፡፡
፯፣ አታድንቅ፡ስላልሁህ።ይገባችኋል፡ ትወለዱ፡ ዘ
ንድ፡ከላይ።
፰፣ ነፋስ፡ወደ፡ወደደችው፡ ትነፍሳለች፡ ድምጽዋ
ንም፡ትሰማለህ፡ነገር፡ ግን፡ አታውቅም፡ ከወዴት፡ ት
መጣለች ፡ ወዴት ፡ ዘንድስ ፡ ትሔዳለች ። እንደሁ፡
ነው፡ከመንፈስ፡የሚወለድ፡ሁሉ። መዝ፡ ፻፴፭፣ ፯፡፡
፱፣ ኒቆዲሞስ፡መለሰ፡አለውም። እንዴት፡ ይቻላ
ል፡ ይህ፡ ይሆን፡ ዘንድ።
፲፣ የሱስም፡መለሰ፡አለውም። አንተ፡ የእሥራኤ
ል፡መምህር፡ ይህነን፡ አታውቅምን።
፲፩፣ እውነት፡እውነት፡ እልሃለሁ። በምናውቀው፡
እንድንናገር፡ባየነውም፡እንመሰክራለን፡ ምስክራች
ንንም፡ አትቀበሉም። ም፡ ፯፣ ፲፮፡፡ ፰፣ ፳፮፡ ፳፰፡፡
፲፪፣ የምድሩን ፡ ብነግራችሁ፡ ካላመናችሁ ፡ እንዴ
ት፡የሰማዩን፡ብነግራችሁ፡ ታምናላችሁ።
፲፫፣ ማንም፡ ወደ፡ ሰማይ፡ የወጣ፡ የለም፡ ከሰማ
ይ፡ከወረደው፡በቀር። እርሱም፡ የሰው፡ ልጅ፡ በሰማ
ይ፡ የሚኖር። ም፡ ፩፣ ፶፩፡፡ ኤፌ፡ ፬፣ ፱፡፡
፲፬፣ ሙሴም፡እባብ፡እንደ፡ ሰቀለ፡ በምድረ፡ በዳ፡
እንደሁ፡ ይገባዋል፡ የሰው፡ ልጅ፡ ይሰቀል፡ ዘንድ።
ዘኍል፡ ፳፩፣ ፱፡፡
፲፭፣ በርሱ፡የሚያምን፡ሁሉ፡ እንዳይጠፋ፡የዘላለ
ም፡ ሕይወት፡ ትሆንለት፡ ዘንድ፡ እንጂ።
ም፡ ፳፣ ፴፩፡፡
፲፮፣ እግዚአብሔር፡ እንደሁ ፡ ዓለሙን፡ ወድዋል
ና፡አንድ፡ልጁን፡ እስኪለውጥ፡ ድረስ። በርሱ፡ ያመነ፡
ሁሉ፡ እንዳይጠፋ፡ የዘላለም፡ ሕይወት ፡ ትሆንለት፡
ዘንድ፡ እንጂ። ሮሜ፡ ፭፣ ፰፡፡ ፰፣ ፴፪፡፡
፩፣ ዮሐ፡ ፬፣ ፱፡፡
፲፯፣ እግዚአብሔር፡ልጁን፡ ወደ፡ዓለም፡ አላከም
ና፡ ዓለምን፡ ሊኰንን፡ ነገር፡ ግን፡ ዓለም ፡ ይድንበት፡
ዘንድ። ም፡ ፱፣ ፴፱፡፡ ሉቃ፡ ፱፣ ፶፮፡፡
፲፰፣ በርሱ፡ ያመነ፡ *አይኰነንም ። የማያምንበት
ም፡ አሁን፡ የተኰነነ፡ነው። †ባንድ፡በእግዚአብሔር፡
ልጅ፡ ስም፡ አላመነምና። *ም፡ ፮፣ ፵፡፡
†ም፡ ፭፣ ፳፬፡፡ ሮሜ፡ ፰፣ ፩፡፡

፲፱፤ ኵነኔ፡ቱም፡ ይህች፡ ናት።ብርሃን፡ ወደ፡ ዓለ
ም፡ መጥትዋልና፡ ሰዎችም፡ ጨለማ፡ ከብርሃን፡ ይል
ቅ፡ ወደዱ፡ ስራቸው፡ ክፉ፡ ናትና። ም፡ ፩፤ ፭፤ ፱።
ሮሜ፡ ፲፫፤ ፲፪።

፳፤ ክፉ፡የሚያደርግ፡ሁሉ፡ብርሃንን፡ይጠላልና፡ወ
ደ፡ ብርሃንም፡ አይቀርብም፡ ስራው፡ እንዳይዘለፍ።
ኤፌ፡ ፭፤ ፲፫።

፳፩፤ እውነት፡ግን፡የሚያደርግ፡ወደ፡ብርሃን፡ይመ
ጣል፡ ስራው፡ ትገለጥ፡ዘንድ፡ በእግዚአብሔር፡ የተደ
ረገች፡ ናትና። ኤፌ፡ ፭፤ ፲፫፤ ፱።

፳፪፤ ከዚህ፡በኋላ፡ ሔደ፡ የሱስ፡ ደቀ፡መዛሙርቱ
ም፡ወደ፡ ይሁዳ፡ ምድር። ከዚያም፡ ከርሳቸው፡ ጋራ፡
ይመላለስ፡ ያጠምቅም፡ ነበር። ም፡ ፬፤ ፩፤ ፪።

፳፫፤ ዮሐንስም፡ደግሞ፡ ያጠምቅ፡ ነበረ፡ በሄኖን፡
አርሰዋም፡ ለሳሌም፡የቀረበች። ከዚያ፡ እጅግ፡ ው
ኃ፡ ነበረና። ይመጡም፡ ይጠመቁም፡ ነበሩ።
ም፡ ፩፤ ፳፰።

፳፬፤ ዮሐንስ፡ ገና፡ በግዞት፡ አልተጨመረም፡ ነበ
ርና። ማቴ፡ ፲፬፤ ፫።

፳፭፤ ክርክርም፡ነበረ፡በዮሐንስ፡ደቀ፡መዛሙርት
ና፡ በአይሁድ፡ መካከል፡ ስለ፡ ማንጻት።
ዘኍል፡ ፴፩፤ ፳፫።

፳፮፤ ወደ፡ዮሐንስም፡መጡ፡አሉትም።ረቢ፡ያ፡ካ
ንተ፡ጋራ፡ የነበረው፡ በዮርዳኖስ፡ ማዶ፡አንተ፡ *የመሰ
ከርህለት፡ እነሆ፡ እርሱ፡ ያጠምቃል፡ ሁሉም፡ ወደር
ሱ፡ ይመጣሉ። *ም፡ ፩፤ ፳፯፤—፴፬።

፳፯፤ ዮሐንስም፡ መለሰ፡ አለም። ሰው፡ አንዳች፡
ይወስድ፡ዘንድ፡አይችልም፡ከሰማይ፡ካልተሰጠው።
ም፡ ፲፱፤ ፲፩። ዕብ፡ ፭፤ ፬።

፳፰፤ እላንትም፡ ትመሰክሩላችሁ፡ እኔ፡ እንደል
ሁ። እኔ፡ ክርስቶስ፡ አይደለሁም። በፊቱ፡ ተልኪያለ
ሁ፡ እንጂ። ም፡ ፩፤ ፳፤ ፴።

፳፱፤ ሙሽራ፡ያለችው፡እርሱ፡ሙሽራ፡ነው። የሙ
ሽራውም፡ ወደጅ፡ የቀመው፡ እርሱንም፡ የሚሰማ
ው፡ደስ፡ይለዋል፡ስለ፡ሙሽራው፡ቃል። እንግዴህ፡ ይ
ህ፡ ደስታዬ፡ የተፈጸመ፡ ነው። ማቴ፡ ፳፪፤ ፪።

፴፤ ለዚያ፡ይገባዋል፡ያድግ፡ዘንድ፡ ለኔ፡ ግን፡አንስ፡
ዘንድ።

፴፩፤ ከላይ፡የመጣ፡እርሱ፡ከሁሉ፡ በላይ፡ ነው። ከ
ምድር፡ የሚሆን፡ እርሱ፡ ምድራዊ፡ ነው፡ የምድሩን
ም፡ ይናገራል። ከሰማይ፡ የመጣ፡ እርሱ፡ ከሁሉ፡ በላ
ይ፡ ነው። ም፡ ፰፤ ፳፫።

፴፪፤ ባየውም፡በሰማውም፡ ይመሰክራል፡ምስክ
ሩንም፡ ማንም፡ አይቀበላትም።
ቍ፡ ፲፩፤ ም፡ ፭፤ ፲፱፤ ፴፩።

፴፫፤ ምስክሩን፡ የተቀበለ፡ አተመ፡ እግዚአብሔ
ር፡ እውነተኛ፡ እንደሆነ። ሮሜ፡ ፫፤ ፬።

፴፬፤ እግዚአብሔር፡የላከው፡የእግዚአብሔርን፡
ነገር፡ይናገራልና።እግዚአብሔር፡ መንፈስን፡ሰፍሮ፡አ
ይሰጥምና። ም፡ ፩፤ ፴፫፤ ፴፬።

፴፭፤ አባት፡ልጅን፡ ይወዳል፡ ሁሉንም፡ በጁ፡ ሰጠ
ው። ማቴ፡ ፲፩፤ ፳፯። ፳፰፤ ፲፰።

፴፮፤ በልጅ፡ ያመነ፡ የዘላለም፡ ሕይወት፡ አለው።
ልጅንም፡የማይሰማ፡ሕይወትን፡ አያይም። የእግዚ
አብሔር፡ ቍጣ፡ በላዩ፡ ይኖራል፡ እንጂ።
ቍ፡ ፲፮፤ ፲፰። ኤፌ፡ ፪፤ ፫። ራእ፡ ፲፬፤ ፲፤ ፲፩፤

## ምዕራፍ፡ ፬፤

፩፤ ጌታም፡ባወቀ፡ጊዜ፡ፈሪሳውያን፡ እንደ፡ ሰሙ፡
የሱስ፡እጅግ፡ደቀ፡ መዛሙርት፡ እንዳደረገ፡ ከዮሐን
ስም፡ይልቅ፡ እንዲያጠምቅ። ም፡ ፫፤ ፳፪፤ ፳፮።

፪፤ (የሱስም፡ ራሱ፡ ስላጠመቀ፡ አይደለም፡ ደቀ፡
መዛሙርቱ፡እንጂ)።

፫፤ የይሁዳን፡ አገር፡ ተወ፡ ደግሞም፡ ወደ፡ ገሊላ፡
ሔደ።

፬፤ በሰማርያም፡አኩል፡ያልፍ፡ ዘንድ፡ይገባው፡ነበ
ር፡ወደ፡ሰማርያም፡ አገር፡ ሲካር፡ ወደሚልዋት፡ ደረ
ሰ። ያዕቀብ፡ለዮሴፍ፡ለልጁ፡ወደ፡ ሰጠው፡ መንደር፡
አጠገብ፡ ያለች።

፭፤ ከዚያም፡ የያዕቀብ፡ ውኃ፡ ምንጭ፡ ነበረ።
ዘፍጥ፡ ፵፰፤ ፳፪።

፮፤ የሱስ፡ግን፡መንገድ፡ ከመሔድ፡ ደከመ፡ እንዲ
ሁም፡ወደ፡ምንጩ፡ተቀመጠ። የስድስት፡ ሰዓት፡ጊዜ
ም፡ ነበረ።

፯፤ ሴትም፡ ከሰማርያ፡ መጣች፡ ውኃ፡ ልትቀዳ፡ የ
ሱሰም፡ አላት። ስጭኝ፡ እጠጣ። ቍ፡ ፱።

፰፤ ደቀ፡መዛሙርቱ፡ወደገር፡ ሒደው፡ነበሩና፡እን
ጀራ፡ ሊገዙ።

፱፤ የሰማርያዪቱም፡ሴት፡አለችው። እንዴት፡አን
ተ፡የአይሁድ፡ወገን፡ከኔ፡ውኃ፡ትጠጣለህ፡እኔ፡የሰማ
ርያ፡ሴት። (አይሁድ፡ ከሰማርያ፡ ሰዎች፡ ጋራ፡ አይገና
ኙምና)። ማቴ፡ ፲፤ ፭።

፲፤ የሱስም፡ መለሰ፡ አላትም። የእግዚአብሔርን
ስ፡ጸጋ፡ብታውቂ፡ስጭኝ፡እጠጣ፡ ያለሽም፡ ማን፡ እን
ደሆነ። አንቺ፡ትለምኚው፡ነበርሽ፡ እርሱም፡ የሕይወ
ት፡ውኃ፡ ይሰጥሽ፡ ነበር። ም፡ ፯፤ ፴፰፤ ፴፱።

፲፩፤ ሴቲቱም፡አለችው። አቤቱ፡መቅጃ፡የለህ፡ም
ንጭም፡ጥልቅ፡ነው። ከወዴት፡ታገኘለህ፡ የሕይወት፡
ውኃ።

፲፪፤ አንተን፡ካባታችን፡ከያዕቆብ፡ትበልጣለህ፡ ይ
ህነን፡ ምንጭ፡ የሰጠን፡ እርሱም፡ ከርሱ፡ጠጣ፡ ልጆቹ
ም፡ እንስሶቹም።

፲፫፤ የሱስም፡መለሰ፡አላትም። ከዚህ፡ ውኃ፡ የጠ
ጣ፡ ሁሉ፡ ደግሞ፡ ይጸማል። ም፡ ፮፤ ፶፰።

፲፬፤ እኔ፡ ከምሰጠው፡ ውኃ፡ ግን፡ የጠጣ፡ ለዘላለ
ም፡ አይጸማም፡ ነገር፡ ግን፡ እኔ፡ የምሰጠው፡ ውኃ፡የ

ውኃ፡ምንጭ፡ይሆንበታል፡ለዘላለም፡ሕይወት፡የሚ
ፈላ። ም: ፯: ፴፰::

፲፭፤ ሴቲቱም፡ አለችው። አቤቱ፡ ይህነን፡ ውኃ፡ ስ
ጠኝ፡እንዳልጸማ፡ወደዚህም፡ እንዳልመጣ፡ ለመቅ
ደት። ም: ፯: ፴፬::

፲፮፤ የሱስም፡ አላት። ሒጂ፡ባልሽን፡ ጥሪና፡ ወደዚ
ህ፡ ነዪ።

፲፯፤ መለሰች፡ሴቲቱ፡አለችም። ባል፡የለኝም። የሱ
ስም፡ አላት። መልካም ፡ አልሽ ፡ ባል ፡ እንደ ፡ሌለሽ።

፲፰፤ አምስት፡ባሎች፡ነበሩሽና፡ዛሬም፡ካንች፡ጋራ፡
ያለው፡ ባልሽ፡ አይደለውም ። ይህነንስ፡ እውነት፡ አ
ልሽ።

፲፱፤ ሴቲቱም፡አለችው። አቤቱ፡እኔ፡አይሃለሁ፡ አ
ንተ፡ ነቢይ፡እንደ፡ሆንህ። ቍ: ፳፱:: ም: ፯: ፲፬::

፳፤ አባቶቻችን፡ በዚህ፡ተራራ፡ሰገዱ፡ እላንትም፡
ትላላችሁ፡ *በየሩሳሌም ፡ስፍራ፡ እንደለ፡ ይሰገድበ
ት፡ዘንድ፡የሚገባ። *ዘዳግ፡ ፲፪፤ ፭፡፡ መዝ፡ ፻፳፪፡፡

፳፩፤ የሱስም፡አላት። አንች፡ሴት፡ እመኚኝ፡ ጊዜ፡
እንድትመጣ፡በዚህም፡ተራራ፡ በየሩሳሌምም፡ ለአ
ብ፡ የማይሰግዱበት። መል: ፩: ፲፩::
ሉቃ: ፲፯: ፳: ፳፩::

፳፪፤ እላንተ፡ትሰግዳላችሁ፡*ለማታውቁት፡እኛ፡
ለምናውቀው፡ እንሰግዳለን። መድኀኒት፡ †ከአይሁ
ድ፡ነውና። *፪: ነገሥ: ፲፯: ፳፱:: †ዘፍ: ፵፱: ፲:: ሚክ: ፭: ፩፤

፳፫፤ ነገር፡ግን፡ ጊዜ፡ ትመጣለች፡እርስዋም፡ አሁ
ን። በውነት፡ የሚሰግዱ፡ ለአብ፡ በመንፈስ፡ በውነት
ም፡እንዲሰግዱ። አብ፡እንደለዚህ፡ያሉትን፡ይሻልና፡
የሚሰግዱለት።

፳፬፤ እግዚአብሔር ፡ መንፈስ፡ ነው፡ የሚሰግዱለ
ትም፡ በመንፈስ፡ በውነትም፡ ይገባል ፡ ይሰግዱ፡ ዘን
ድ። ፪: ቆሮ: ፫: ፲፯:: መዝ: ፵: ፲:—፲፭::

፳፭፤ ሴቲቱም፡አለችው። አውቃለሁ፡ መሢሕ፡ክ
ርስቶስ፡የሚሉት፡እንዲመጣ። ያም፡በመጣ፡ጊዜ፡ሁ
ሉን፡ያስተምረናል። ም: ፩: ፵፩:: ዳን: ፱: ፳፭::

፳፮፤ የሱስ፡ አላት። እኔ፡ ነኝ፡ የምናገርሽ።
ም: ፱: ፴፯:: ኢሳ: ፶፪: ፮:: ፳፭: ፩::

፳፯፤ በዚህም፡ መጡ፡ ደቀ፡ መዛሙርቱ ፡ አደነቁ
ም፡ከሴት፡ጋራ፡ ስለ፡ መናገሩ። ማንም፡ አላለም፡ ም
ን፡ትሻለህ፡ወይስ፡ ለምን፡ ትናገራታለህ። ቍ: ፱::

፳፰፤ ሴቲቱም፡ማድጋዋን፡ ተወች፡ ወደገርም፡ሔ
ደች፡ ለሰውም፡ አለች።

፳፱፤ኑ፡እዩ፡ ባደረግሁት፡ነገር፡ሁሉ፡ ያስተወቀኝ፡ሰ
ው። ይህ፡ክርስቶስ፡አይደለውምን። ቍ:፲፯:—፳፮::

፴፤ ካገርም፡ ወጡ፡ ወደርሱም፡ መጡ።

፴፩፤ በዚህም፡ ለመኑት፡ደቀ፡መዛሙርቱ፡ እንደ
ህ፡ ሲሉ። መምህር፡ ሆይ፡ ብላ።

፴፪፤ እርሱም፡አላቸው። የምበላው፡መብል፡ አለ
ኝ፡ እላንተ፡ የማታውቁት።

፴፫፤ ደቀ፡መዛሙርቱም፡እርሱ፡በርሳቸው፡አሉ።
አንድ፡ ሰውን፡ አንዳች፡ የሚበላው፡ አመጣለት።

፴፬፤ የሱስም፡ አላቸው። የኔስ፡መብል፡ የላከኝን፡
ፈቃድ ፡ አደርግ ፡ ዘንድ፡ ነው፡ ስራውንም፡ እፈጽም፡
ዘንድ። ም: ፮: ፴፰:—፵:: መዝ: ፵: ፱፤

፴፭፤ እላንተ፡ትሉ፡የላችሁምን። ካራት፡ ወር፡በኋ
ላ፡መከር፡ ይመጣል። እነሆ፡ እላችኋለሁ። ዓይናቻች
ሁን፡አንሡ፡አገሩንም፡እዩ፡መከሩ፡ እንደ፡ ነጸ፡ዛሬ።
ማቴ: ፱: ፴፯::

፴፮፤ የሚያጭድም፡ዋጋውን፡ይወስዳል፡ፍሬም፡
ይሰበስባል፡ለዘላለም፡ ሕይወት። የሚያጭድ፡ የሚ
ዘራም፡ደግሞ፡ባንድ፡ ደስ፡ ይላቸው፡ ዘንድ።

፴፯፤ በዚህ፡ይህ፡ነገር፡እውነት፡ይሆናልና። አንዱ፡
እንዲዘራ፡አንዱም፡ እንዲያጭድ።

፴፰፤ እኔ፡ሰደድኋችሁ፡ እላንተ፡ ያልደከማችሁብ
ትን፡ልታጭዱ። ሌሎች፡ደከሙ፡እላንትም፡በድካማ
ቸው፡ ገባችሁ።

፴፱፤ ከዚያችም፡አገር፡ብዙ፡ የሰማርያ፡ሰዎች፡ በ
ርሱ፡አመኑበት፡ስለ፡ሴቲቱ፡ነገር፡ስለ፡ መሰከረችው።
የሰራሁትን፡ ሁሉ፡ ነገረኝ፡ ብላ።

፵፤ የሰማርያ፡ሰዎችም፡ወደርሱ፡ በመጡ፡ጊዜ፡ለ
መኑት፡ወደርሳቸው፡ይቀመጥ፡ ዘንድ። ከዚያም፡ ሁ
ለት፡ ቀን፡ ተቀመጠ።

፵፩፤ ከዚህም ፡ የበለጠ፡ ብዙ ፡ አመኑበት ፡ ስለ፡
ነገሩ።

፵፪፤ ሴቲቱንም፡ይልዋት፡ነበሩ። አሁን፡በነገርሽ፡ያ
መነ፡አይደለነም፡እኛ፡ሰምተናልና፡ አውቀናልም፡ ይ
ህ ፡ በውነት፡ ክርስቶስ፡ የዓለሙ ፡ መድኀኒት፡ እንደ፡
ሆነ።

፵፫፤ ከሁለት፡ ቀንም፡ በኋላ፡ ከዚያ፡ ወጣ፡ ወደ፡
ገሊላም፡ ሔደ። ማቴ: ፬: ፲፪: ፲፫፤

፵፬፤ የሱስ፡ ራሱ፡ መሰከርዋልና፡ ነቢይ፡ባገሩ፡ እን
ደደከብር። ማቴ: ፲፫: ፶፯፤

፵፭፤ ወደ፡ገሊላም፡ በመጣ፡ ጊዜ፡ የገሊላ፡ ሰዎች፡
ተቀበሉት። በየሩሳሌም፡ በበዓሉ፡ ጊዜ፡ ያደረገውን፡
ሁሉ፡አይተዋልና፡ እርሳቸውም፡ ደግሞ፡ ለበዓል፡መ
ጥተው፡ ነበሩና።

፵፮፤ የሱስም፡ደግሞ፡ወደ፡ቃና፡ገሊላ፡መጣ፡ውኃ
ውን፡ጸጅ፡ ወደደረገበት። በቅፍርናሆም፡ ሰው፡ነበረ፡
የንጉሥ፡ወገን፡ ልጁም፡ ታሞ፡ ነበር። ም: ፪: ፩: ፱::

፵፯፤ ይህ፡በሰማ፡ጊዜ፡የሱስ፡ ከይሁዳ፡ እንደ፡ መ
ጣ፡ወደ፡ገሊላ፡ወደርሱ፡ሔደ፡ ለመነውም፡ ይወርድ፡
ዘንድ፡ ልጁን፡ ሊፈውሰው ። ለሞት ፡ ቀርቦ ፡ ነበረና።
ኤር: ፲፯: ፲፬::

፵፰፤ የሱስም ፡ አለው፡ ምልክት፡ ተአምራትም፡
ካላያችሁ፡ አታምኑም። ም: ፪: ፲፰::
፩: ቆሮ: ፩: ፳፪::

፵፱፤ የንጉሡ፡ሰው፡አለው። ጌታ፡ሆይ፡ውረድ፡ ብ
ላቴናዬ፡ ሳይሞት።

፶፤ የሱስም፡አለው። ሒድ፡ልጅህ፡ ደኅ፡ነው። ያም፡ ሰው፡ አመነ፡ የሱስ፡ ባለው፡ ነገር፡ ሔደም።

ም፡ ፲፬፤ ፲፱፡፡

፶፩፤ እርሱም፡ሲወርድ፡ተቀበሉት፡ባሮቹ፡የምስራቹም፡ ነገሩት፡እንደ፡ሕያው፡ሲሉ። ልጅህ፡ደኅ፡ነው።

፶፪፤ ከርሳቸውም፡ጠየቀ፡የደኅናባትን፡ ጊዜ፡ አሉት፡ም። ትላንት፡ በሰባት፡ ሰዓት፡ ምንቸቱ፡ ተወችው።

፶፫፤ አባቱም፡አወቀ፡የሱስ፡ ልጅህ፡ ደኅ፡ ባለው፡ሰዓት፡እንደ፡ሆነች።እርሱም፡አመነ፡የቤቱም፡ ሰዎች፡ ሁሉ።

ዘፍ፡ ፲፰፤ ፲፱፡፡

፶፬፤ ይህችን፡ ደግሞ፡ ሁለተኛ፡ ተአምራት፡ አደረገ፡የሱስ፡ከይሁዳ፡ ወደ፡ ገሊላ፡ በመጣ፡ ጊዜ።

ም፡ ፪፤ ፲፩፤ ፳፫፡፡

ምዕራፍ፡ ፭፤

፩፤ ከዚህ፡በኋላ፡የአይሁድ፡በዓል፡ ነበረ፡የሱስም፡ ወደ፡ የሩሳሌም፡ ወጣ። ዘሌዋ፡ ፳፫፤ ፴፬፤

፪፤ በየሩሳሌም፡ወደ፡በግ፡ገቢያ፡አጠገብ፡ መጠመቂያ፡ነበራች፡በዕብራይስጥ፡ቤቴስዳ፡የምትባል።አምስት፡ መድረክም፡ ነበረባት ነህም፡ ፫፤ ፩፡፡

፫፤ በዚያ፡ ብዙ፡ በሽተኞች፡ የወደቁ፡ ነበሩ። ዕውሮች፡ አንካሶችም፡ ጎባጦችም። የውኃውንም፡ መታወክ፡ ይጠብቁ፡ ነበሩ።

፬፤ መልአክ፡ በየጊዜው፡ ወደ፡ መጠመቂያው፡ ይወርድ፡ነበርና፡ውኃውንም፡ ያንቀሳቅሰው፡ ነበርና።በፊትም፡የሚወርድ፡ ከውኃው፡ መንቀሳቀስ፡ በኋላ፡ ይፈወስ፡ ነበረ፡ ካለበት፡ ደዌ፡ ሁሉ።

፭፤ ከዚያም፡ ሰው፡ ነበረ፡ ከሠላሳ፡ ስምንት፡ አመት፡ ጀምሮ፡ የታመመ።

፮፤ የሱስም፡ይህነን፡ወድቆ፡ባየ፡ጊዜ፡ ባወቀም፡ ጊዜ፡ብዙ፡ዘመን፡ እንደ፡ሆነው፡ አለው። ትፈወስን፡ ትወዳለህ።

፯፤ ድውዩም፡መለሰለት፡አለውም። ጌታ፡ ሆይ፡ሰው፡የለኝም፡ውኃው፡በተንቀሳቀሰ፡ጊዜ፡ ወደ፡ መጠመቂያው፡ያወርደኝ፡ ዘንድ። ነገር፡ ግን፡ እኔ፡ እስክመጣ፡ ድረስ፡ ሌላው፡ በፊቴ፡ ይወርዳል።

፰፤ የሱስም፡አለው። ተነሣ፡አልጋህን፡ተሸከምና፡ ሒድ።

፱፤ በዚያን፡ጊዜም፡ ደኅ፡ ያ፡ ሰው፡ አልጋውንም፡ ተሸከመና፡ሔደ።ያም፡ቀን፡ሰንበት፡ነበር። ም፡ ፱፤ ፲፬፡፡

፲፤ አይሁድም፡ የዳነውን፡ አሉት። ዛሬ፡ ሰንበት፡ ነው፡ አልጋህን፡ ትሸከም፡ ዘንድ፡ አይገባህም።

ዘፀአ፡ ፳፡ ፰፡፡ ኤር፡ ፲፯፤ ፳፩፡፡

፲፩፤ መለሰላቸው፡አላቸውም። ያዳነኝ፡ እርሱ፡ አለኝ፡ አልጋህን፡ ተሸከምና፡ ሒድ።

፲፪፤ ጠየቁት፡አሉትም። ማነው፡ ያለህ፡ ሰው፡ አልጋህን፡ተሸከምና፡ ሒድ።

፲፫፤ የተፈወሰው፡ግን፡አላወቀም፡ማንም፡እንደ፡ ሆነ።የሱስ፡ተሠውሮ፡ነበርና፡ከዚያ፡በነበሩት፡ ሰዎች፡ መካከል፡እንደሁም፡ሔደ።

፲፬፤ ከዚህ፡በኋላ፡የሱስ፡አገኘው፡በመቅደስ፡አላውም።እነሆ፡ተፈወስህ። ደግሞ፡ተመልሰህ፡ ኃጢአት፡ አትስራ፡ ከዚህ፡ የከፋ፡ እንዳያገኝህ።

ምሳ፡ ፲፬፤ ፴፬፡፡ ሕዝ፡ ፲፰፤ ፬፤ ፳፡፡

መዝ፡ ፴፯፤ ፬፤ ፭፡፡

፲፭፤ ያ፡ሰው፡ሔደ፡ ለአይሁድም፡ ነገረ፡ ያዳነው፡የሱስ፡እንደ፡ሆነ።

፲፮፤ ስለዚህም፡አይሁድ፡የሱስን፡ ያሳድዱት፡ ነበሩ፡ ሊገሉትም፡ይሹ፡ነበሩ፡ይህነን፡ *በሰንበት፡ያደርግ፡ነበርና። *ሉቃ፡ ፲፬፤ ፫፤—፭፡፡

፲፯፤ የሱስ፡ግን፡መለሰላቸው፡አላቸውም። አባቴ፡ እስከ፡ ዛሬ፡ ያደርጋል፡ እኔም፡ *አደርጋለሁ።

*ም፡ ፱፤ ፬፡፡ ፲፬፤ ፲፡

፲፰፤ *ስለዚህም፡ደግሞ፡አይሁድ፡አብዝተው፡ሊገሉት፡ይወዱ፡ነበሩ፡ ሰንበትን፡ በቻ፡ ስላፈረሰ፡ አይደለም፡አባቱንም፡እግዚአብሔር፡ ነው፡ ይል፡ ነበርና፡እንጂ፡ተራሱንም፡በእግዚአብሔር፡ያስተከክል፡ነበር።

*ሮሜ፡ ፰፤ ፴፩፡፡ †ፊል፡ ፪፤ ፮፡፡

፲፱፤ የሱስም፡ መለሰ፡ አላቸውም፡ እውነት፡ እውነት፡እላችኋለሁ።አይችልም፡ ልጅ፡ አንዳች፡ ያደርግ፡ ዘንድ፡ከራሱ፡አብ፡የሚያደርገውን፡ያያል፡እንጂ።እርሱ፡የሚሰራትን፡ስራ፡እርሰዋንም፡ ደግሞ፡ ልጅ፡ እንደሁ፡ ያደርጋልና።

ም፡ ፫፤ ፲፩፤ ፴፪፡፡ ፰፤ ፳፰፤—፳፱፡፡

፳፤ አብ፡ ልጅን፡ *ይወዳልና፡ የሚያደርገውንም፡ ሁሉ፡ ያሳየዋል፡ ከዚህም፡ የሚበልጥ፡ ስራ፡ ያሳየዋል፡እላንት፡ †ልታደንቁ። *ማቴ፡ ፫፤ ፲፯፡፡ †ም፡ ፩፤ ፶፡፡

፳፩፤ አብም፡ሙታንን፡*እንደ፡ያስነሣ፡እንደ፡ያድናቸውም፡ እንደሁ፡ ልጅም፡ደግሞ፡ የወደደውን፡ ያድናል። *ዘዳግ፡ ፴፪፤ ፴፱፡፡ ሆሴ፡ ፮፤ ፩፤ ፪፡፡

፳፪፤ አብ፡ በማንም፡አይፈርድምና። ነገር፡ ግን፡ ፍርድን፡ ሁሉ፡ ለልጅ፡ ሰጠው። ዳን፡ ፯፤ ፲፫፤ ፲፬፡፡

የሐዋ፡ ፲፯፤ ፴፩፡፡

፳፫፤ ሰው፡ ሁሉ፡ልጅን፡ ያከብሩ፡ ዘንድ፡ አብን፡ እንደ፡ያከብሩ። ልጅን፡የማያከብር፡አብን፡የላከውን፡ አያከብርም። ፊል፡ ፪፤ ፲፤ ፲፩፡፡ ፩፤ ዮሐ፡ ፪፤ ፳፫፡፡

፳፬፤ እውነት፡ እውነት፡ እላችኋለሁ። ነገሬን፡ *የሚሰማ፡ በሰደደኝም፡ የሚያምን፡ ለዘላለም፡ ሕይወት፡ †አለው፡ ወደ፡ ፍርድም፡ አይሔድም፡ከሞት፡ ወደ፡ ሕይወት፡ ተሻገረ፡ እንጂ። *ም፡ ፲፯፤ ፴፮፡፡

መዝ፡ ፴፪፤ ፩፤ ፪፡፡ †ሮሜ፡ ፰፤ ፩፡፡ ፩፤ ዮሐ፡ ፫፤ ፲፬፡፡

፳፭፤ እውነት፡ እውነት፡ እላችኋለሁ፡ ጊዜ፡ እንድ፡ ትመጣ፡እርሰዋም፡ዛሬ፡ሙታን፡የእግዚአብሔርን፡ ልጅ፡ ቃል፡ የሚሰሙባት፡ የሚሰሙም፡ ይድናሉ።

ኤፌ፡ ፪፤ ፭፤ ፮፡፡

፳፮፤ አብ፡ከርሱ፡ ዘንድ፡ ሕይወት፡ *እንደለው፡ እንደሁ፡ ደግሞ፡ ለልጅ፡ ሰጠው፡ ሕይወት፡ †ከርሱ፡ ትሆን፡ ዘንድ። *ም፡ ፩፤ ፩፤—፬፡፡

†፩፤ ዮሐ፡ ፭፤ ፲፩፤—፲፪፡፡

፳፯፡ ደግሞም፡ሥልጣን፡ሰጠው፡ፍርድ፡ ያደርግ፡ ዘንድ፡ የሰው፡ ልጅ፡*ነውና። *ዳን፡ ፯፡ ፲፫፡ ፲፬፡፡

፳፰፡ በዚህ፡አታድንቁ። ጊዜ፡ትመጣለችና፡በመቃብር፡ያሉት፡ ሁሉ፡ ቃሉን፡ የሚሰሙባት። ፩፡ ተሰ፡ ፬፡ ፲፯፡፡

፳፱፡ ይወጡማል፡ መልካም፡ የሰሩ፡ ወደ፡ ሕይወት፡ ትንሣኤ፡ክፉም፡ የሰሩ፡ ወደ፡ ፍርድ፡ ትንሣኤ። ምዕ፡ ፮፡ ፵፡፡ ዳን፡ ፲፪፡ ፪፡፡

፴፡ እኔ፡ ከራሴ፡ አንዳች፡ አደርግ፡ ዘንድ፡ አልችልም። እንድሰማ፡ እፈርዳለሁ፡ ፍርዴም፡ እውነት፡ ነው። ፈቃዴን፡አልሻምና፡የአብን፡የላከኝን፡ ፈቃድ፡ እንጂ። ቍ፡ ፲፱፡፡ ምዕ፡ ፮፡ ፴፰፡፡

፴፩፡ እኔስ፡ ለራሴ፡ብመሰክር፡ምስክሬ፡እውነት፡ አይደለችም። ምዕ፡ ፰፡ ፲፫፡ ፲፬፡ ፶፬፡፡

፴፪፡ ለኔ፡ የሚመሰክረው፡ ሌላ፡ነው። ስላኔም፡ የሚመሰክራት፡ምስክር፡ እውነት፡እንደ፡ ሆነች፡ አውቃለሁ። ቍ፡ ፴፯፡፡ ማቴ፡ ፫፡ ፲፯፡፡

፴፫፡ እላንት፡ ወደ፡ዮሐንስ፡ላካችሁ፡ለውነትም፡ መሰከረ። ምዕ፡ ፩፡ ፲፱፡፡

፴፬፡ እኔ፡ ግን፡ ምስክር፡ ከሰው፡ አልወስድም፡ ነገር፡ግን፡ይህነን፡ ማለቴ፡ እላንት፡ ልድኑ፡ነው።

፴፭፡ ያ፡ መብራት፡ ነበረ፡ የሚቃጠል፡ የሚያበራም፡ እላንትም፡ ጥቂት፡ ዘመን፡ በብርሃኑ፡ ደስ፡ ይላችሁ፡ ዘንድ፡ ወደዳችሁ።

፴፮፡ እኔ፡ግን፡*ምስክር፡ አለኝ፡ከዮሐንስ፡ምስክር፡ የሚበልጥ። አባቴ፡ የሰጠኝ፡ ስራ፡ልፈጽማት። ይህች፡ †ስራ፡ ራስዋ፡ የማደርጋት፡ ስለኔ፡ ትመሰክራለች፡ አብ፡ እንደ፡ ላከኝ። *፩፡ ዮሐ፡ ፭፡ ፱፡፡ †ምዕ፡ ፲፬፡ ፲፩፡፡

፴፯፡ አብም፡ የላከኝ፡ እርሱ፡ ስለኔ፡ መሰከረ። ቃሉን፡ አልሰማችሁም፡ ከቶ፡ ምሳሌውንም፡ *አላያችሁም። ማቴ፡ ፫፡ ፲፯፡፡ *ዘፀአ፡ ፴፫፡ ፳፡፡

፴፰፡ ነገሩም፡ በላንት፡ ጸንታ፡ የለችባችሁም፡ እላንት፡ እርሱ፡ በላከው፡ አታምኑምና።

፴፱፡ መጻሕፍትን፡ *እሹ። እላንት፡ ይመስላችኋልና፡ በርሳቸው፡ የዘላለም፡ ሕይወት፡ የምታገኙ። እርሳቸውም፡ †ስለኔ፡የሚመሰክሩ፡ናቸው። *ኢሳ፡ ፴፬፡ ፲፮፡፡ †ዘዳግ፡ ፲፰፡ ፲፭፡—፲፰፡፡

፵፡ ወደኔም፡ ትመጡ፡ ዘንድ፡አትወዱም፡ሕይወት፡ ተሆንላችሁ፡ ዘንድ። ማቴ፡ ፳፫፡ ፴፯፡፡

፵፩፡ ከሰው፡ ምስጋና፡ አልወስድም። ቍ፡ ፴፬፡ ፵፬፡፡

፵፪፡ ነገር፡ግን፡ እላንትን፡ አወቅኋችሁ፡ የእግዚአብሔር፡ ፍቀር፡ በውሥጣችሁ፡ እንደ፡ ሌለባችሁ።

፵፫፡ እኔ፡ባባቴ፡ ስም፡ መጣሁ፡ አልተቀበላችሁኝም። ሌላው፡ ቢመጣ፡ *በራሱ፡ ስም፡ ትቀበሉታላችሁ። *ማቴ፡ ፳፬፡ ፭፡፡

፵፬፡ እንዴት፡ ትችላላችሁ፡ እላንት፡ ታምኑ፡ ዘንድ፡ እርሱ፡ በርሳችሁ፡ ክብር፡ ስትቀበሉ፡ ካንዱ፡ም፡ እግዚአብሔር፡ ያለውን፡ *ክብር፡ አትሹም። *ምዕ፡ ፲፪፡ ፵፪፡ ፵፫፡፡

፵፭፡ እኔ፡ ከአብ፡ዘንድ፡ የማጣላችሁ፡ አይምሰላችሁ። የሚያጣላችሁ፡ አለ። ሙሴ፡ እላንት፡ የምትታመኑት። ዘዳግ፡ ፴፩፡ ፳፮፡፡

፵፮፡ በሙሴስ፡ ብታምኑ፡በኔ፡ባመናችሁብኝ፡ ደግሞ። እርሱ፡ ስለኔ፡ጽፏልና። ዘፍ፡ ፫፡ ፲፭፡፡ ፵፱፡ ፲፡፡ ዘዳግ፡ ፲፰፡ ፲፭፡፡

፵፯፡ በዚያ፡ መጻሕፍት፡ ግን፡ካላመናችሁ፡እንዴት፡ በነገሬ፡ ታምናላችሁ።

## ምዕራፍ፡ ፮፡

፩፡ ከዚያ፡ በኋላ፡ የሱስ፡ ሔደ፡ ወደ፡ ገሊላ፡ባሕር፡ ማዶ፡ እርሱም፡ የጥብርያደስ፡ ባሕር።

፪፡ እጅግም፡ሰዎች፡ተቀተሉት፡በድውያን። የሚያደርጋትን፡ ተአምራት፡ ያዩ፡ ነበሩና።

፫፡ የሱስም፡ ወደ፡ ተራራ፡ደግሞ፡ወጣ፡ ከዚያም፡ ተቀመጠ፡ ከደቀ፡ መዛሙርቱ፡ ጋራ።

፬፡ ፋሲካም፡ የአይሁድ፡ በዓል፡ ቀርቦ፡ ነበረ። ምዕ፡ ፪፡ ፲፫፡፡ ፲፩፡ ፶፭፡፡

፭፡ የሱስም፡ ዓይኑን፡ አነሣ፡ ብዙ፡ ሰዎችም፡ ወደ፡ ርሱ፡ ሲመጡ፡ አየ፡ ፊልጶስንም፡ አለው። ከወዴት፡ እንጀራ፡ እንገዛለን፡ እሌህ፡ ይበሉ፡ ዘንድ። ማቴ፡ ፲፬፡ ፲፭፡—፳፩፡፡ ማር፡ ፮፡ ፴፬፡—፵፬፡፡ ሉቃ፡ ፱፡ ፲፪፡—፲፯፡፡

፮፡ ይህነንም፡ ማለቱ፡ ሊፈትነው። እርሱ፡ የሚያደርገውን፡ ያውቅ፡ ነበርና።

፯፡ ፊልጶስም፡ መለሰለት፡ አለውም። እንጀራ፡ በሁለት፡ መቶ፡ ድሪም፡ አይበቃቸውም፡ ከርሳቸው፡ ኢያንዳንዱ፡ ጥቂት፡ ጥቂት፡ ይወስድ፡ዘንድ።

፰፡ ከደቀ፡ መዛሙርቱም፡ እንዱ፡ አለው፡ እርሱም፡ እንድርያስ፡ የሲሞን፡ ጴጥሮስ፡ ወንድም።

፱፡ ከዚህ፡ ጕልማሳ፡ አለ፡ አምስት፡ ገብስ፡ እንጀራ፡ የያዘ፡ ሁለትም፡ ዓሣ። ነገር፡ ግን፡ ምን፡ ይበቃል፡ ይህ፡ እሌህን፡ ለሚያህሉ።

፲፡ የሱስም፡ አለ። ሰዎችን፡ እንዲቀመጡ፡ አድርጉ። በዚያም፡ሰፊ፡ እጅግ፡ መስክ፡ነበረ። ሰዎችም፡ ተቀመጡ፡ ቍጥራቸውም፡ አምስት፡ ሺህ፡ ነበሩ።

፲፩፡ የሱስም፡እንጀሮችም፡ወሰደ፡ አመሰገነም፡ ለደቀ፡ መዛሙርቱም፡ሰጠ።ደቀ፡መዛሙርቱም፡ ለተቀመጡት፡ ሰጡ። እንደሁም፡ ከሁለቱ፡ዓሦች፡ በወደዱት፡ መጠን።

፲፪፡ በጸገቡም፡ ጊዜ፡ደቀ፡መዛሙርቱን፡ አለ። የቀረውን፡ቍራሽ፡አከማቹ፡ከርሱ፡አንድ፡ እንደይጠፋ።

፲፫፡ አከማቹም፡አሥራ፡ሁለትም፡ ሞሰብ፡መሉ፡ ካምስቱ፡ገብስ፡ እንጀራ፡ ቍራሽ፡ የቀረ፡ ከበሎች።

፲፬፡ ሰዎችም፡ የሱስ፡ ያደረገውን፡ ተአምራት፡ ባ

ዩ፡ ጊዜ፡ አሉ። በውነት፡ ይህ፡ *ነቢይ፡ ነው፡ ወደ፡ ዓለ
ም፡ የሚመጣው። *ዘዳግ፡ ፲፰፡ ፲፭፡—፲፰።

፲፭፡ የሱስም፡አውቀ፡እንዲመጡ፡ እንዲነጥቁት
ም፡ያነግሡት፡ ዘንድ። ደግሞ፡ ወደ፡ ተራራ፡ ፈቀቅ፡
አለ፡ ብቻውን። ም፡ ፲፰፡ ፴፮።

፲፮፡ በመሸም፡ ጊዜ፡ደቀ፡መዛሙርቱ፡ወደ፡ባሕር፡
ወረዱ። ማቴ፡ ፲፬፡ ፳፫፡—፴፮።
ማር፡ ፮፡ ፵፯፡—፶፮።

፲፯፡ በታንኳም፡ተቀመጡ፡ወደ፡ቅፍርናሆምም፡
በባሕር፡ ማዶ፡ ሔዱ። ጨልሞም፡ ነበር። የሱስም፡ ገ
ና፡ ወደርሳቸው፡ አልመጣም።

፲፰፡ ባሕሩም፡ በጽኑ፡ ነፋስ፡ ታወከ።

፲፱፡ ሔዱም፡ ሀያ፡ አምስት፡ ምዕራፍ፡ ያህል፡ ወ
ይም፡ሠላሳ። የሱስንም፡በባሕር፡ ላይ፡ሲሔድ፡ አዩ፡
ወደ፡ ታንኳውም፡ ሲቀርብ። ፈሩም።

፳፡ እርሱ፡ ግን፡ አላቸው። እኔ፡ ነኝ። አትፍሩ።
ኢሳ፡ ፵፫፡ ፩፡—፫።

፳፩፡ ወደ፡ መርከብም፡ ያወጡት፡ ዘንድ፡ ወደዱ።
የዚያን፡ ጊዜውም፡ መርከቢቱ፡ ወደ፡ ምድር፡ ደረሰ
ች፡ ይሔዱባት፡ ወደ፡ ነበሩ።

፳፪፡ በነገውም፡ በባሕር፡ ዳር፡ ቁመው፡ የነበሩት፡
ሰዎች፡ ባዩ፡ጊዜ፡ ሌላ፡መርከብ፡ ከዚያ፡እንዳልነበረ፡
ደቀ፡ መዛሙርቱ፡ገብተውባት፡ከነበረበት፡ከዚያች፡
ካንዲት፡ በቀር፡ የሱስም፡ ከደቀ፡ መዛሙርቱ፡ ጋራ፡
ወደ፡ መርከብ፡ እንዳልገባ። ነገር፡ ግን፡ ደቀ፡ መዛሙ
ርቱ፡ ሔደ፡ ለብቻቸው።

፳፫፡ ሌላ፡ መርከብ፡ ግን፡ ደግሞ፡ ነበረች፡ ከጥብር
ያዶስ፡የመጣች፡ እንጀራ፡በበሉበት፡ስፍራ፡አጠገብ፡
ጌታ፡ በባረከ፡ ጊዜ። ቍ፡ ፲፩።

፳፬፡ ሕዝቡም፡ ባዩ፡ጊዜ፡የሱስ፡ እርሱ፡ ከዚያ፡ እ
ንደ፡ ሌለ፡ ደቀ፡ መዛሙርቱም። እርሳቸውም፡ ደግ
ሞ፡በመርከቦች፡ ሰፈሩ፡ ወደ፡ቅፍርናሆምም፡መጡ፡
የሱስን፡ ሊሹ።

፳፭፡ ባገኙትም፡ ጊዜ፡ በባሕር፡ ማዶ፡ አሉት። ረ
ቢ፡ መቼ፡ ወደዚህ፡ መጣህ።

፳፮፡ የሱስም፡ መለሰላቸው፡ አለም። እውነት፡
እውነት፡ እላችኋለሁ። ትሹኛላችሁ፡ ተአምራት፡ በ
ማየታችሁ፡ እኩል፡አይደለም። እንጀራ፡ ስለ፡ በላች
ሁና፡ ስለ፡ ጸገባችሁም፡ እንጂ።

፳፯፡ አድርጉ፡ ለሚጠፋው፡ መብል፡ አይደለም፡
ለመብል፡ እንጂ፡ ለዘላለም፡ ሕይወት፡ ለሚኖር፡ የሰ
ው፡ ልጅ፡ የሚሰጣችሁ። ይህነን፡ እግዚአብሔር፡ አ
ብ፡ አትሞታልና። ም፡ ፫፡ ፲፮። ፬፡ ፲፬።

፳፰፡ አሉትም። ምን፡ እንስራ፡ የእግዚአብሔር
ን፡ ስራ፡ እናደርግ፡ ዘንድ።

፳፱፡ መለሰ፡ የሱስ፡አላቸውም። ይህ፡ ነው፡የእግ
ዚአብሔር፡ ስራ፡ ታምኑ፡ ዘንድ፡ እርሱ፡ በላከው።
፩፡ ዮሐ፡ ፫፡ ፳፫።

፴፡ አሉትም። ምን፡ ተአምራት፡ ታደርጋለህ፡ አይ
ተናት፡ እናምንብህ፡ ዘንድ። ምንድር፡ ትሰራለህ።
ማቴ፡ ፲፮፡ ፩።

፴፩፡ አባተቻችን፡ መና፡ በሉ፡ በምድረ፡ በዳ፡ እንደ፡
ተጻፈ። እንጀራ፡ ከሰማይ፡ ሰጣቸው፡ ይበሉ፡ ዘንድ።
ዘፀአ፡ ፲፮፡ ፲፫፡ ፲፬። መዝ፡ ፸፰፡ ፳፬።

፴፪፡ የሱስም፡ አላቸው። እውነት፡ እውነት፡ እላ
ችኋለሁ። ሙሴ፡ ከሰማይ፡ እንጀራ፡ እንደልሰጣች
ሁ። ነገር፡ ግን፡ አባቴ፡ እውነተኛ፡ እንጀራ፡ ከሰማይ፡
ይሰጣችኋል። ቍ፡ ፴፫፡ ፶፰።

፴፫፡ የእግዚአብሔር፡ እንጀራ፡ እርሱ፡ ከሰማይ፡
የወረደው፡ ነውና፡ ሕይወትም፡ ለዓለም፡ የሚሰጥ።
ዘዳግ፡ ፰፡ ፫።

፴፬፡ አሉትም። ጌታ፡ ሆይ፡ ይህነን፡ እንጀራ፡ ሁለግ
ዜ፡ ስጠነ።

፴፭፡ የሱስም፡ አላቸው። እኔ፡ ነኝ፡ የሕይወት፡ እ
ንጀራ። ወደኔ፡ የሚመጣ፡ አይራብም። የሚያምን
ብኝም፡ *አይጸማም፡ ለዘላለም። ም፡ ፬፡ ፲፬።
ኢሳ፡ ፶፭፡ ፩።

፴፮፡ ነገር፡ ግን፡ አልኋችሁ፡ አይታችሁኝ፡ ደግሞ፡ እ
ንደላመናችሁብኝ።

፴፯፡ አብ፡ የሰጠኝ፡ ሁሉ፡ ወደኔ፡ ይመጣል። ወደኔ
ም፡ የሚመጣውን፡ ወደ፡ ሜዳ፡ *አልሳደውም።
ማቴ፡ ፲፩፡ ፳፰። *ም፡ ፲፯፡ ፮፡—፰።

፴፰፡ ከሰማይ፡ ወርጀለሁና፡ ፈቃዴን፡ ለማድረግ፡
አይደለም። *የላከኝን፡ ፈቃድ፡ እንጂ።
*ም፡ ፬፡ ፴፬። መዝ፡ ፵፡ ፰።

፴፱፡ የላከኝም፡ የአብ፡ ፈቃድ፡ ይህች፡ ናት፡ የሰጠኝ
ን፡ ሁሉ፡ ማንንም፡ እንዳላጠፋ። ነገር፡ ግን፡ አስነሣዋ
ለሁ፡ በኋለኛዪቱ፡ ቀን። ም፡ ፲፡ ፳፰፡ ፳፱።

፵፡ የላከኝም፡ ፈቃድ፡ ይህች፡ ናት። *ልጁን፡ ያየ፡
ሁሉ፡ የሚያምንበትም፡ የዘላለም፡ ሕይወት፡ ትሆን
ለት፡ ዘንድ። እኔም፡ አስነሣዋለሁ፡ በኋልኛዪቱ፡ ቀን።
*ዘኍል፡ ፳፩፡ ፰፡ ፱። ም፡ ፫፡ ፲፬።

፵፩፡ ስለዚህም፡ አይሁድ፡ አንጐረጐሩበት። ብል
ዋልና፡ እኔ፡ ነኝ፡ ከሰማይ፡ የወረደ፡ እንጀራ።

፵፪፡ ይሉም፡ ነበሩ። ይህ፡ የሱስ፡ *የዮሴፍ፡ ልጅ፡
አይደለምን። እኛ፡ አባቱንና፡ እናቱን፡ የምናውቃቸ
ው። እንዴትስ፡ ይላል፡ ይህ። ከሰማይ፡ ወረድሁ።
*ማቴ፡ ፲፫፡ ፶፭።

፵፫፡ የሱስም፡ መለሰ፡ አላቸውም። አታንጐርጐ
ሩ፡ እርሱ፡ በርሳችሁ።

፵፬፡ ማንም፡ ወደኔ፡ መምጣት፡ አይችልም፡ የላ
ከኝ፡ አብ፡ ከሳበው፡ በቀር። እኔም፡ አስነሣዋለሁ፡ በ
ኋለኛው፡ ቀን። ቍ፡ ፷፭።

፵፭፡ በነቢያት፡ የተጻፈ፡ ነው። ሁላቸውም፡ ከእግ
ዚአብሔር፡ ዘንድ፡ *የተማሩ፡ ይሆናሉ። ካባትም፡ የ
ሰማ፡ ሁሉ፡ ከርሱም፡ የተማረ፡ ወደኔ፡ ይመጣል።
*ኢሳ፡ ፶፬፡ ፲፫። ኤር፡ ፴፩፡ ፴፫፡ ፴፬።

፵፮፤ አንድም፡ አብን፡ያየ፡የለም፡ከእግዚአብሔ
ር፡ ከሚሆን፡ በቀር። እርሱ፡ አባትን፡ አየ።
፩፤ ጢሞ፡ ፮፤ ፲፮።
፵፯፤ እውነት፡እውነት፡እላችኋለሁ። በኔ፡የሚያ
ምን፡የዘላለም፡ ሕይወት፡ እንዳለው። ም፡ ፫፤ ፲፮።
፵፰፤ እኔ፡ ነኝ፡ የሕይወት፡ እንጀራ። ቍ፡ ፴፭።
፵፱፤ አባቶቻችሁ፡ መና፡ በሉ፡ በምድረ፡ በዳ፡ ሞ
ቱም። ቍ፡ ፴፩፤ ፴፪። ፩፤ ቆሮ፡ ፲፤ ፫፤ ፭።
፶፤ ይህ፡ነው፡ከሰማይ፡የወረደው፡እንጀራ፡ከርሱ፡
የሚበላ፡ ሁሉ፡ እንዳይሞት።
፶፩፤ እኔ፡ ነኝ፡ ሕያው፡እንጀራ፡ከሰማይ፡የወርደ።
ማንም፡ በዚህ፡እንጀራ፡የበላ፡ *ለዘላለም፡ይኖራል።
እኔም፡ የምሰጠው፡ እንጀራ፡ ሥጋዬ፡ ነው፡ ስለ፡ ዓለ
ም፡ ሕይወት፡ እሰጠው፡ ዘንድ፡ ያለኝ።
*ም፡ ፲፩፤ ፳፮። †ገላት፡ ፪፤ ፳። ዕብ፡ ፲፤ ፲።
፶፪፤ አይሁድም፡ እርሱ፡ በርሳቸው፡ተከራከሩ፡ እ
ንደሁ፡ ሲሉ። እንዴት፡ ይችላል፡ ይህ፡ ሥጋውን፡ ይሰ
ጠን፡ ዘንድ፡ ልንበላው።
፶፫፤ የሱስም፡አላቸው። እውነት፡እውነት፡ እላች
ኋለሁ። የሰውን፡ ልጅ፡ሥጋ፡ ካልበላችሁ፡ደሙንም፡
ካልጠጣችሁ፡ በላንት፡ ሕይወት፡ የላችሁም።
፶፬፤ ሥጋዬን፡ የበላ፡ ደሜንም፡ የጠጣ፡ለርሱ፡ የዘ
ላለም፡ ሕይወት፡አለው። እኔም፡አስነሣዋለሁ፡በኋ
ለኛው፡ ቀን።
፶፭፤ ሥጋዬ፡ በውነት፡ መብል፡ ነውና። ደሜም፡ በ
ውነት፡ መጠጥ፡ ነውና።
፶፮፤ ሥጋዬን፡የበላ፡ ደሜንም፡ የጠጣ፡ በኔ፡ ይኖራ
ል፡ እኔም፡ በርሱ፡ እኖራለሁ። ም፡ ፲፭፤ ፬።
፩፤ ዮሐ፡ ፫፤ ፳፬።
፶፯፤ ሕያው፡ አብ፡ እንደ፡ ላከኝ፡ እኔም፡ ሕያው፡
ነኝ፡ ስለ፡ አብ። የሚበላኝም፡ ደግሞ፡ እርሱ፡ ስለኔ፡
ሕያው፡ ይሆናል።
፶፰፤ ይህ፡ ነው፡ከሰማይ፡ የወረደ፡እንጀራ። አባቶ
ቻችሁ፡ በልተውት፡ እንደ፡ ሞቱ፡ ያለ፡ መና፡ አይደለ
ም። ይህነን፡ እንጀራ፡ የበላ፡ ለዘላለም፡ ይኖራል።
፶፱፤ ይህነን፡ አለ፡ በመስጊድ፡ ሲያስተምር፡ በቅፍ
ርናሆም።
፷፤ ብዙም፡ሰዎች፡ ከደቀ፡ መዛሙርቱ፡ይህነን፡ በ
ሰሙ፡ ጊዜ፡ አሉ። ይህች፡ነገር፡ ጭንቅ፡ ናት። ማን፡ ይ
ችላል፡ ሊሰማት።
፷፩፤ የሱስም፡ በልቡ፡ ባወቀ፡ጊዜ፡ ደቀ፡ መዛሙር
ቱ፡ ስለዚህ፡ እንዲያንጐረጕሩ፡ አላቸው። ይህን፡ ያ
ጠራጥራችኋል።
፷፪፤ እንዴት፡ ነው፡ ብታዩ፡ የሰው፡ ልጅ፡ ሲወጣ፡
ቀድሞ፡ ወደ፡ ነበረበት።
፷፫፤ መንፈስ፡ ነው፡ ሕይወት፡ የሚሰጥ። ሥጋ፡ አ
ንዳች፡ አይጠቅምም። እኔ፡የምነግራችሁ፡ነገር፡ መን
ፈስ፡ ነው፡ ሕይወትም፡ ነው። ፪፤ ቆሮ፡ ፫፤ ፮።
፷፬፤ ነገር፡ ግን፡ ከላንት፡ ሰዎች፡ የማያምኑ፡ አሉ።
የሱስ፡ ከጥንት፡ ጀምሮ፡ ያውቅ፡ ነበርና፡ ማንኛቸው፡ የ
ማያምኑ፡ አሳልፎ፡ የሚሰጠውስ፡ ማነው።
ም፡ ፲፫፤ ፲፩።
፷፭፤ አለም። ስለዚህ፡ አልኋችሁ። ወደኔ፡ መም
ጣት፡ የሚችል፡ እንደ፡ ሌለ፡ ካባቴ፡ የተሰጠው፡ ካል
ሆነ። ቍ፡ ፵፬።
፷፮፤ ስለዚህም፡ ነገር፡ እጅግ፡ ሰዎች፡ከደቀ፡ መዛ
ሙርቱ፡ ወደ፡ ኋላቸው፡ ተመለሱ፡ ከዚያም፡ በኋላ፡
ከረሱ፡ ጋራ፡ አልሔዱም።
፷፯፤ የሱስም፡ ለሠራ፡ ሁለቱ፡ አለ። እላንትምን፡
መሔድ፡ ትሻላችሁ።
፷፰፤ ሲሞን፡ ጴጥሮስም፡ መለሰለት፡ አለውም።
ጌታ፡ ሆይ፡ ወዴት፡ ዘንድ፡ እንሔዳለን። የዘላለም፡
የሕይወት፡ ቃል፡ ላንት፡ ናት። ቍ፡ ፷፫።
፷፱፤ እኛስ፡ ፈጽመን፡ አምነናል፡ አውቀናልም፡
አንተ፡ *ክርስቶስ፡ የሕያው፡ የእግዚአብሔር፡ ልጅ፡
እንደ፡ ሆንህ። *ም፡ ፩፤ ፵፱። ፲፩፤ ፳፯።
ማቴ፡ ፲፮፤ ፲፮።
፸፤ የሱስም፡ መለሰላቸው፡ አላቸውም። እኔ፡ አ
ሥራ፡ ሁለት፡ መርጫችሁ፡ አልነበርሁምን፡ ከላንት
ም፡ አንዱ፡ ሰይጣን፡ ነው። ሉቃ፡ ፮፤ ፲፫።
፸፩፤ ይህነንም፡ ስለ፡ ይሁዳ፡ አስቆርታዊ፡ ስለ፡ ሲ
ሞን፡ ልጅ፡ አለ። ይህ፡ ነበረና፡ ኋላ፡ያስያዘው፡ እርሱ
ም፡ ካሥራ፡ ሁለቱ፡ አንዱ፡ ነበር።

## ምዕራፍ፡ ፯፤

፩፤ ከዚህም፡ በኋላ፡ የሱስ፡ ወደ፡ ገሊላ፡ ይሔድ፡
ነበረ። ወደ፡ ይሁዳ፡ ይሔድ፡ ዘንድ፡ አልወደደምና፡
አይሁድ፡ ይገሉት፡ ዘንድ፡ ይሹ፡ ነበሩና።
፪፤ የአይሁድም፡ በዓል፡ደስ፡ የሚተክሉበት፡ ቀር
ቦ፡ ነበረ። ዘሌዋ፡ ፳፫፤ ፴፬።
፫፤ ወንድሞቹም፡አሉት። ከዚህ፡ ውጣ፡ ወደ፡ ይ
ሁዳም፡ ምድር፡ ሒድ፡ ደቀ፡ መዛሙርትህ፡ ደግሞ፡
የምትሰራትን፡ ስራ፡ ያዩ፡ ዘንድ። ማቴ፡ ፲፪፤ ፵፮።
የሐዋ፡ ፩፤ ፲፬።
፬፤ ማንም፡ በቀስታ፡ ነገር፡ የሚያደርገው፡ የለም
ና፡ እርሱም፡ በግልጥ፡ ይሆን፡ ዘንድ፡ ይወዳል። ይህነ
ንስ፡ ማድረግ፡ ትወድ፡ እንደ፡ ሆንህ፡ ራስህን፡ ለዓለ
ም፡ አሳይ።
፭፤ ወንድሞቹም፡ደግሞ፡አላመኑበትም፡ነበሩና።
መዝ፡ ፷፱፤ ፱።
፮፤ የሱስም፡ አላቸው። *ጊዜዬ፡ ገና፡አልደረሰም።
የላንት፡ ጊዜ፡ ሁለጊዜ፡ የተዘጋጀ፡ ነው። *ም፡ ፪፤ ፬።
፯፤ ዓለም፡ እላንትን፡ ይጸላችሁ፡ ዘንድ፡ አይችል
ም። እኔን፡ ግን፡ይጸላኛል። እኔ፡ እመሰክርበታለሁና፡
ስራው፡ ክፉ፡ እንደ፡ ሆነች። ም፡ ፫፤ ፲፱፤ ፳።
፰፤ እላንት፡ ወደዚህ፡ በዓል፡ ውጡ፡ እኔ፡ ዛሬ፡ ወ
ደዚህ፡ በዓል፡ አልወጣም። ጊዜዬ፡ ገና፡ አልተፈጸመ
ምና። ም፡ ፰፤ ፳።

፱፤ ይህነንም፡ ገላቸው፡ ጊዜ፡ በገሊላ፡ ቀረ።

፲፤ ወንድሞቹ፡ግን፡ ከወጡ፡በኋላ፡እርሱም፡ ደግሞ፡ የዚያን፡ ጊዜ፡ ለበዓል፡ ወጣ። ተገልጦ፡ አይደለም፡ ተሠውሮ፡እንጂ።

፲፩፤ አይሁድ፡ግን፡በበዓል፡ይሹት፡ነበረ፡ይላሉም። ያ፡ ወዴት፡ነው።

፲፪፤ በሕዝብም፡ ብዙ፡ማንጐራጐር፡ ነበር፡ ስለርሱ። ከርሳቸውም፡ ቸር፡ ነው፡ የሚሉ፡ ነበሩ፡ ሌሎችም፡ አይደለም፡ሕዝቡን፡ያስታል፡ እንጂ፡ ይሉ፡ነበር። ም፡ ፱፡ ፲፮፡፡

፲፫፤ ማንም፡ ተገልጦ፡ የሚናገርበት፡ አልነበረም። ከአይሁድ፡ ስለ፡ ፈሩ። ም፡ ፲፪፡ ፵፪፡፡

፲፬፤ በበዓሉም፡ እኩሌታ፡ወጣ፡የሱስ፡ ወደ፡ መቅደስ፡ ያስተምርም፡ ነበር።

፲፭፤ አይሁድም፡ ይደነቁ፡ ነበር፡ እንደሁ፡ ሲሉ፡ ይህ፡ እንዴት፡ መጽሐፍ፡ ያሳምራል፡ እርሱም፡ ያልተማሬት። ማቴ፡ ፲፫፡ ፶፬፡፡

፲፮፤ የሱስም፡ መለሰላቸው፡ አለም። ትምህርቴ፡ የኔ፡ አይደለም፡ የላከኝ፡ ነው፡ እንጂ። ም፡ ፰፡ ፳፮፡ ፳፰፡፡

፲፯፤ አንድም፡ፈቃዱን፡ ያደርግ፡ዘንድ፡ የሚወድ፡ ቢኖር፡ እርሱ፡ ትምህርቱን፡ ያውቃል፡ከእግዚአብሔር፡ ዘንድ፡ ነው፡ ወይስ፡ እኔ፡ ከራሴ፡ እናገርበታለሁ። ም፡ ፫፡ ፳፩፡፡ ፰፡ ፴፩፡ ፴፪፡ ፵፯፡፡

፲፰፤ ከራሱ፡ የሚናገር፡ የራሱን፡ ክብር፡ ይሻልና። የላከውን፡ግን፡ ክብር፡ የሚሻ፡ እርሱ፡ እውነተኛ፡ ነው። በርሱም፡አሰት፡የለበትም። ም፡ ፭፡ ፵፩፡ ፵፬፡፡

፲፱፤ ሙሴ፡*ኦሪትን፡ የሰጣችሁ፡ አይደለምን። ከላንትም፡አንድ፡ኦሪትን፡የሚያደርግ፡የለም። †ለምን፡ ትገሉኝ፡ ተሻላችሁ። *ዘፀአ፡ ፳፡ ፩፡፡ ፳፬፡ ፫፡ ፬፡፡ †ም፡ ፭፡ ፲፮፡ ፲፰፡፡

፳፤ ሕዝብም፡ መለሱ፡ አሉም። ጋኔን፡ አለብህ። ማን፡ ሊገልህ፡ ይሻል። ም፡ ፰፡ ፵፰፡ ፶፪፡፡

፳፩፤ መለሰ፡የሱስ፡አላቸውም። አንድ፡ ስራ፡ አደረግሁ፡ ሁላችሁም፡ ስለዚህ፡ አደነቃችሁ። ም፡ ፭፡ ፰፡ ፲፮፡፡

፳፪፤ ስለዚህ፡ሙሴ፡ግዝረት፡ሰጣችሁ፡(እርሱም፡ ከሙሴ፡ አይደለም፡ ነገር፡ግን፡ ካባቶች፡ ነው)። በሰንበትም፡፡ ሰውን፡ ትገዝራላችሁ። ዘፍ፡ ፲፯፡ ፲፡፡

፳፫፤ ሰውስ፡በሰንበት፡ ግዝረት፡የሚቀበል፡ከሆነ፡ የሙሴ፡ ሕግ፡ እንዳይፈረስ። እኔን፡ለምን፡ትነቅፉኛላችሁ፡ ሰውን፡ ሁለንትናውን፡ በሰንበት፡ ስለ፡ ፈወስሁ።

፳፬፤ በአድልዎ፡ አትፍረዱ፡ ነገር፡ግን፡ እውነተኛ፡ ፍርድ፡ ፍረዱ።

፳፭፤ ከየሩሳሌምም፡ ሰዎች፡ አሉ። ይህ፡አይደለምን፡ ይገሉት፡ ዘንድ፡ የሚሹት። ቍ፡ ፲፱፡፡

፳፮፤ እርሱም፡ እነሆ፡ፊት፡ ለፊት፡ ይናገራቸዋል፡ እርሳቸውም፡ ምንም፡ አይነግሩበትም። በውኑን፡ አወቁ፡ አለቆች፡ ይህ፡እውነተኛ፡ ክርስቶስ፡እንደ፡ሆነ።

፳፯፤ ነገር፡ ግን፡ ይህን፡አውቀናል፡ከወዴት፡እንደ፡ ሆነ። ክርስቶስ፡ ግን፡ በመጣ፡ ጊዜ፡ ማንም፡የሚያውቅ፡ የለም፡ ከወዴት፡ እንደ፡ ሆነ። ቍ፡ ፵፩፡፡

፳፰፤ የሱስም፡ ጮኸ፡ በመቅደስ፡ሲያስተምር፡ አለም፡ እኔን፡ ታውቃላችሁ። ከወዴትም፡ እንደ፡ ሆንሁ፡ ታውቃላችሁ። እኔ፡ በራሴ፡ የመጣሁ፡ አይደለሁም። ነገር፡ ግን፡ የላከኝ፡እውነተኛ፡ነው፡እላንት፡የማታውቁት።

፳፱፤ እኔ፡ ግን፡ አውቀዋለሁ፡ እኔ፡ ከርሱ፡ ነኝና፡ እርሱም፡ ልኮኛልና። ማቴ፡ ፲፩፡ ፳፯፡፡

፴፤ ስለዚህም፡ ሊይዙት፡ ወደዱ፡ ነገር፡ ግን፡ ማንም፡ እጁን፡ አልዘረጋበትም። ጊዜው፡ ገና፡ አልደረሰችምና። ም፡ ፰፡ ፳፡፡ ሉቃ፡ ፳፪፡ ፶፫፡፡

፴፩፤ ከሕዝቡም፡ ብዙ፡ አመኑበት፡ አሉም። ክርስቶስ፡ በመጣ፡ ጊዜ፡ በውኑ፡ ተአምራትን፡ ያደርጋል፡ ይህ፡ ካደረጋት፡ ተአምራት፡የሚስልጥ። ም፡ ፰፡ ፴፡፡

፴፪፤ ፈሪሳውያንም፡ ሕዝቡ፡ ይህነን፡ ስለርሱ፡ እንደ፡ያንጐረጐሩ፡ ሰሙ። ፈሪሳውያንም፡ የካህናትም፡ አለቆች፡ ሎላልትን፡ ሰደዱ፡ ሊይዙት።

፴፫፤ የሱስም፡ አላቸው። ገና፡ ጥቂት፡ ቀን፡ እኔ፡ ከላንት፡ ጋራ፡ ነኝ፡ ወደ፡ ላከኝ፡ እሔዳለሁ። ም፡ ፲፫፡ ፴፫፡፡

፴፬፤ ትሹኛላችሁ፡ አታገኙኝምም። እኔም፡ ወደለሁበት፡ እላንት፡ ትመጡበት፡ ዘንድ፡ አትችሉም። ም፡ ፰፡ ፳፩፡፡

፴፭፤ አይሁድም፡ እርሱ፡ በርሳቸው፡ አሉ። ይህ፡ ወዴት፡ ይሔድ፡ ዘንድ፡ አለው፡ እኛ፡እንዳናገኘው። ወይስ፡ በፅርዕ፡ አገር፡ ወደ፡ ተበተኑት፡ ይሔዳልን፡ የፅርዕን፡ ሰዎች፡ ሊያስተምር። የሐዋ፡ ፮፡ ፩፡፡

፴፮፤ ምንድር፡ነው፡ ይህ፡ ነገር፡ የሚለው። ትሹኛላችሁ፡አታገኙኝምን። እኔ፡ወደለሁበትም፡እላንት፡ መምጣት፡አይቻላችሁም።

፴፯፤ ከበዓሉም፡ በታላቁ፡ በኋለኛው፡ ቀን፡ቆመ፡ የሱስ፡ ጸራም፡ እንደሁ፡ ሲል። ማንም፡ የተጸማ፡ ቢኖር፡ ወደኔ፡ ይምጣና፡ ይጠጣ። ዘሌዋ፡ ፳፫፡ ፴፮፡፡ ራእ፡ ፳፪፡ ፲፯፡፡

፴፰፤ በኔ፡ *የሚያምን፡ መጽሐፍ፡ እንደለ፡የሕይወት፡ ወኃ፡ ፈሳሽ፡ ከሆዱ፡ ትፈሳለች። *መዝ፡ ፴፮፡ ፱፡ ፲፡፡ ኢሳ፡ ፲፪፡ ፫፡፡ ፵፱፡ ፫፡፡

፴፱፤ ይህነንም፡ማለቱ፡ስለ፡መንፈስ፡ቅዱስ፡ነው፡ በርሱ፡ ያመኑ፡ይቀበሉት፡ዘንድ፡ያላቸው። መንፈስ፡ ገና፡ አልመጣም፡ ነበርና፡ የሱስ፡ ገና፡ ስላልተመሰገነ። ዮኤል፡ ፫፡ ፩፡፡

፵፤ ከሕዝቡም፡ ብዙ፡ሰዎች፡ነገሩን፡በሰሙ፡ጊዜ፡ ይሉ፡ነበሩ።ይህ፡በውነት፡ነቢይ፡ነው። ዘዳግ፡ ፲፰፡ ፲፭፡፡

፵፩፤ ሌሎችም፡ ይሉ፡ነበሩ። ይህ፡ ክርስቶስ፡ ነው።

ሌሎች፡ ግን፡ ይሉ፡ ነበረ። በውኑ፡ ክርስቶስ፡ ከገሊላ፡ ይመጣልን። ም፡ ፩፥ ፵፮፡፡

፵፪፥ መጽሐፍ፡ይል፡የለምን፡ከዳዊት፡ ዘር፡ ቤተ፡ ልሔምም፡ ዳዊት፡ ከነበረባት፡ አገር፡ ክርስቶስ፡ እን ዲመጣ። መዝ፡ ፻፴፪፥ ፲፩፡፡ ሚክ፡ ፭፥ ፩፡፡ ማቴ፡ ፪፥ ፭፥ ፮፡፡

፵፫፥ በሕዝቡም፡መካከል፡ክርክር፡ ሆነ፡ ስለርሱ። ም፡ ፱፥ ፲፮፡፡

፵፬፥ ከርሳቸውም፡ ሰዎች፡ ሊይዙት፡ ይወዱ፡ ነበ ሩ፡ነገር፡ ግን፡ ማንም፡ እጁን፡ አላነሣበትም። ቍ፡ ፴፡፡

፵፭፥ ሎሌዎችም፡ ወደ፡ካህናቱ፡ አለቆች፡ ወደ፡ ፈ ሪሳውያንም፡ መጡ። እሊያም፡ አልዋቸው፡ለምን፡ አላመጣችሁት።

፵፮፥ መለሱ፡ሎሌዎች፡አሉም። ሰው፡ እንደሁ፡ከ ቶ፡አልተናገረም፡እንደዚህ፡ሰው። ማቴ፡ ፯፥ ፳፱፡፡

፵፯፥ ፈሪሳውያንም፡ መለሱላቸው፡ አልዋቸው ም። በውኑ፡ እላንተም፡ ደግሞ፡ ጠፋችሁ።

፵፰፥ ወይስ፡ ካለቆች፡ ከፈሪሳውያንም፡ አንድ፡ ያመነበትን፡ አለ።

፵፱፥ ይህ፡ ሕዝብ፡ ግን፡ ኦሪትን፡ የማያውቁ፡ እር ሳቸው፡ የተረገሙ፡ ናቸው።

፶፥ ኒቆዲሞስም፡ ወደርሱ፡ በሌሊት፡ የመጣው፡ አላቸው። እርሱም፡ ከርሳቸው፡ አንዱ፡ ነበር። ም፡ ፫፥ ፩፥ ፪፡፡

፶፩፥ ኦሪታችን፡ በሰው፡ ይፈርድለን፡ ከርሱ፡ አስቀ ድሞ፡ ሳይሰማ፡ ሳያውቅስ፡ ምን፡ እንደደረገ። ዘዳግ፡ ፩፥ ፲፮፡፡

፶፪፥ መለሱ፡ አሉትም። አንተም፡ደግሞ፡ ከገ ሊላ፡ ነህ። እኀ፡ እይም፡ ነቢይ፡ ከገሊላ፡ እንዳይነሣ። ቍ፡ ፵፩፡፡

፶፫፥ ሁሉም፡ኢያንዳንዱ፡ ወደ፡ ቤቱ፡ ሔደ።

ምዕራፍ፡ ፰፥

፩፥ የሱስም፡ ወደ፡ደብረ፡ ዘይት፡ ሔደ።

፪፥ ማልዶም፡ደግሞ፡ወደ፡ መቅደስ፡ ገባ። ሕዝብ ም፡ ሁሉ፡ወደርሱ፡ መጡ። ተቀምጦም፡ ያስተምራ ቸው፡ ነበር።

፫፥ ጸፎችም፡ ፈሪሳውያንም፡በምንዝር፡ የተያዘ፡ ሴት፡ወደርሱ፡ አመጡ፡በመካከልም፡ አቆምዋት። ዘፀአ፡ ፳፥ ፲፬፡፡

፬፥ አሉት። መምህር፡ ሆይ፡ ይህች፡ሴት፡ ተያዘች፡ ምንዝር፡ ስታደርግ።

፭፥ በኦሪትም፡ሙሴ፡አዘዘ፡እንደዚች፡ያሉችው፡ ትወገር፡ ዘንድ። አንተስ፡ እንጊዲህ፡ ምን፡ ትላለህ። ዘሌዋ፡ ፳፥ ፲፡፡

፮፥ ይህነንም፡ ሊፈትኑት፡ አሉ፡ የሚያጣሉበትን፡ ያገኙ፡ ዘንድ። የሱስ፡ ግን፡ ወደ፡ ታች፡ ዝቅ፡ አለ፡ በፃ ቱም፡ ጻፈ፡ በምድር፡ ላይ።

፯፥ እርሱንም፡ በመጠየቅ፡ በጸኑ፡ ጊዜ፡ቀና፡ አላቸ ውም። ከላንተ፡ ኀጢአት፡ የሌለበት፡ እርሱ፡ አስቀ ድሞ፡ በድንጊያ፡ ይውገራት።

፰፥ ደግሞም፡ ወደ፡ ታች፡ዝቅ፡ አለ፡ በምድር፡ ላይ ም፡ ጻፈ።

፱፥ እርሳቸው፡ ግን፡ ይህነን፡ በሰሙ፡ ጊዜ፡ ባሳባቸ ው፡ ከራሳቸው፡ ተዘለፉ፡ ኢያንዳንዱም፡ ወጡ። ከ ሽማግሌዎች፡ ጀምረው፡ እስከ፡ ኋለኞች። የሱስም፡ ብቻውን፡ ቀረ፡ ሴቲቱም፡ በማከል፡ ቁማ። ሮሜ፡ ፪፥ ፳፪፡፡

፲፥ የሱስም፡ ቀና። ማነንም፡ ባላየ፡ ጊዜ፡ ከሴቲቱ፡ በቀር፡ አላት። አንቺ፡ ሴት፡ የሚያሳጡሽ፡ የታሉ። የ ፈረደብሽ፡ የለምን።

፲፩፥ እርስዋም፡ አለች። አቤቱ፡ አንድ፡ ስንኳ። የ ሱሰም፡አላት። እኔም፡አልፈርድብሽም። ሒጅ፡ ከን ጊዲህ፡ወዲህም፡ደግመሽ፡*አትበድይ።*ም፡ ፭፥ ፲፬፡፡

፲፪፥ ደግሞም፡ተናገራቸው፡የሱስ፡ እንደሁ፡ሲል። እኔ፡ ነኝ፡ የዓለም፡ *ብርሃን። የሚከተለኝ፡ በጨለ ማ፡ አይሔድም። የሕይወት፡ ብርሃን፡ ይሆንለታል፡ እንጂ። *ኢሳ፡ ፵፱፥ ፮፡፡ ም፡ ፩፥ ፭፥ ፱፡፡

፲፫፥ ፈሪሳውያንም፡ አሉት። አንተ፡ለራስህ፡ትመ ሰክራለህ። ምስክርህ፡ እውነት፡ አይደለም።

፲፬፥ የሱስም፡መለሰ፡አላቸውም። እኔም፡ለራሴ፡ ብመሰክር፡ምስክሬ፡ እውነት፡ነው። ከወዴት፡ መጣ ሁ፡ አውቃለሁና፡ ወዴት፡ ዘንድስ፡ እሔዳለሁ። እላ ንተ፡ ግን፡ አታውቁም፡ ከወዴት፡ መጣሁ፡ ወዴት፡ ዘ ንድስ፡ እሔዳለሁ። ም፡ ፭፥ ፴፩፡፡

፲፭፥ እላንተ፡ የሥጋ፡ ፍርድ፡ ትፈርዳላችሁ። እኔ፡ በማንም፡ አልፈርድም።

፲፮፥ እኔም፡ብፈርድ፡ ፍርዴ፡እውነት፡ነው። እኔ፡ ለ ብቻዬ፡ አይደለሁምና። ነገር፡ ግን፡እኔ፡ የላከኝ፡ አብ፡ እንጂ። ቍ፡ ፳፱፡፡

፲፯፥ በኦሪታችሁም፡ደግሞ፡ ተጽፏዋል። የሁለት፡ ሰው፡ ምስክር፡ እውነት፡ እንደ፡ ሆነ። ዘዳግ፡ ፲፯፥ ፮፡፡ ም፡ ፲፱፥ ፲፭፡፡

፲፰፥ እኔ፡ ነኝ፡ ለራሴ፡ የምመሰክር። አብም፡ የላ ከኝ፡ ይመሰክርልኛል።

፲፱፥ አሉትም፡ አባትህ፡ ወዴት፡ ነው። መለሰ፡የሱ ስ፡አላቸውም። እኔንም፡ አታውቁ፡ አባቴንም። እኔ ንስ፡ ብታውቁኝ፡ አባቴንም፡ ደግሞ፡ ባወቃችሁ። ም፡ ፲፬፥ ፯፡፡

፳፥ ይህነን፡ ነገር፡ ተናገረ፡ በመዝገብ፡አጠገብ፡ እር ሱ፡ሲያስተምር፡በመቅደስ። ማንም፡አልያዘውም። ጊዜው፡ ገና፡ አልደረሰምና። ም፡ ፯፥ ፴፡፡ ሉቃ፡ ፳፪፥ ፶፫፡፡

፳፩፥ ደግሞም፡አላቸው፡የሱስ። እኔ፡እሔዳለሁ። ትሹኛላችሁ፡በኃጢአታችሁም፡ትሞታላችሁ። እ ኔ፡ ወደምሔድበት፡ እላንተ፡ ትመጡ፡ ዘንድ፡ አትች ሉም። ም፡ ፯፥ ፴፬፡፡ ም፡ ፲፫፥ ፴፫፡፡

፳፪፤ አይሁድም፡ አሉ። እርሱን፡ ራሱን፡ ይገላል፡
ማለቱ፡ እኔ፡ ወደምሔድበት፡ እላንተ፡ መምጣት፡
አትችሉም። ምዕ፡ ፯፡ ፴፭።።
፳፫፤ አላቸውም። እላንተ፡ከታች፡እኔም፡ ከላይ።
እላንተ፡ ከዚህ፡ ዓለም፡ እኔ፡ ከዚህ፡ዓለም፡አይደለ
ሁም።
፳፬፤ ስለዚህም፡ አልኋችሁ፡ በኃጢአታችሁ፡ እን
ድትሞቱ። እኔ፡ እንደ፡ ሆንሁ፡ ባታምኑ፡ በኃጢአታ
ችሁ፡ ትሞታላችሁና።
፳፭፤ አሉትም።አንተ፡ማነህ።የሱስም፡አላቸው።
እኔ፡ ነኝ፡ ያ፡ ከጥንት፡ ጀምሬ፡ እነግራችሁ፡ የነበርሁ።
፳፮፤ እጅግ፡ ነገር፡አለኝ፡ ስለላንተ፡የምናገረው፡የ
ምፈርድበትም። ነገር፡ግን፡ የላከኝ፡ እውነተኛ፡ነው።
ከርሱም፡ የሰማሁትን፡ ለዓለም፡ እናገራለሁ።
፳፯፤ አላወቁም፡ በዚህ፡ ነገር፡ ስለ፡ አብ፡ እንደላ
ቸው።
፳፰፤ ደግሞም፡ አላቸው፡ የሱስ። የሰውን፡ ልጅ፡
ከፍ፡ ከፍ፡ ባደረጋችሁት፡ ጊዜ፡ በዚያን፡ ጊዜ፡ ታውቃ
ላችሁ፡ እኔ፡ እንደ፡ ሆንሁ። ከራሴም፡እንዳች፡ እንደ
ልሰራ። ነገር፡ ግን፡ አባቴ፡ እንደሰተማረኝ፡ እንደሁ፡
እላለሁ። ምዕ፡ ፫፡ ፲፬።። ምዕ፡ ፲፪፡ ፴፪።።
፳፱፤ የላከኝም፡ እርሱ፡ ከኔ፡ ጋራ፡ ነው። አብ፡ብቻ
ዬን፡አይተወኝም። ሁልጊዜ፡ፈቃዱን፡ አደርጋለሁና።
ቍ፡ ፲፮።።
፴፤ እርሱም፡ ይህነን፡ ሲናገር፡ ብዙ፡ አመኑበት።
ምዕ፡ ፯፡ ፴፩።።
፴፩፤ የሱስም፡ ያመኑበትን፡አይሁድ፡ አለ። እላን
ተ፡ በነገሬ፡ ብትጸኑ፡ እላንተም፡ በውነት፡ ደቀ፡ መዛ
ሙርቴ፡ ናችሁ። ምዕ፡ ፲፭፡ ፲፬።።
፴፪፤ እውነትንም፡ ታውቃላችሁ፡ እውነትም፡አር
ነት፡ ያወጣችኋል።
፴፫፤ መለሱለት፡ አሉትም። እኛ፡ የአብርሃም፡ ል
ጆች፡ ነነ፡ ለማንም፡ ከቶ፡አልተገዛነም። አንተ፡ እንዴ
ት፡ ትላለህ፡ አርነት፡ ትወጣላችሁ። ማቴ፡ ፫፡ ፱።።
፴፬፤ መለሰ፡ የሱስ፡ አላቸውም። እውነት፡ እውነ
ት፡ እላችኋለሁ። ኃጢአት፡የሚያደርግ፡ሁሉ፡እርሱ፡
የኃጢአት፡ ባርያ፡ ነው። ሮሜ፡ ፮፡ ፲፮፡ ፳።።
፩፡ ዮሐ፡ ፫፡ ፰።።
፴፭፤ ባርያውም፡ በቤት፡ አይኖርም፡ ለዘላለም።
ልጅ፡ ግን፡ ለዘላለም፡ ይኖራል።
፴፮፤ ልጅም፡ ቢያወጣችሁ፡ በውነት፡ ጌቶች፡ ናች
ሁ። ሮሜ፡ ፮፡ ፲፰፡ ፳፪።።
፴፯፤ ፈጽሜ፡አወቅሁ፡የአብርሃም፡ልጆች፡እንደ፡
ሆናችሁ። ነገር፡ ግን፡ ልትገሉኝ፡ ትሻላችሁ። ነገሬ፡ በላ
ንተ፡ አይኖርምና።
፴፰፤ እኔ፡ ካባቴ፡ዘንድ፡ያየሁትን፡እናገራለሁ። እ
ላንተም፡ ካባታችሁ፡ ዘንድ፡ ያያችሁትን፡ ታደርጋላ
ችሁ።
፴፱፤ መለሱ፡ አሉትም። አባታችንስ፡ አብርሃም፡
ነው። የሱስም፡አላቸው። የአብርሃምስ፡ልጆች፡ብት
ሆኑ፡ የአብርሃምን፡ ስራ፡ በሰራችሁ።
፵፤ ነገር፡ግን፡ዛሬ፡ልትገሉኝ፡ ትሻላችሁ፡ *እውነት፡
የነገርኋችሁን፡ሰው፡ ከእግዚአብሔር፡ የሰማሁትን።
አብርሃም፡ እንዲህ፡ አላደረገም። *ምዕ፡ ፲፯፡ ፲፯።።
፵፩፤ እላንተ፡ ያባታችሁን፡ ስራ፡ ታደርጋላችሁ። አ
ሉትም። እኛስ፡ ከዝሙት፡ አልተወለድነም። ለኛስ፡
አንድ፡ አባት፡ አለን፡ እርሱም፡ *እግዚአብሔር።
ኤር፡ ፫፡ ፬።።
፵፪፤ አላቸው፡ የሱስ። እግዚአብሔርስ፡ አባታች
ሁ፡ቢሆን፡ በወደዳችሁኝ፡ ነበራችሁ። ከእግዚአብሔ
ር፡ወጥቼ፡መጥቻለሁና። እኔም፡ ከራሴ፡ የመጣሁ፡አ
ይደለሁም፡ እርሱ፡ ላከኝ፡ እንጂ።
፵፫፤ ምነው፡ቃሌን፡አታስተውሉ።ነገሬን፡መስማ
ት፡ አትችሉምና።
፵፬፤ *እላንተ፡ካባታችሁ፡ከሰይጣን፡ናችሁ፡ያባታ
ችሁንም፡ፈቃድ፡ታደርጉ፡ ዘንድ፡ ትሻላችሁ። ያ፡ †ገዳ
ይ፡ነበረ፡ከጥንት፡††በውነትም፡አልጸናም።እውነት፡
የለበትምና።ሐሰት፡በተናገረ፡ጊዜ፡ከራሱ፡ ይናገራል።
አሰተኛ፡ነውና፡ ያሰትም፡ አባት።
*፩፡ ዮሐ፡ ፫፡ ፰—፲።። †ዘፍጥ፡ ፫፡ ፬።።
††፪፡ ጴጥ፡ ፪፡ ፬።።
፵፭፤ እኔ፡ግን፡ እውነት፡ እናገራለሁና፡ አታምኑብ
ኝም።
፵፮፤ ማነው፡ ከላንተ፡ ስለ፡ ኃጢአት፡ የሚወቅሰ
ኝ።እውነትም፡የምናገር፡ ከሆንሁ፡ ለምን፡ አታምኑ
ብኝ። ፪፡ ቆሮ፡ ፭፡ ፳፩።። ፩፡ ጴጥ፡ ፪፡ ፳፪።።
፵፯፤ ከእግዚአብሔር፡ የሆነ፡ የእግዚአብሔርን፡
ቃል፡ይሰማል። ስለዚህ፡ እላንተ፡ አትሰሙም፡ ከእግ
ዚአብሔር፡ አይደላችሁምና። ምዕ፡ ፲፰፡ ፴፯።።
፩፡ ዮሐ፡ ፬፡ ፮።።
፵፰፤ መለሱ፡አይሁድ፡አሉትም።እኛ፡መልካም፡
እንል፡የለነምን፡ ሳምራዊ፡እንደ፡ሆንህ፡ ሰይጣንም፡
አለብህ። ምዕ፡ ፯፡ ፳።።
፵፱፤ መለሰ፡የሱስ፡አለም።እኔስ፡ ሰይጣን፡ የለብ
ኝም።ነገር፡ግን፡አባቴን፡አከብራለሁ፡ እላንተም፡ትን
ቁኛላችሁ።
፶፤ እኔም፡*ክብሬን፡አልሻም። የሚሻ፡ የሚፈርድ
ም፡አለ። *ምዕ፡ ፭፡ ፳፫፡ ፵፩።።
፶፩፤ እውነት፡እውነት፡እላችኋለሁ።ማንም፡ ቃሌ
ን፡ *ቢጠብቅ፡ ሞትን፡ አያይም፡ ለዘላለም።
*ምዕ፡ ፮፡ ፵፡ ፵፯።።
፶፪፤ አይሁድም፡አሉት።አሁን፡ አወቅነ፡ ሰይጣን፡
እንዳለብህ።አብርሃም፡ሰንኳ፡ሞተ፡ *ነቢያትም። አ
ንተም፡ትላለህ።ማንም፡ቃሌን፡ቢጠብቅ፡ ሞትን፡ አ
ይቀምሰውም፡ ለዘላለም። *ዘካ፡ ፩፡ ፭።።
፶፫፤ በውኑ፡ አንተ፡ ካባታችን፡ ካብርሃም፡ ከሞተ
ው፡ ትበልጣለህ። ነቢያትም፡ ሞቱ። አንተ፡ ራስህን፡
ማነን፡ ታደርጋለህ።

፶፬፡ መለሰ፡የሱስ፡አለም።እኔም፡ራሴን፡ባከብር፡
ክብሬ፡አንዳች፡አይሆንም።አባቴ፡ነው፡የሚያከብረ
ኝ። እላንት፡ የምትሉት፡ አምላካችሁ፡እንደ፡ ሆነ።

፶፭፡ አታውቁትም፡ ስንኳ። እኔ፡ ግን፡ አውቀዋለ
ሁ።አላውቀውምም፡ብል፡እንደላንት፡ አሰተኛ፡ ሆን
ሁ።ነገር፡ ግን፡አውቀዋለሁ፡ ቃሉንም፡ እጠብቃለሁ።
ምዕ፡ ፯፡ ፳፱፡፡

፶፮፡ አብርሃም፡ አባታችሁ፡ ተመኘ፡ ቀኔን፡ ያይ፡ዘ
ንድ። አየም፡ ደስም፡ አለው። ዕብ፡ ፲፩፡ ፲፫፡፡

፶፯፡ አይሁድም፡አሉት። ገና፡አምሳ፡ አመት፡ አል
ሆነህ፡አንተምን፡አብርሃምን፡ አየህ። ሉቃ፡ ፫፡ ፳፫፡፡

፶፰፡ አላቸው፡የሱስ።እውነት፡እውነት፡እላችኋለ
ሁ።አብርሃም፡ሳይወለድ፡እኔ፡ነኝ። ኢሳ፡ ፵፫፡ ፲፫፡፡

፶፱፡ *ደንጊያም፡አነሡ፡ሊወግሩት።የሱስ፡ ግን፡ ተ
ሠወረ፡ከመቅደስም፡ ወጣ፡ በመካከላቸውም፡ አለ
ፈ፡እንደሁም፡ ሔደ። *ዘሌዋ፡ ፳፬፡ ፲፮፡፡

ምዕራፍ፡ ፱፡

፩፡ እርሱም፡ ሲያልፍ፡ ሰው፡ አየ፡ ዕውር፡ የሆነ፡ ከ
መወለዱ፡ ጀምሮ። ሉቃ፡ ፲፫፡ ፪፡ ፬፡፡

፪፡ ደቀ፡ መዛሙርቱም፡ ጠየቁት፡ እንዲህ፡ ሲሉ።
መምህር፡ሆይ፡ ማነው፡ የበደለ። እርሱን፡ ወይስ፡አባ
ቶቹ፡ዕውር፡ ሁኖ፡ ይወለድ፡ ዘንድ። ምዕ፡ ፲፩፡ ፬፡፡

፫፡ መለሰ፡የሱስ፡አለም። ይህም፡ አልበደለም፡ አ
ባቶቹ፡ ነገር፡ ግን፡ የእግዚአብሔር፡ ስራ፡ ልትገለጥበ
ት፡ነው።

፬፡ ይገባኛል፡የላከኝን፡ስራ፡አደርግ፡ ዘንድ፡ቀን፡ ሳ
ለ።ሌሊት፡ይመጣልና፡ ማንም፡ ስራ፡ ያደርግ፡ ዘንድ፡
የማይቻልበት። ምዕ፡ ፭፡ ፲፯፡፡

፭፡ በዓለም፡ሳለሁ፡ እኔ፡ የዓለም፡ ብርሃን፡ ነኝ።
ምዕ፡ ፩፡ ፱፡፡ ምዕ፡ ፰፡ ፲፪፡፡

፮፡ ይህነንም፡ብሎ፡በመሬት፡ ላይ፡ ተፋ፡ በምራቁ
ም፡ጭቃ፡ አደረገ፡ የውሩንም፡ ዓይን፡ ጭቃውን፡ ቀ
ባው።

፯፡ አለውም።ሒድ፡*በሰሊሆም፡ መጠመቂያ፡ ታ
ጸብ። ትርጓሜዋ፡ የተላከች፡ የምትሆን። ሒደም፡
†ታጸበ፡ኢያየም፡ ተመለሰ። *ነህም፡ ፫፡ ፲፭፡፡
ኢሳ፡ ፰፡ ፮፡፡ †፪፡ ነገሥ፡ ፭፡ ፲፡ ፲፬፡፡

፰፡ ጎረቤቶቹ፡ግን፡ቀድሞም፡የሚያውቁት፡ ዕው
ር፡እንደ፡ ሆነ፡ አሉ። ይህ፡ ተቀምጦ፡ ይለምን፡ የነበረ
ው፡ አይደለምን።

፱፡ ሌሎችም፡አሉ።እርሱ፡ ነው። ሌሎችም፡ አሉ።
እርሱ፡ ይመስለዋል።እርሱ፡ግን፡አለ።እኔ፡ነኝ።

፲፡ አሉትም። ዓይንህ፡ እንዴት፡ ተከፈተ።

፲፩፡ ያም፡መለሰ፡ አለም። የሱስ፡ የሚሉት፡ ሰው፡
ጭቃ፡አደረገ፡ዓይኔንም፡ቀባኝ፡አለኝም።ወደ፡ሰሊሆ
ም፡መጠመቅያ፡ሒድ፡ ታጸብም። ሔድሁም፡ ታጸብ
ሁም፡አየሁም።

፲፪፡ አሉትም። ያ፡ ወዴት፡ ነው። አለም። አላው
ቅም።

፲፫፡ ያነንም፡ቀድሞ፡ዕውር፡የነበረውን፡ ወሰዱት፡
ወደ፡ ፈሪሳውያንም፡ ይዘውት፡ መጡ።

፲፬፡ ሰንበትም፡ነበረ፡የሱስ፡ጭቃ፡ ቀብቶ፡ ዓይኑን፡
በከፈተው፡ጊዜ። ምዕ፡ ፭፡ ፱፡፡

፲፭፡ ፈሪሳውያንም፡ደግሞ፡ ጠየቁት፡ እንዴት፡ እ
ንዳየ። እርሱም፡አላቸው። ባይኔ፡ ላይ፡ጭቃ፡ አደረገ፡
ታጸብሁም፡ አየሁም።

፲፮፡ ከፈሪሳውያንም፡ ሰዎች፡ አሉ። ይህ፡ ሰው፡ከ
እግዚአብሔር፡ አይደለም፡ ሰንበትን፡ አይጠብቅም
ና።ሌሎችም፡አሉ። እንዴት፡ይቻላል፡ *ኃጢአተኛ፡ሰ
ው፡ይህነን፡ተአምራት፡ ያደርግ፡ ዘንድ። በመካከላቸ
ውም፡ †ፀብ፡ሆነ። *ቍ፡ ፹፩፡ ፹፫፡፡ †ምዕ፡ ፯፡ ፵፫፡፡

፲፯፡ ደግሞም፡ ዕውሩን፡ አሉት። አንተ፡ ስለርሱ፡
ምን፡ትላለህ፡ዓይንህን፡ ከፍቶዋልና። እርሱም፡ መ
ለሰ፡ አለም። ነቢይ፡ ነው። ምዕ፡ ፬፡ ፲፱፡፡

፲፰፡ አይሁድም፡አላመኑም፡ ዕውር፡ እንደ፡ ነበረ፡
እንዳየም።የዚያን፡ያየውን፡ አባቶች፡ እስኪጸሩ፡ ድ
ረስ።

፲፱፡ ጠየቋቸውም፡ እንዲህ፡ ሲሉ። ይህን፡ ልጃች
ሁ፡ነው፡እላንት፡የምትሉት፡ዕውር፡ሁኖ፡ተወለደ። ዛ
ሬስ፡ እንዴት፡ አየ።

፳፡ አባቶቹም፡መለሱላቸው፡አሉም።እናውቃለ
ን፡ይህ፡ልጃችን፡ እንደ፡ ሆነ፡ ዕውር፡ ሁኖም፡ እንደ፡ ተ
ወለደ።

፳፩፡ ዛሬ፡ግን፡እንዴት፡እንዳየ፡አናውቅም። ወይ
ስ፡ዓይኑን፡የከፈተው፡ ማነው፡ እኛ፡ አናውቅም። እ
ርሱ፡ፍጹም፡ጕልማሳ፡ነው፡ጠይቁት።እርሱ፡ ስለ፡ ራ
ሱ፡ይናገራል።

፳፪፡ ይህነን፡አሉ፡ አባቶቹ፡ አይሁድን፡ ይፈሩ፡ ነበ
ሩና።አይሁድ፡አዘው፡ነበሩና፡ማንም፡ሰው፡በርሱ፡ ቢ
ያምን፡ክርስቶስ፡እንደ፡ሆነ፡ከመሰጊድ፡ እንዲወጣ።
ምዕ፡ ፲፪፡ ፵፪፡፡

፳፫፡ ስለዚህ፡ አሉ፡ አባቶቹ። እርሱ፡ ፍጹም፡ ጕል
ማሳ፡ ነው፡ ጠይቁት።

፳፬፡ ሁለተኛም፡ዕውር፡የነበረውን፡ ሰው፡ ጸሩት፡
አሉትም። *ለእግዚአብሔር፡ ምስጋና፡ ስጥ። እኛ፡ እ
ናውቃለን፡ ይህ፡ ሰው፡ ኃጢአተኛ፡ እንደ፡ ሆነ።
ኢያ፡ ፯፡ ፲፱፡፡

፳፭፡ ያም፡መለሰ፡አለም።እርሱ፡ ኃጢአተኛ፡እን
ደ፡ሆነ፡አላውቅም። እኔ፡ አንድ፡ ነገር፡ አውቃለሁ። ዕ
ውር፡እንደ፡ ነበርሁ፡ አሁንም፡ እኔ፡ እንዳይ።

፳፮፡ ደግሞም፡አሉት።ምን፡አደረገልህ፡ እንዴት
ስ፡ ዓይንህን፡ ከፈተልህ።

፳፯፡ መለሰላቸው፡አላቸውም።አንድግዜ፡ነገርኋ
ችሁ፡ አልሰማችሁምም። ለምን፡ ትሻላችሁ፡ ደግሞ፡
ትሰሙ፡ዘንድ። ወይስ፡ እላንትምን፡ትወዳላችሁ፡ ደ
ቀ፡ መዛሙርቱ፡ ትሆኑለት፡ ዘንድ።

፳፰፤ ሰደቡትም፡አሉትም። አንተ፡ የዚያ፡ ደቀ፡ መዝሙር፡ነኽ። እኛ፡ግን፡የሙሴ፡ደቀ፡ መዛሙርት፡ነን።

፳፱፤ እኛ፡እናውቃለን፡ እግዚአብሔር፡ ሙሴን፡እንዲ፡ተናገረ። ይህን፡ግን ፡ እናውቅም፡ከወዴት፡እንደ፡ሆነ።

፴፤ ያ፡ሰው፡መለሰ፡ አላቸውም ። ይህም፡ ድንቅ፡ ነው፡ ከወዴት ፡ እንደ፡ ሆነ ፡ ሳታውቁት፡ ዓይኔን ፡ የከፈተኝ።

፴፩፤ እኛም፡ እናውቃለን ፡ *እግዚአብሔር ፡ ኃጢአተኞችን፡እንደይሰማ። ነገር፡ ግን፡ አንድ፡ እግዚአብሔርን፡የሚፈራ፡ቢኖር፡ ፈቃደ ንም፡ የሚያደርግ፡ ያነን፡ ይሰማዋል። *ኢሳ፡ ፩፤ ፲፭፡፡ ምሳ፡ ፲፭፤ ፳፱፡፡

፴፪፤ ከዓንት፡አልተሰማም፡ማንም፡ዕውር፡ ሁኖ፡ የተወለደውን፡ ዓይን፡ እንደ፡ ከፈተ።

፴፫፤ ይህስ፡ ከእግዚአብሔር፡ ባይሆን፡ ምንም፡ ያደርግ፡ ዘንድ፡ ባልቻለም። ቍ፡ ፲፯፡፡

፴፬፤ መለሱ፡አሉትም። አንተ፡ሁለንትናህ፡በኃጢአት፡ተወለድህ፡አንተምን፡ እኛን፡ ታስተምረናለህ። ወደ፡ ሜደም፡ አወጡት።

፴፭፤ የሱስም፡ሰማ፡ወደ፡ሜዳ፡ እንደወጡት። አግኝውም፡አለው። አንተ፡በእግዚአብሔር፡ልጅ፡ታምናለህን። ምዕ፡ ፯፤ ፵፡፡

፴፮፤ ያም፡መለሰ፡አለም። ጌታ፡ሆይ፡ ማነው፡ እርሱ፡ አምንበት፡ ዘንድ።

፴፯፤ የሱስም፡አለው። እነሆ፡አየኸው፡ ካንተም፡ ጋራ፡ የሚናገረው፡ እርሱ፡ ነው። ምዕ፡ ፬፤ ፳፮፡፡

፴፰፤ እርሱም፡ አለ ። አምናለሁ፡ አቤቱ ። ሰገደለትም።

፴፱፤ የሱስም፡ አለ ። እኔ፡ ለፍርድ፡ ወደዚህ፡ ዓለም፡መጣሁ። የማያዩት፡ያዩ፡ዘንድ፡ የሚያዩትም፡ ይታወሩ፡ ዘንድ። ማቴ፡ ፲፫፤ ፲፫፡፡

፵፤ ከፈሪሳውያንም፡ሰዎች፡ከርሱ፡ጋራ፡የነበሩ፡ ይህነን፡ሰሙ፡አሉትም። እኛምን፡ደግሞ፡ ዕውራን፡ነን።

፵፩፤ አላቸው፡የሱስ። ዕውራንስ፡ ብትሆኑ፡ ኃጢአትም፡ባልሆነባችሁም፡ነበረ። አሁን፡ግን፡ ትላላችሁ፡እናያለን ። ስለዚህ፡ኃጢአታችሁ ፡ ጸንታ ፡ ትኖራለች። ምዕ፡ ፲፭፤ ፳፬፡፡

ምዕራፍ፡ ፲፤

፩፤ እውነት፡እውነት፡እላችኋለሁ። ወደ፡ በጎች፡ ስፍራ፡በደጅ፡ያልገባ፡በሌላም፡ መንገድ፡ የሚሔድ፡ እርሱ፡ ሌባ፡ ወንበዴም፡ ነው።

፪፤ በደጅ ፡ ግን፡ የሚገባ፡ እርሱ ፡ የበጎች ፡ ጠባቂ፡ ነው።

፫፤ ለርሱ ፡ በረኛው፡ ይከፍትለታል፡ በጎችም፡ ቃሉን፡ ይሰሙታል። በጎችንም፡ በየስማቸው፡ ይጠራቸዋል፡ያወጣቸዋልም።

፬፤ በጎችንም፡ ባወጣ፡ጊዜ፡ በፊታቸው፡ ይሔዳል። በጎቹም፡ ይከተሉታል ፡ ቃሉን፡ ያውቃሉና።

፭፤ ለሌላውን፡ግን፡አይከተሉትም፡ከርሱ፡ይሸሻሉ፡ እንጂ፡ የሌሎችን፡ ቃል፡ አያውቁምና።

፮፤ ይህነን፡ምሳሌ፡አላቸው፡የሱስ። እርሳቸው፡ ግን፡ ይነግራቸው፡ የነበረውን፡ አላስተዋሉም።

፯፤ የሱስም፡ደግሞ፡አላቸው። እውነት፡ እውነት፡ እላችኋለሁ። እኔ፡ የበጎች፡ ደጅ፡ እንደ፡ ሆንሁ።

፰፤ በኔ ፡ በፊት፡ የመጡ፡ ሁሉ ፡ እርሳቸው፡ ሌቦች፡ ወንበዴችም፡ናቸው። ነገር፡ ግን፡በጎች ፡ አልሰሙዋቸውም። እር፡ ፳፫፤ ፪፡፡

፱፤ ደጁ፡እኔ፡ነኝ። ማንም፡በኔ፡የገባ፡ ይድናል፡ ይገባልም፡ ይወጣልም፡ መሰማርያም ፡ ያገኛል።

፲፤ ሌባው፡ አይመጣም፡ ሊሰርቅ፡ እንጂ፡ ሊያርድም፡ ሊገልም። እኔ፡ መጣሁ፡ ሕይወት ፡ ሊሆንላቸው፡ በትርፍም፡እንዲ፡ሆንላቸው። መዝ፡ ፳፫፤ ፩፡፡

፲፩፤ እኔ፡ነኝ፡ቸር፡*ጠባቂ። ቸር፡ጠባቂ፡ ራሱን፡ ስለ፡ በጎቹ፡ይለውጣል። *ኢሳ፡ ፵፤ ፲፩፡፡ ሕዝ፡ ፴፬፤ ፲፩፤—፳፫፡፡

፲፪፤ ብንደኛ፡ግን፡ጠባቂም፡ ያይደለ፡በጎቹ፡ የርሱ፡ ያይደሉ። ጅብ፡ሲመጣ፡ባየ፡ጊዜ፡ በጎችን፡ ትቶ፡ ይሸሻል፡ ጅብም፡ ይነጥቃቸዋል፡ በጎችንም ፡ ይበትናል። *ኢሳ፡ ፵፤ ፲፩፡፡ ሕዝ፡ ፴፯፤ ፳፬፡፡

፲፫፤ ብንደኛ ፡ ግን፡ ይሸሻል ፡ የተገዛ፡ ነውና፡ ለበጎችም፡አያዝንም።

፲፬፤ እኔ፡ነኝ፡ቸር፡ጠባቂ፡በጎቼንም፡ አውቃለሁ፡ በጎቼም፡ ያውቁኛል። ፪፡ ጢሞ፡ ፪፤ ፲፱፡፡

፲፭፤ አብ፡እኔን ፡ እንደ ያውቀኝ፡ እኔም፡ አብን፡ አውቃለሁ። ራሴንም፡ስለ፡በጎች፡ እለውጣለሁ። ማቴ፡ ፲፩፤ ፳፯፡፡

፲፯፤ ደግሞም፡*ሌሎች፡በጎች፡አሉኝ፡ ከዚህ፡ መንጋ፡ያይደሉ። አመጣቸውም፡ ዘንድ፡ጊዜ፡አለኝ፡ ቃሌንም፡ይሰሙኛል። መንጋውም፡ አንድ፡ ይሆናል፡ ጠባቂውም፡ አንድ። *ሕዝ፡ ፴፯፡ ፴፩፡፡ ዘካ፡ ፲፱፤ ፱፡፡

፲፯፤ ስለዚህ፡አብ፡ ይወደኛል፡ እኔ፡ ነፍሴን፡ እሰጣለሁና፡ ደግሞ፡ እወስዳት፡ ዘንድ። ኢሳ፡ ፶፫፤ ፲፡፡

፲፰፤ ማንም፡ከኔ፡አይወስዳትም፡ ነገር፡ግን፡ እኔ፡ በፈቃደ፡እሰጣታለሁ። ለኔ፡ችሎት፡ አለኝ፡ እሰጣት፡ ዘንድ፡ደግሞም፡ችሎት፡ አለኝ፡ *እወስዳት፡ ዘንድ። ይህነን፡ትእዛዝ፡ ካባቴ፡ ተቀበልሁ። *ምዕ፡ ፭፤ ፳፮፡፡

፲፱፤ በአይሁድም፡መካከል፡ደግሞ፡ ፀብ፡ ሆነ፡ ስለ ዚህ፡ነገር። ምዕ፡ ፯፤ ፵፫፡፡ ፱፡ ፲፮፡፡

፳፤ ከርሳቸውም፡ ብዙው፡አሉ። በርሱ፡ጋኔን፡አድሮበታል ፡ ፈጽሞም ፡ አበደ ። ለምን ፡ ታደምጹታላችሁ።

፳፩፤ ሌሎችም፡አሉ። ይህ፡ነገር፡የእብድ፡ነገር፡አይደለም። በውኑ፡ጋኔን፡የዕውራንን፡ዓይን፡ ይከፍት፡ ዘንድ፡ ይችላል። መዝ፡ ፻፵፯፤ ፰፡፡

፳፪፤ የማደሰም፡በዓል፡በየሩሳሌም፡ ነበር፡ ክረምትም፡ ነበረ።

፳፫፡ የሱስም፡በመቅደስ፡ ይሔድ፡ ነበረ፡ በስሎሞን፡ደጅ። የሐዋ፡ ፫፡ ፲፩።

፳፬፡ አይሁድም፡ ከበቡት፡ አሉትም። እስከ፡ መቼ፡ድረስ፡ ስውነታችነን፡ ታስጨንቀናለህ። አንተ፡ ክርስቶስ፡ እንደ፡ ሆንህ፡ገልጠህ፡ንገረን።

፳፭፡ መለሰላቸው፡ የሱስ፡ አላቸውም። ፈጽሜ፡ ነገርኋችሁ፡አታምኑምም። እኔ፡የማደርገው፡ ማድረግ፡ ባባቴ፡ ስም፡ እርሱ፡ ይመሰክርልኛል። ም፡ ፭፡ ፴፮።

፳፮፡ እላንት፡ግን፡አታምኑም፡ከበጎቼ፡ አይደላችሁምና፡ እንደልኋችሁ። ም፡ ፰፡ ፵፭።

፳፯፡ በጎቼ፡ቃሌን፡ይሰማሉ።እኔም፡አውቃቸዋለሁ፡እርሳቸውም፡ ይከተሉኛል። ም፡ ፰፡ ፵፯።

፳፰፡ እኔም፡ የዘላለም፡ ሕይወት፡ እሰጣቸዋለሁ። ለዘላለምም፡ አይጠፉም፡ማንም፡ከጁ፡ አይነጥቃቸውም። ም፡ ፫፡ ፲፭። ፲፯፡ ፱።

፳፱፡ አባቴ፡እርሳቸውን፡የሰጠኝ፡ከሁሉ፡ ይበልጣል። ማንም፡አይችልም፡ ካባቴ፡ እጅ፡ ይነጥቃቸው፡ ዘንድ። ም፡ ፲፬፡ ፳፰።

፴፡ እኔና፡ አብ፡ አንድ፡ ነን። ም፡ ፭፡ ፳፫። ፩፡ ዮሐ፡ ፭፡ ፯።

፴፩፡ አይሁድም፡ ደግሞ፡ ደንጊያ፡ አነሡ፡ ይወግሩት፡ ዘንድ።

፴፪፡ የሱስም፡መለሰላቸው፡አላቸውም። መልካም፡ብዙ፡ስራ፡ካባቴ፡ዘንድ፡አሳየኋችሁ። ስለ፡ማናቸው፡ ስራ፡ ከርሳቸው፡ ትወግሩኛላችሁ።

፴፫፡ አይሁድም፡መለሱለት፡እንደዚህ፡ሲሉ። ስለ፡መልካም፡ስራህ፡የምንወግርህ፡አይደለነም፡ ስለ፡መሳደብህ፡እንጂ። አንተም፡ሰው፡ ስትሆን፡ ራስህን፡ አምላክ፡ ታደርጋለህና። ም፡ ፭፡ ፲፰።

፴፬፡ የሱስም፡ መለሰላቸው፡ አለም። በኦሪታችሁ፡የተጻፈ፡አይደለምን። *እኔ፡አልሁ፡አማልክት፡ እንደ፡ ሆናችሁ። *መዝ፡ ፹፪፡ ፮።

፴፭፡ እሊያንም፡የእግዚአብሔር፡ነገር፡ የነበረባቸውን፡አማልክት፡ካላቸው፡መጽሐፍ፡ ይፈታ፡ ዘንድ፡ አይቻልም። ም፡ ፭፡ ፲፯—፳።

፴፮፡ አብ፡ የቀደሰውን፡ ወደ፡ ዓለምም፡ የላከውን፡ እንዴት፡ ትላላችሁ፡ ትሳድባለህ፡ የእግዚአብሔር፡ ልጅ፡ ነኝ፡ ስላልሁ።

፴፯፡ ያባቴን፡ ስራ፡ባልሰራ፡አትመኑብኝ።

፴፰፡ ባደርግም፡በኔም፡ባታምኑ፡ በስራዬ፡ እመኑ። እንድታውቁ፡እንድታምኑም፡ አብ፡በኔ፡እንዳለ፡እኔም፡በአብ።

፴፱፡ ደግሞም፡ሊይዙት፡ እሹ፡ከጃቸውም፡ አመለጠ። ም፡ ፰፡ ፶፱። ሉቃ፡ ፬፡ ፴።

፵፡ ደግሞም፡ ወደ፡ ዮርዳኖስ፡ ማዶ፡ ሔደ፡ ዮሐንስ፡ቀድሞ፡ያጠምቅበት፡ወደ፡ነበረው፡ስፍራ። ከዚያም፡ ተቀመጠ። ም፡ ፩፡ ፳፰።

፵፩፡ ብዙ፡ሰዎችም፡ ወደርሱ፡ መጡ፡ አሉም። ዮሐንስ፡ አንዲት፡ ስንኳ፡ ተአምራት፡ አላደረገም። ነገር፡ግን፡ ዮሐንስ፡ ስለዚህ፡ የተናገረው፡ ሁሉ፡ እውነት፡ ነው።

፵፪፡ ከዚያም፡ ብዙ፡ አመኑበት።

## ምዕራፍ፡ ፲፩፡

፩፡ አንድ፡ሰውም፡ነበረ፡ የታመመ፡ ስሙን፡ አልዓዛር፡የሚሉት። ከቢታንያ፡*ከማርያም፡ከትዋም፡ ከማርታ፡ አገር። *ሉቃ፡ ፲፡ ፴፰፡ ፴፱።

፪፡ ይህችም፡ማርያም፡ጌታን፡ሽቱ፡የቀባችው፡እግሩንም፡ በጸጕርዋ፡ ያበሰችው፡ ናት። የታመመውም፡ አልዓዛር፡ ወንድምዋ፡ ነበር። ም፡ ፲፪፡ ፫።

፫፡ እኅቶቹም፡ወደርሱ፡ላኩ፡እንደዚህ፡ሲሉ። ጌታ፡ሆይ፡ እነሆ፡ የምትወደው፡ ታምሟል።

፬፡ የሱስም፡ በሰማ፡ጊዜ፡ አለ። ይህ፡ ደዌ፡ ለሞት፡ አይደለም፡ ነገር፡ ግን፡ ስለ፡ እግዚአብሔር፡ ምስጋና፡ ነው። የእግዚአብሔር፡ልጅ፡በርሱ፡ይመሰገን፡ ዘንድ። ም፡ ፱፡ ፫።

፭፡ የሱስም፡ማርታን፡ይወድ፡ ነበር፡ እትዋንም፡ አልዓዛርንም።

፮፡ እንደ፡ ታመመም፡ በሰማ፡ ጊዜ፡ የዚያን፡ ጊዜ፡ ሁለት፡ ቀን፡ ተቀመጠ፡ በነበረበት፡ ስፍራ።

፯፡ ከዚህም፡በኋላ፡ደቀ፡መዛሙርቱን፡አላቸው። ኑ፡ ወደ፡ ይሁዳ፡ ምድር፡ ደግሞ፡ እንሒድ።

፰፡ ደቀ፡መዛሙርቱም፡ አሉት። መምህር፡ ሆይ፡ ዛሬ፡አይሁድ፡ሊወግሩህ፡ይሹ፡ነበሩ። ደግመህን፡ወደ፡ ዚያ፡ ትሔዳለህ። ም፡ ፲፡ ፴፩።

፱፡ መለሰ፡ የሱስ፡ አላቸውም። ቀኑ፡ አሥራ፡ሁለት፡ሰዓት፡አይደለምን። ማንም፡በቀን፡ ቢሔድ፡ አይሰናከልም፡ የዚህን፡ ዓለም፡ ብርሃን፡ ያያልና። ም፡ ፱፡ ፬፡ ፭።

፲፡ ማንም፡በሌት፡ግን፡ቢሔድ፡ ይሰናከላል፡ ብርሃን፡ የለበትምና። ም፡ ፲፪፡ ፴፭።

፲፩፡ ይህነን፡አለ፡ከዚህም፡በኋላ፡ አላቸው። አልዓዛር፡ወዳጃችን፡*ተኝትዋል፡ነገር፡ግን፡ እሔዳለሁ፡ እስነሣው፡ ዘንድ። *ማቴ፡ ፱፡ ፳፬።

፲፪፡ ደቀ፡መዛሙርቱም፡አሉ። ጌታ፡ሆይ፡ተኝቶስ፡ እንደ፡ሆነ፡ ይድናል።

፲፫፡ የሱስም፡አለ፡ስለ፡ ሞቱ። እርሳቸው፡ ግን፡ መለሰላቸው፡ስለ፡እንቅልፍ፡ መተኛት፡ያላቸው።

፲፬፡ የዚያን፡ጊዜም፡በግልጽ፡አላቸው። አልዓዛር፡ ሞተ።

፲፭፡ እኔም፡ደስ፡ይለኛል፡ስለላንት፡ከዚያ፡እንዳልነበርሁም፡እንድታምኑ። ነገር፡ግን፡ኑ፡ እንሒድ፡ ወደርሱ።

፲፮፡ ቶማስም፡ ዲዲሞስ፡ የሚሉት፡ ለባልንጀሮቹ፡ለደቀ፡መዛሙርት፡አለ። እኛም፡እንሒድ፡ከርሱ፡ ጋራ፡ እንሞት፡ ዘንድ። ም፡ ፳፡ ፳፬።

፲፯፤ የሱስም፡መጣ፡ላልዓዛርም፡ አራት፡ ቀን፡ሁኖት፡በመቃብር፡አገኘ።

፲፰፤ ቢታንያም፡ ለየሩሳሌም፡ቅርብ፡ ነበረች፡ አሥራ፡ አምስት፡ ምዕራፍ፡ ያህል።

፲፱፤ ከአይሁድም፡ብዙ፡ወደ፡ ማርታና፡ ወደ፡ ማርያም፡ መጡ፡ ሊያጽናንዋቸው፡ ስለ፡ ወንድማቸው።

፳፤ ማርታም፡ በሰማች፡ጊዜ፡ የሱስ፡ እንደ፡ መጣ፡ ልትቀበለው፡ወጣች። ማርያም፡ግን፡ ወደ፡ቤት፡ ተቀምጣ፡ ነበረች። ሉቃ፡ ፲፤ ፴፱፤ ፵፤

፳፩፤ ማርታም፡ለየሱስ፡ አለች። ጌታ፡ ሆይ፡ ከዚህስ፡ በኖርህ፡ ወንድሜ፡ ባልሞተም።

፳፪፤ ነገር፡ግን፡ዛሬ፡ ደግሞ፡ አውቃለሁ፡ ከእግዚአብሔር፡የለምንኸውን፡ሁሉ፡ እግዚአብሔር፡ እንዲሰጥህ።

፳፫፤ የሱስም፡ አላት። ወንድምሽ፡ ይነሣል።

፳፬፤ ማርታም፡አለችው ። እኔ፡ አውቃለሁ፡ በትንሣኤ፡ *እንዲነሣ፡ በኋለኛው፡ ቀን። *ምዕ፡ ፭፤ ፳፱፤ የሐዋ፡ ፳፬፤ ፲፭፡፡

፳፭፤ የሱስም፡አላት።እኔ፡ነኝ፡ ትንሣኤ፡ሕይወትም።ያመነብኝ፡ ቢሞትም፡ ይድናል።

፳፮፤ ሕያውም፡ የሆነ፡ሁሉ፡ ያመነብኝመ፡ ለዘላለም፡ አይሞትም። ይህን፡ ታምኘለሽን።

ምዕ፡ ፮፤ ፶፩፡፡ ፰፤ ፶፩፡፡

፳፯፤ አለችውም፡አዎን፡ ጌታ፡ሆይ። እኔ፡ አምናለሁ፡አንተ፡ክርስቶስ፡የእግዚአብሔር፡ ልጅ፡እንደ፡ ሆነህ፡ ወደ፡ ዓለም፡ ይመጣ ፡ ዘንድ ፡ ያለው።

ምዕ፡ ፮፤ ፷፱፡፡

፳፰፤ ይህነንም፡ብላ፡ ሔደች፡ ማርያምንም፡ እትዋን፡ጸራች፡ቀስ፡ብላ፡ አለቻትም። መምህር፡ መጥትዋል፡ እርሱም፡ ይጸራሻል።

፳፱፤ እርስዋም፡ይህነን፡በሰማች፡ጊዜ፡ ፈጥና፡ ተነሣች፡ ወደርሱም፡ መጣች።

፴፤ የሱስ፡ግን፡ወደ፡ገር፡ገና፡አልመጣም። ነገር፡ግን፡ ማርታ፡ ወደገኘችው፡ ሰፈራ፡ ነበረ።

፴፩፤ አይሁድ፡ግን፡ከርስዋ፡ጋራ፡ በቤት፡ ያጽናንዋት፡የነበሩ፡ ማርያምን፡ ባዩ፡ ጊዜ፡ፈጥና፡ እንደ፡ ተነሣች፡እንደ፡ወጣችም፡ተከተልዋት፡ እንደህ፡ ሲሉ። ወደ፡ መቃብር፡ ትሔዳለች፡ ከዚያ፡ ታለቅስ፡ ዘንድ።

፴፪፤ ማርያምም፡ በደረሰች፡ ጊዜ፡ የሱስ፡ ወደለበቱ፡ባየችውም፡ጊዜ፡ በግሩ፡ ወደቀች፡ አለችውም። ጌታ፡ሆይ፡ከዚህስ፡ በኖርህ፡ ወንድሜ፡ ባልሞተም።

፴፫፤ የሱስም፡ስታለቅስ፡ባያት፡ጊዜ፡ከርስዋ፡ጋራ፡ የመጡትንም፡አይሁድን ፡ ሲያለቅሱ። በልቡ፡ አዘነ፡ ራሱንም፡ አንቀሳቀሰ። ምዕ፡ ፲፫፤ ፳፩፡፡

፴፬፤ አለም፡ወደ፡ት፡ቀበራችሁት።አሉትም፡ጌታ፡ ሆይ፡ ናና፡ እይ።

፴፭፤ የሱስ፡ እንባውን፡ አፈሰሰ። ሉቃ፡ ፲፱፤ ፵፩፡፡

፴፮፤ አይሁድም ፡ አሉ። እዩ፡ እንዴት፡ ይወደው፡ ነበረ።

፴፯፤ ከርሳቸውም፡የነበሩ፡አሉ።በውኑ፡ይህ፡የውሩን፡ዓይን፡የከፈተ፡ባልቻለም፡ ነበረ፡ይህነን፡ ደግሞ፡ እንደይሞት፡ ያደርግ፡ ዘንድ። ምዕ፡ ፱፤ ፴፪፡፡

፴፰፤ የሱስም ፡ ደግሞ፡ ራሱን ፡ አንቀሳቀሰ፡ ወደ፡ መቃብርም፡መጣ።ዋሻም፡ነበረ፡በላዩም፡ ደንጊያ፡ ተከድኖ፡ ነበር።

፴፱፤ የሱስም፡ አለ። ደንጊያውን ፡ አንሡ ። አለችው፡ማርታ፡የሞተው፡እኅት።ጌታ፡ሆይ፡ፈጽሞ፡ ተልትዋል።አራት፡ ቀን፡ ሁኖታልና። ቍ፡ ፲፯፤

፵፤ የሱስም፡አላት።አላልሁሽምን፡ያመንሽ፡ እንደ፡ ሆንሽ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ምስጋና ፡ እንድታዪ።

ቍ፡ ፬፤ ፳፫፤ ፳፮፡፡

፵፩፤ ደንጊያውንም ፡ አነሡ ፡ የሞተው ፡ ከነበረበት፡ሰፈራ። የሱስም፡ዓይኖቹን፡ወደ፡ ላይ፡ አነሣ፡ አለም ። አባቴ፡ ሆይ ፡ አመሰግንሃለሁ ፡ ስምተኸኛልና።

ማር፡ ፯፤ ፴፬፡፡

፵፪፤ እኔም፡ አውቃለሁ ፡ ሁለጊዜ ፡ እንድስማኝ። ነገር፡ግን፡ስለለዚህ፡ ስለ፡ ቀሙቱ፡ ሕዝብ፡ አልሁ። ያምኑ ፡ ዘንድ፡ አንተ ፡ እንደ፡ ላክኸኝ። ምዕ፡ ፲፪፤ ፴፡፡

፵፫፤ ይህነንም፡ባለ፡ጊዜ፡በታላቅ፡ ቃል፡ጮኸ። አልዓዛር፡ ና፡ወደ፡ ሜዳ፡ ውጣ።

፵፬፤ የሞተውም፡ወጣ፡እጆቹ፡እግሮቹም፡ በከፈን፡ ተጠቅልለው። ፊቱም ፡ ተጠቅልሎ፡ በመጠምጠምያ። አላቸው፡ የሱስ ። ፍቱት፡ ተውትም፡ ይሒድ።

፵፭፤ ከአይሁድም፡ብዙ፡ ሰዎች፡ ወደ፡ ማርያም፡ የመጡ ፡ የሱስ ፡ ያደረገውን ፡ ባዩ ፡ ጊዜ ፡ አመኑበት።

ምዕ፡ ፯፤ ፴፩፡፡

፵፮፤ ከርሳቸው፡ግን፡ተከፍለው፡ ወደ፡ ፈሪሳውያን፡ሔዱ፡ የሱስ፡ ያደረገውንም፡ ነገር፡ ነገርዋቸው።

፵፯፤ የካህናት፡አለቆችም፡ፈሪሳውያንም፡ሸንጎ፡ ሰበሰቡ፡አሉም።ምን፡ እናድርግ። ይህ፡ ሰው፡ እጅግ፡ ተአምራት ፡ ያደርጋልና። መዝ፡ ፪፤ ፪፡፡

፵፰፤ እንደሁ፡ብንተወው፡ሁሉ፡ያምንበታል።የሮሜ ፡ ሰዎችም፡ ይመጣሉ ፡ ስፍራችነንም ፡ ወገናችነንም፡ ይወስዳሉ።

፵፱፤ ከርሳቸውም፡አንዱ፡ሰሙን፡ቀያፋ፡ የሚሉት፡ በዚያች፡ አመት፡ የካህናት፡ አለቃ ፡ የነበረ፡ አላቸው። እላንት፡ ምንም፡ አታውቁም።

ምዕ፡ ፲፰፤ ፲፬፡፡ ሉቃ፡ ፫፤ ፪፡፡

፶፤ አታስቡምምም፡ ለኛ፡እንዲሻለነ፡አንድ፡ሰው፡ቢሞት፡ ስለ ፡ ሕዝቡ ፡ ሕዝብም ፡ ሁሉ፡ እንደይጠፋ።

ምዕ፡ ፲፰፤ ፲፬፡፡

፶፩፤ ይህነንም፡ከልቡ፡ ያለ፡ አይደለም። ነገር፡ግን፡ በዚያች፡አመት፡ የካህናት፡አለቃ፡ነበረና፡ትንቢት፡ተናገረ፡የሱስ፡ስለ፡ሕዝብ፡ ይሞት፡ ዘንድ፡ እንደለው።

ዘፀአ፡ ፳፰፤ ፴፡፡ ዘኁ፡ ፳፯፤ ፳፩፡፡

፶፪፤ ስለ፡ሕዝብም፡ብቻ፡አይደለም።የእግዚአብሔርን፡ልጆች፡ደግሞ፡የተበተኑትን፡ወደአንድ፡ ሊሰበስባቸው፡ እንጂ። ምዕ፡ ፲፤ ፲፮፡፡ ኤፌ፡ ፪፤ ፲፮፤

፶፫፡ ከዚያም፡ቀን፡ ጀምሮ፡ ተማከሩ፡ ይገሉት፡ዘንድ።

፶፬፡ የሱስ፡ ግን፡ ከዚያ፡ በኋላ፡በአይሁድ፡ መካከል፡ተገልጦ፡አልሔደም፡ነገር፡ግን፡ ከዚያ፡ ለምድረ፡በደ፡ወደ፡ቀረበች፡ኤፍሬም፡ወደምትባል፡አገር፡ሔደ፡ ከዚያም፡ይመላለስ፡ነበረ፡ ከደቀ፡ መዛሙርቱ፡ጋራ።

፶፭፡ የአይሁድም፡ፋሲካ፡ቀርቦ፡ነበረ። ብዙም፡ሰዎች፡ ከዚያች፡ አገር፡ ወደ፡የሩሳሌም፡ ወጡ፡ ከፋሲካ፡በፊት፡ራሳቸውን፡ያነጹ፡ዘንድ። ፪፡ ዜና፡ ፴፡ ፲፯።

፶፮፡ የሱስንም፡ ፈለጉት፡ እርሱ፡ በርሳቸውም ፡ አሉ፡እርሳቸውም፡በመቅደስ፡ቁመው። ምን፡ይመስላችኋል። ወደ፡ በዓል፡ አይመጣምን።

፶፯፡ የካህናት፡አለቆችም፡ፈሪሳውያንም፡ ትእዛዝ፡ሰጡ፡ማንም፡ቢያውቅ፡እርሱ፡ ወዴት፡ ነው፡ያመለክታቸው፡ ዘንድ፡ ሊይዙት።

## ምዕራፍ፡ ፲፪፡

፩፡ ስድስት፡ቀን፡ከፋሲካ፡በፊት፡የሱስ፡ወደ፡ቢታንያ፡መጣ፡የሞተው፡አልዓዛር፡ወደ፡ ነበረበቱ፡ ከሙታን፡ ያስነሣው። ማቴ፡ ፳፮፡ ፮—፲፫። ማር፡ ፲፬፡ ፫—፱።

፪፡ ከዚያም፡ምሳ፡አደረጉለት። ማርታም፡ ታገለግል፡ነበራች። አልዓዛር፡ግን፡ከርሱ፡ጋራ፡ተቀምጠው፡ከነበሩት፡ አንዱ፡ እርሱ፡ ነበር። ሉቃ፡ ፲፡ ፴፱፡ ፵።

፫፡ ማርያመም፡ረጥል፡ሽቱ፡ወሰደች፡ ናርደስ፡የሚሉት፡የከበረ፡ዋጋውም፡ የበዛ። በርሱም፡የየሱስን፡ እግር፡ቀባች፡በጸጕርዋም፡ አበሰች። ቤቱም፡ ከሽቱው፡ መዓዛ፡መላ። ሉቃ፡ ፯፡ ፴፰።

፬፡ ከደቀ፡መዛሙርቱም፡አንዱ፡አለ፡እርሱም፡ይሁዳ፡ የአስቆሮቱ፡ የሲሞን፡ ልጅ፡ ያሲዘው፡ ዘንድ፡ያለው።

፭፡ ምነው፡አይሸጥ፡ይህ፡ ሽቱ፡ በሦስት፡ መቶ፡ ድሪም፡ ለድኆች፡ አይሰጥ። ማር፡ ፲፬፡ ፭።

፮፡ ይህነንም ፡ አለ ፡ ለድኆች፡አዝኖ ፡ አይደለም። ሌባ፡ነበረና፡እንጂ፡ከረጢቱም፡ከርሱ፡ ጋራ፡ ነበረ፡ በርሱም፡*የተገኘውን፡ሁሉ፡ይይዝ፡ነበር። *ሉቃ፡ ፰፡ ፫።

፯፡ የሱስም፡አለ። ተዋት። ለመቃብሬ፡ ቀን፡ ጠብቃው፡አለችና።

፰፡ *ድኆች፡ ሁልጊዜ፡ በላንት፡ ዘንድ፡ ናቸውና፡ እኔ፡ ግን ፡ ከላንት፡ ጋራ፡ ሁልጊዜ፡ አይደለሁም። *ዘዳግ፡ ፲፭፡ ፫።

፱፡ ከአይሁድም፡እጅግ፡ሰዎች፡ አወቁ፡ ከዚያ፡ እንደ፡ሆነ፡መጡም፡ስለ፡የሱስ፡ብቻ፡አይደለም፡አልዓዛርንም ፡ ከሙታን፡ ያስነሣውን ፡ ደግሞ ፡ ለማየት፡ እንጂ። ም፡ ፲፩፡ ፵፫።

፲፡ የካህናት፡አለቆችም፡ ተማከሩ፡ አልዓዛርን፡ደግሞ፡ ይገድሉት፡ ዘንድ።

፲፩፡ ከአይሁድ፡ብዙ፡ሰዎች፡ስለርሱ፡ ይሔዱ፡ በየሱስም፡ ያምኑ፡ ነበሩና።

፲፪፡ በነገውም፡ብዙ፡ሕዝብ፡ወደ፡ በዓል፡ የመጡ፡ የሱስ ፡ ወደ ፡ የሩሳሌም፡ እንዲመጣ ፡ በሰሙ፡ ጊዜ። ማቴ፡ ፳፩፡ ፩—፲፩። ማር፡ ፲፩፡ ፩—፲። ሉቃ፡ ፲፱፡ ፳፱—፵፰።

፲፫፡ የተምር ፡ ዛፍ ፡ ዝንጣፊ ፡ ወስዱ ፡ ሊቀበሉትም፡ወጡ፡ይጮሁም፡ነበሩ፡እንዲህ፡ ሲሉ ። ሆሣዕና። በእግዚአብሔር፡ ስም፡ የሚመጣ፡ የተባረከ፡ ነው፡ የእሥራኤል፡ ንጉሥ። መዝ፡ ፻፲፰፡ ፳፭፡ ፳፮።

፲፬፡ የሱስም፡አህያ፡ አገኘ፡ተቀመጠበትም። እንደ፡ ተጻፈ፡ እንዲህ፡ ሲል። ዘካ፡ ፱፡ ፱።

፲፭፡ አትፍሪ፡ የፅዮን፡ ልጅ። እነሆ፡ ንጉሥሽ፡ ይመጣል፡ ባህያ፡ ግልገል፡ ተቀምጦ።

፲፮፡ ደቀ፡መዛሙርቱም፡ይህነን፡ ነገር፡ አስቀድመው፡አላወቁም፡ነገር፡ግን፡የሱስ፡በተመሰገነ፡ ጊዜ፡የዚያን፡ጊዜ፡አሰቡ፡ይህ፡ነገር፡ስለርሱ፡ እንደ፡ ተጻፈ፡ይህነንም፡ እንደደረጉለት።

፲፯፡ ከርሱ፡ጋራ፡ የነበሩት፡ሕዝብም፡ ይመሰክሩለት፡ነበሩ፡አልዓዛርን፡ከመቃብር፡እንደ፡ጸራው፡ከሙታንም፡ እንደስነሣው።

፲፰፡ ስለዚህም ፡ ሕዝቡ ፡ ሊቀበሉት፡ ወጡ፡ ሰምተዋልና፡ ይህነን፡ ተአምራት፡ እንደደረገ።

፲፱፡ ፈሪሳውያንም፡እርሱ፡ በርሳቸው፡ አሉ። ታያላችሁን፡ በማናቸውም፡ እንዳልተረባችሁ። እነሆ፡ ዓለሙ፡ በኋላው፡ ተከተለዋል። ም፡ ፲፩፡ ፵፰።

፳፡ ከዮናውያንም፡ በበዓል፡ ሊሰግዱ ፡ ከወጡት፡ ነበሩ።

፳፩፡ እርሳቸውም፡ወደ፡ ፊልጶስ፡ መጡ፡ ከገሊላ፡ አገር፡ከቤተ፡ሰይደ፡የሚሆን። ለመኑትም፡ እንዲህ፡ ሲሉ። ጌታ፡ሆይ፡ እንወዳለን፡ የሱስን፡ እናይ፡ ዘንድ።

፳፪፡ ፊልጶስም፡ መጣ፡ ለእንድርያስም፡ ነገረው። ደግሞም፡ እንድርያስ፡ ፊልጶስም፡ ለየሱስ፡ ነገሩት።

፳፫፡ የሱስም፡ መለሰላቸው፡ እንዲህ፡ ሲል ። ጊዜው፡ ደረሰ፡ የሰው፡ ልጅ፡ የሚመስገንበት።

፳፬፡ እውነት፡እውነት፡ እላችኋለሁ። *የስንዴ፡ ቅንጣት፡ በምድር፡ ካልወደቀች፡ ባልሞተችም፡ ለብቻዋ፡ቀረች። የሞተች፡እንደሆን፡ግን፡ ብዙ፡ ፍሬ፡ ታደርጋለች። *ሮሜ፡ ፲፬፡ ፱። ፩፡ ቆሮ፡ ፲፭፡ ፴፮።

፳፭፡ ነፍሱን፡ የወደደ፡ ያጠፋታል ። ነፍሱንም፡ የጸላ፡ በዚህ፡ ዓለም፡ ለዘላለም፡ ሕይወት፡ ይጠብቃታል። ሉቃ፡ ፲፯፡ ፴፫።

፳፮፡ ማንም፡ የሚያገለግለኝ፡ ቢኖር ፡ ይከተለኝ። *እኔም፡ወደምኖርበት፡ከዚያም፡ ደግሞ፡ ይኖራል፡ የሚያገለግለኝ። ማንም፡ቢያገለግለኝ፡ እርሱን፡ አብ፡ †ያከብረዋል። *ም፡ ፲፬፡ ፫። †መዝ፡ ፸፫፡ ፳፬።

፳፯፡ ዛሬስ፡ ነፍሴ፡ ታውካለች። ምን፡ እላለሁ። አባቴ፡ሆይ፡ አድነኝ፡ ከዚህች፡ ሰዓት። ነገር፡ግን፡ ስለዚህች፡ ሰዓት፡ መጣሁ።

፳፰፡ አባቴ፡ሆይ ፡ ስምህን፡ አክብረው ። ከሰማይ

ም፡ቃል፡መጣ፡የሚል። ፈጽሚ፡ አከበርሁት፡ ደግሞም፡ *አከብረዋለሁ። *ማቴ፡ ፫፤ ፲፯።

፳፱፤ ሕዝብም፡ቆመው፡የነበሩ፡የሰሙም፡ አሉ። ነጐድጓድ ፡ነው ። ሌሎችም ፡ አሉ ። መልአክ ፡ ተናገረው።

፴፤ መለሰ፡የሱስ ፡አለም። ይህ፡ ቃል፡ስለኔ፡አልመጣም፡*ስለላንት፡ እንጂ። *ም፡ ፲፩፤ ፵፪።

፴፩፤ አሁን፡ደረሰ፡የዚህ፡ዓለም ፡*ፍርድ። አሁን፡ የዚህ፡ ዓለም፡አለቃ፡ወደ፡ሚደ፡ †ይጣላል። *ም፡ ፱፤ ፴፱። †ም፡ ፲፮፤ ፲፩። ቆላ፡ ፪፤ ፲፭።

፴፪፤ እኔም፡ከምድር፡ከፍ፡ከፍ፡ ባልሁ፡ ጊዜ፡ ሁሉን፡ወደኔ፡ እስባለሁ። ም፡ ፰፤ ፳፰።

፴፫፤ ይህነንም፡ያለ፡በምን፡ ሞት፡ ይሞት፡ ዘንድ፡ እንደለው፡ ይነግር፡ዘንድ፡ ነው። ም፡ ፲፰፤ ፴፪።

፴፬፤ ሕዝብም፡ መለሰለት፡አለውም። እኛ፡ ከኦሪት፡ሰማነ፡ክርስቶስ፡*ለዘላለም፡እንዲኖር። እንዴትም፡ትላለህ፡ አንተ፡ የሰው፡ ልጅ፡ ከፍ፡ከፍ፡ ይል፡ ዘንድ፡ እንደለው ። ይህ፡ ማነው፡ የሰው፡ ልጅ። መዝ፡ ፻፲፤ ፬። ዳን፡ ፯፤ ፲፬።

፴፭፤ የሱስም ፡ አላቸው ። ደግሞ፡ ጥቂት፡ ዘመን፡ *ብርሃን፡ከላንት፡ጋራ፡ነው። †ተመላለሱ፡ብርሃን፡ሳላላችሁ፡ጨለማ፡እንዳያገኛችሁ። **በጨለማ፡የሚሔድ፡አያውቅምና፡ወዴት፡ እንዲሔድ። *ቍ፡ ፵፮። †ኤር፡ ፲፫፤ ፲፮። **ም፡ ፲፩፤ ፲።

፴፮፤ ብርሃን፡ሳላላችሁ፡ በብርሃን፡ እመኑ፡ የብርሃን፡ልጆች፡እንድትሆኑ። ይህነንም፡ ተናግሮ፡ የሱስ፡ ሔደ፡ ተሠወራቸውም። ኤፌ፡ ፭፤ ፰።

፴፯፤ እርሱ ፡ ግን፡ ይህነን ፡ ያህል ፡ ተአምራት ፡ ምንስ ፡ ቢያደረግ ፡ በፊታቸው ፡ እርሳቸው ፡ አላመኑበትም።

፴፰፤ የኢሳይያስ፡*የነቢዩ፡ነገር፡ይፈጸም፡ዘንድ፡ያለው። አቤቱ፡ማን፡በምስክርነታችን፡ አመነ። የእግዚአብሔርስ፡ ክንድ፡ ለማን፡ ተገለጠ። ኢሳ፡ ፶፫፤ ፩። ሮሜ፡ ፲፤ ፲፮።

፴፱፤ ስለዚህም፡ ሊያምኑ ፡ አልቻሉም ። ኢሳይያስ፡ደግሞ፡ ብሏልና። ኢሳ፡ ፮፤ ፱፤ ፲።

፵፤ ዓይናቸውን፡አሳወረ፡ልባቸውንም፡ አደነደነ። ባይናቸው ፡ እንዳያዩ ፡ በልባቸውም ፡ እንዳያስተውሉ ። ተመልሰውም፡ ይቅር፡ እንዳልላቸው።

፵፩፤ ይህነን፡ተናገረ፡ኢሳይያስ፡ ክብሩን፡ባየ፡ጊዜ፡ ስለርሱም፡ አለ። ኢሳ፡ ፮፤ ፩።

፵፪፤ ከዚህም፡ጋራ፡ካለቆች፡ደግሞ፡ብዙ፡ ሰዎች፡ አመኑበት። ነገር፡ግን፡ስለ፡ ፈሪሳውያን፡ ይህነን፡ አልገለጡም፡ወደ፡መስጊድ፡ከመግባት፡እንዳይከለከሉ። ም፡ ፱፤ ፳፪።

፵፫፤ የሰውን፡ ምስጋና፡ወደዋልና፡ ከእግዚአብሔር፡ምስጋና፡ ይልቅ። ም፡ ፭፤ ፵፬።

፵፬፤ የሱስም፡ጮኸ፡አለም። በኔ፡የሚያምን፡በኔ፡ የሚያምን፡አይደለም፡በላከኝ፡እንጂ።

፵፭፤ የሚያየኝም ፡ እኔን ፡ የላከኝ፡ አየ። ም፡ ፲፬፤ ፱።

፵፮፤ እኔ፡ብርሃን፡ሁኜ፡ወደ፡ዓለም፡መጣሁ፡ያመነብኝ፡ ሁሉ፡ በጨለማ፡ እንዳይኖር።

፵፯፤ ማንም፡ነገሬን፡ ቢሰማ፡ ባይጠብቀውም፡ እኔ፡ አልፈርድበትም ። በዓለም ፡ ልፈርድ ፡ አልመጣሁምና፡ዓለምን፡*ላድን፡ እንጂ። *ም፡ ፫፤ ፲፯፤ ፲፰።

፵፰፤ *የናቀኝም፡ነገሬንም፡ያልተቀበለ፡ የሚፈርድበት፡አለ። የተናገርኋት፡ ነገር፡ እርስዋ፡ ትፈርድበታለች፡ †በኋለኛው፡ ቀን። *ም፡ ፰፤ ፵፯፤ ፵፭። †ዘዳግ፡ ፲፰፤ ፲፱። ሮሜ፡ ፪፤ ፲፪።

፵፱፤ እኔ፡ ከራሴ፡ አልናገርምና፡ የላከኝ፡ አብ፡ እርሱ፡ትእዛዝ፡ሰጠኝ፡እንጂ፡የምልበትን፡የምናገርበትንም። ም፡ ፲፬፤ ፲።

፶፤ አውቃለሁም፡ ትእዛዙ፡ የዘላለም፡ ሕይወት፡ እንደ፡ሆነች። ነገሬቱም፡እኔ፡ የምናገራት፡ አብ፡ እንደለኝ፡ እንዲሁ፡ እናገራለሁ። ም፡ ፭፤ ፴።

## ምዕራፍ፡ ፲፫፤

፩፤ ከፋሲካም፡በፊት፡ የሱስ፡ባወቀ፡ጊዜ፡ጊዜው፡ እንደ፡ደረሰ፡ ከዚህ፡ ዓለም፡ ወደ፡ አብ፡ ይሔድ፡ ዘንድ። ወገኖቹን፡በዓለም፡ያሉትን፡ የወደዳቸውን፡ እርሳቸውን፡ለፍጻሚው፡ ወደዳቸው። ም፡ ፲፮፤ ፳፰።

፪፤ እራትም፡ከበላ፡በኋላ፡ሰይጣንም፡በይሁዳ፡ ልብ፡በአስቀሮቱ፡በሲሞን፡ልጅ፡ አሁን፡በአኖረ፡ ጊዜ፡አሳልፎ፡ ይሰጠው፡ ዘንድ። ሉቃ፡ ፳፪፤ ፫።

፫፤ የሱስም፡ባወቀ፡ጊዜ፡አብ፡ ሁሉን፡ በጁ፡ እንደ፡ ሰጠው፡ከእግዚአብሔርም፡እንደ፡ወጣ፡ወደ፡እግዚአብሔርም፡እንዲሔድ።

፬፤ ከራት፡ተነሣ፡ ልብሱንም፡ አኖረ ። የሚያብስበትም፡ ማበሻ፡ ወሰደ፡ ታጠቀበትም።

፭፤ በመታጠቢያውም፡ውኃ፡ አፈሰሰ፡ የደቀ፡መዛሙርትንም፡እግር፡ያጽበው፡በታጠቀበትም፡ማበሻ፡ ያደርቀው፡ጀመረ። ፩፤ ሳሙ፡ ፳፭፤ ፵፩።

፮፤ ወደ፡ ሲሞን፡ጴጥሮስም፡መጣ። ያም፡አለው። አቤቱ፡አንተን፡እግሬን፡ ታጽብልኛለህ።

፯፤ የሱስም ፡ መለሰለት፡ አለውም። እኔ፡ የምሰራውን፡አንተ፡ዛሬ፡አታውቀውም፡ነገር፡ግን፡ ኋላ፡ታውቀዋለህ።

፰፤ ጴጥሮስም፡አለው። እግሬን፡አታጸበኝም፡ ለዘላለም። የሱስም ፡ መለሰለት፡ አለውም። ካላጸብሁህ፡ከኔ፡ ጋራ፡ ክፍል፡ የለህም። ራእ፡ ፩፤ ፭።

፱፤ ሲሞን ፡ ጴጥሮስም፡ አለው። ጌታ፡ ሆይ፡ እግሬን፡ ብቻ፡ የምታጽበኝ፡ አትሁን ፡ እጄንም፡ ራሴንም፡ እንጂ።

፲፤ የሱስም፡አለው። ማጸብ፡የገባ፡አይሻም፡ እግሩን፡ከመታጸብ፡በቀር። ሁለንትናው፡ንጹ፡ ነው፡ እንጂ፡ እላንትም፡ንጹሓን፡ናችሁ፡ነገር፡ግን፡ ሁላችሁ፡ አይደላችሁም። ም፡ ፲፭፤ ፫። ቲቶ፡ ፫፤ ፭።

፲፩፡ ያውቅ፡ነበረና፡አሳልፎ፡የሚሰጠውን። ስለዚ
ህም፡አለ። ሁላችሁ፡ ንጹሓን፡ አይደላችሁም።
ም፡ ፯፡ ፫፡፫፩፡
፲፪፡ እግራቸውንም፡አጽቦ፡ልብሱን፡ ተቀበለ፡ ደግ
ሞም፡ ተቀመጠ፡ አላቸውም ። ያደረግሁባችሁን፡ አ
ወቃችሁን።
፲፫፡ እላንተ፡ትሉኛላችሁ፡መምህር፡ጌታም። መል
ካምም ፡ ትላላችሁ ። እኔ ፡ እንደሁ ፡ ነኝና።
ማቴ፡ ፳፫፡ ፰፡ ፲፡፡
፲፬፡ እንኪያስ፡እኔ፡ጌታ፡መምህር፡ስሆን፡እግራች
ሁን፡ካጸብሁ።እላንተም፡ደግሞ፡ይገባችኋል፡የባልን
ጀራችሁን ፡ እግር፡ ታጽቡ ፡ ዘንድ ፡ እርሱ ፡ በርሳችሁ።
ሮሜ፡ ፲፪፡ ፲፡፡
፲፭፡ ምሳሌ፡ሰጥቻችኋለሁና፡እኔ፡በላንተ፡እንደደ
ረግሁ፡ እላንተም፡ ደግሞ፡ ታደርጉ፡ ዘንድ።
፩፡ ጴጥ፡ ፪፡ ፳፩ ፡
፲፮፡ እውነት፡ እውነት፡ እላችኋለሁ። ባርያ፡ ከጌታ
ው፡ የበለጠ ፡ አይደለም ። መልክተኛም፡ ከላከው።
፲፯፡ እላንተም ፡ ይህነን፡ሁሉ፡ ብታውቁ፡ ብፁዓን፡
ናችሁ፡ ብታደርጉት። ማቴ፡ ፯፡ ፳፬፡፡ ያዕ፡ ፩፡ ፳፭፡፡
፲፰፡ ስለ፡ሁላችሁ፡ አልልም። እኔ፡ የመረጥኋቸው
ን፡አውቃለሁ።ነገር፡ግን፡መጽሐፍ፡ ያለው፡ይፈጸም፡
ዘንድ፡ነው። ከኔ፡ጋራ፡ እንጀራ፡ የበላ፡ እግሩን፡ በላዬ፡
አነሣ። መዝ፡ ፵፩፡ ፲፡፡
፲፱፡ ከዛሬም፡ ጀምሬ ፡ እላችኋለሁ ፡ አስቀድሞ፡
ሳይሆን።በሆነ፡ጊዜ፡እንድታምኑ፡እኔ፡እንደ፡ ሆንሁ።
፳፡ እውነት፡ እውነት፡ እላችኋለሁ ። ማንም፡ የተ
ቀበለ፡በላክሁት፡ጊዜ፡እኔን፡ ይቀበላል። የሚቀበለኝ
ም፡ እርሱም፡ የላከኝን፡ ይቀበላል። ማቴ፡ ፲፡ ፵፡፡
፳፩፡ ይህነንም፡ብሎ፡የሱስ፡በመንፈስ፡ታወከ፡መ
ሰከረም፡አለም ። እውነት ፡ እውነት ፡ እላችኋለሁ።
አንዱ፡ ከላንተ፡አሳልፎ፡ እንዲሰጠኝ።
ማቴ፡ ፳፮፡ ፳፩፡—፳፭፡፡ ማር፡ ፲፬፡ ፲፰፡—፳፩፡፡
ሉቃ፡ ፳፪፡ ፳፩፡—፳፫፡፡
፳፪፡ ደቀ፡ መዛሙርቱም ፡ እርሱ፡ በርሳቸው፡ተያ
ዩ፡ተደንቀው፡ ስለ፡ ማን፡ ይላል።
፳፫፡ ከደቀ፡መዛሙርቱም፡*አንዱ፡በየሱስ፡ጭን፡
ተቀምጦ ፡ ነበረ ። እርሱም ፡ የሱስ፡ ይወደው፡ የነበረ
ው፡ነው። *ም፡ ፳፩፡ ፳፡፡
፳፬፡ እርሱን፡ጠቀሰው፡ሲሞን፡ ጴጥሮስ፡ይጠይቀ
ው፡ዘንድ፡ ማነው፡ ስለርሱ፡ ያለው።
፳፭፡ ያም፡ወደ፡የሱስ፡ደረት፡ተገድፎ፡ አለው። ጌ
ታ፡ ሆይ፡ እርሱ፡ ማነው።
፳፮፡ መለሰ፡የሱስ፡ አለም። ያ፡እኔ፡ ቅማሽ፡ እንጀ
ራ፡ነክሬ፡የምሰጠው።እንጀራም፡ነክሮ፡ለይሁዳ፡ለስ
ቆሮቱ፡ሰጠው፡ለሲሞን፡ ልጅ። ዘፀአ፡ ፲፪፡ ፰፡፡
፳፯፡ ከንጀራም፡በኋላ፡የዚያን፡ጊዜ፡ ሰይጣን፡ ገባ
በት። የሱስም፡ አለው ።የምታደርገውን፡ ፈጥነህ፡ አ
ድርገው።
፳፰፡ ከተቀመጡትም፡ ማንም፡ አያውቅም፡ ነበ
ር፡ለምን፡ ይህን፡ አለው።
፳፱፡ የመሰላቸውም፡አሉ፡ከረጢት፡በይሁዳ፡ዘን
ድ፡ነበረና፡የሱስ፡ ያለው፡ግዛ፡ ለበዓል፡ የምንሻውን።
ወይም ፡ ለድኆች፡ እንደች ፡ ይሰጥ ፡ ዘንድ።
፴፡ ያም፡እንጀራውን፡ከተቀበለ፡በኋላ፡ የዚያን፡
ጊዜውን፡ ወጣ። ሌትም፡ ነበር።
፴፩፡ ይሁዳም፡በወጣ፡ጊዜ፡ የሱስ፡ አለ። ዛሬ፡የሰ
ው፡ልጅ፡ተመሰገነ፡ እግዚአብሔርም፡ተመሰገነበት።
፴፪፡ እግዚአብሔር ፡ ከተመሰገነበት ፡ እግዚአብ
ሔር፡ደግሞ፡በራሱ፡ ያመሰግነዋል፡ በዚህም፡ጊዜ፡ ያ
መሰግነዋል። ም፡ ፲፪፡ ፳፫፡፡
፴፫፡ ልጆቼ፡ሆይ፡እኔ፡ደግሞ፡ ጥቂት፡ዘመን፡ከላን
ት፡ጋራ፡ነኝ። ትሹኛላችሁ፡ ለአይሁድም፡ እንደልኋቸ
ው፡እኔ፡ወደምሔድበት፡ እላንት፡ መምጣት፡ አይቻ
ላችሁም ። ዛሬም ፡ ለላንት ፡ እላችኋለሁ።
ም፡ ፯፡ ፴፬፡፡
፴፬፡ አዲስ፡ትእዛዝ፡እሰጣችኋለሁ፡እርሱ፡ በርሳ
ችሁ፡ ትዋደዱ፡ ዘንድ። እንደ፡ ወደድኋችሁ፡ እላንት
ም፡ ደግሞ፡ እርሱ፡በርሳችሁ፡ ትዋደዱ፡ ዘንድ።
ም፡ ፲፭፡ ፲፪፡ ፲፫፡፡
፴፭፡ በዚህ፡ያውቃል፡ሰው፡ሁሉ፡እላንት፡ደቀ፡መ
ዛሙርቴ፡እንደ፡ሆናችሁ፡እርሱ፡ በርሳችሁ፡ ፍቅር፡ ቢ
ኖርባችሁ። ፩፡ዮሐ፡ ፪፡ ፭፡፡
፴፮፡ ሲሞን፡ጴጥሮስም፡ አለው። ጌታ፡ሆይ፡ ወዴ
ት፡ ትሔዳለህ። የሱስም፡መለሰለት፡ አለውም። *ወ
ደምሔድበት፡ስፍራ፡ዛሬ፡ትከተለኝ፡ዘንድ፡አትችል
ም። ነገር፡ግን፡ኋላ፡ ትትከተለኛለህ። *ም፡ ፯፡ ፴፬፡፡
†ም፡ ፳፩፡ ፲፰፡ ፲፱፡፡
፴፯፡ ጴጥሮስም፡አለው።ጌታ፡ሆይ፡ምነው፡አልችል
ም፡ዛሬ፡እከተልህ፡ዘንድ፡ ነፍሴን፡ ስንኳ፡ ስላንተ፡
እለውጣታለሁ።
፴፰፡ የሱስም፡መለሰለት፡አለውም። ነፍስህን፡
ስለኔ፡ ትለውጣለህ። እውነት ፡ እውነት ፡ እልሃለሁ።
ዶሮ፡ አይጮህም፡ ሶስት፡ ጊዜ፡ እስክትክደኝ፡ ድረስ።

## ምዕራፍ፡ ፲፬፡

፩፡ ልባችሁ፡አይደንግጥ። በእግዚአብሔር፡ ታምና
ላችሁ፡ በኔም፡ እመኑ። ም፡ ፲፪፡፡ ፵፬፡
፪፡ ባባቴ፡ ቤት፡ብዙ ፡ ስፍራ፡ አለ። ያስ ፡ ባይሆን፡ባ
ልኋችሁ፡ ነበርሁ ። እሔዳለሁ፡ ቦታ፡ አዘጋጅላችሁ፡ ዘ
ንድ። ፪፡ ቆሮ፡ ፭፡ ፩፡፡
፫፡ በሔድሁም፡ ቦታም፡ ባዘጋጀሁላችሁ፡ ጊዜ፡ ደግ
ሞ፡እመጣለሁ፡ወደኔም፡እወስዳችኋለሁ። እኔ፡ወደ
ለሁበት፡ እላንትም፡ ደግሞ ፡ ትሆኑ ፡ ዘንድ።
ም፡ ፲፯፡ ፳፬፡፡
፬፡ እላንትም፡ታውቃላችሁ፡ ወዴት፡ እንድሔድ፡
መንገዱንም ፡ ታውቃላችሁ።
፭፡ ቶማስ፡አለው። ጌታ፡ሆይ፡ ወዴት፡ እንድትሔ

ድ፡ አናውቅም ። እንዴትስ፡ እንችላለን ፡ መንገዱን፡ እናውቅ፡ ዘንድ።

፮፡ የሱስም፡አለው።እኔ፡*መንገድ፡ነኝ፡ †እውነትም፡ **ሕይወትም ። አንድም ፡ ወደ፡ አብ፡ አይመጣም፡ በኔ፡ በቀር። *ዕብ፡ ፲፡ ፲፱፡፡ †ራእ፡ ፫፡ ፲፬፡፡ **፩፡ ዮሐ ፭፡፡

፯፡ እኔን፡ብታውቁኝስ፡አባቴንም፡ደግሞ፡ባወቃችሁ።ከዚህስ፡ ወዲህ፡ታውቁታላችሁ፡ፈጽማችሁም፡ አያችሁት።

፰፡ አለው፡ፊልጶስ። ጌታ፡ሆይ፡አብን፡ አሳየንና፡ይበቃናል። ዘፀአ፡ ፴፫፡ ፲፰፡፡

፱፡ አለው፡የሱስ። እኔ፡ ከላንተ፡ጋራ፡ነኝ፡ይህነን፡ያህል፡ዘመን፡አታውቀኝምን፡ፊልጶስ። እኔን፡ያየ፡አብን፡ፈጽሞ፡ አየ ። እንዴትም፡ ትላለህ ፡ አንተ፡ አብን፡ አሳየነ። ም፡ ፲፪፡ ፵፭፡፡

፲፡ አታምንምን፡ *እኔ፡ በአብ፡ እንዳለሁ፡ አብም፡ በኔ። ለላንት፡ የምነግራችሁን፡ ነገር፡ ከኔ፡ አልናገርም። አብ፡ በኔ፡ ያደረብኝ፡ እርሱ፡ †ስራውን፡ ይሰራል፡ እንጂ። *ም፡ ፲፡ ፴፰፡፡ †ም፡ ፭፡ ፲፱፡፡

፲፩፡ በኔ፡ እመኑ፡ እኔ ፡ በአብ ፡ እንዳለሁ ፡ አብም፡ በኔ።ወይም፡ስለ፡ስራዬ፡ በኔ፡እመኑ።

፲፪፡ እውነት፡እውነት፡እላችኋለሁ።የሚያምንብኝ፡እኔ፡የምሰራትን፡ስራ፡ ያም፡ደግሞ፡ ያደርጋል፡ከርስዋም፡ የበለጠ፡ ያደርጋል ። እኔ፡ ወደ፡ባቴ ፡ እሔዳለሁና። ማር፡ ፲፮፡ ፲፱፡ ፳፡፡

፲፫፡ በስሜም ፡*የለመናችሁትን፡ ሁሉ፡ ይህነን፡ አደርጋዋለሁ፡ አባት፡ †በልጁ፡ ይመሰገን፡ ዘንድ። ም፡ ፲፭፡ ፯፡፡ † ም፡ ፭፡ ፳፫፡፡

፲፬፡ ምንም ፡ በስሜ ፡ ብትለምኑ፡ እኔ ፡ አደርገዋለሁ። ፩፡ዮሐ፡ ፭፡ ፲፬፡ ፲፭፡፡

፲፭፡ ብትወዱኝ ፡ ትእዛዜን ፡ ጠብቁ። ፩፡ ዮሐ፡ ፭፡ ፫፡፡

፲፮፡ እኔም፡አብን፡ እለምናለሁ፡ ሌላም፡ የሚያጽና፡ ይሰጣችኋል፡ ከላንት ፡ ጋራ፡ ይኖር፡ ዘንድ፡ ለዘላለም።

፲፯፡ የእውነት፡መንፈስ፡ዓለም፡ የማይችለው፡ ይቀበለው፡ዘንድ።አያየውምና፡አያውቀውምና።እላንት፡ግን፡ ታውቁታላችሁ። በላንት፡ ዘንድ፡ ይኖራልና፡ በላንትም፡ ይሆናል። ም፡ ፯፡ ፴፮፡፡

፲፰፡ ድኆች፡ ሁናችሁ፡ አልተዋችሁም፡ ወደላንት፡ እመጣለሁ። ማቴ፡ ፳፰፡ ፳፡፡

፲፱፡ ጥቂት፡ዘመን፡ዓለምም፡ደግሞ፡ አያየኝም። እላንት፡ ግን፡ *ታዩኛላችሁ። እኔ፡ ሕያው፡ ነኝና፡ እላንትም ፡ ሕያዋን ፡ ትሆናላችሁ። *ም ፲፮፡ ፲፮፡፡ ሆሴ፡ ፮፡ ፪፡፡

፳፡ በዚያን፡ቀን፡ ታውቃላችሁ፡ እኔ፡ ባባቴ፡ እንደ፡ ሆንሁ።እላንትም፡በኔ። እኔም፡ በላንት።

፳፩፡ ትእዛዜ፡ ወደርሱ፡ ያለች ፡ የሚጠብቃትም፡ ያ፡ነው፡ *የሚወደኝ። የሚወደኝንም፡ አባቴ፡ ይወደዋል ፡ እኔም ፡ እወደዋለሁ ፡ ራሴንም ፡ †እገልጥለታለሁ። *ቍ፡ ፲፭፡፡ †ኤፌ፡ ፩፡ ፲፯፡ ፲፰፡፡

፳፪፡ አለው፡ ይሁዳ፡ ያስቆሮቱ፡ አይደለም። ጌታ፡ ሆይ፡ ምንድር፡ ነው፡ ትርጓሚው፡ ራስህን፡ ለኛ፡ትገልጥ፡ዘንድ፡ እንዳለህ፡ለዓለምም፡ ያይደለ። የይሁ፡ ፩፡፡

፳፫፡ መለሰ፡የሱስ፡አለውም። አንድም፡የሚወደኝ፡ ቢኖር፡ ነገሬን፡ ይጠብቃል። አባቴም፡ *ይወደዋል። ወደርሱም፡እንመጣለን፡በርሱም፡ዘንድ፡ †ማደርያ፡ እናደርጋለን። *ቍ፡ ፳፩፡፡ ም፡ ፲፫፡ ፴፬፡፡ ምሳ፡ ፰፡ ፲፯፡፡ †ዘሌዋ፡ ፲፩፡ ፲፪፡

፳፬፡ የማይወደኝ፡ ነገሬን፡ አይጠብቅም ። የምትሰሙዋትም፡ነገር፡ለኔ፡አይደለችም። ለላከኝ፡ለአብ፡ እንጂ። ም፡ ፯፡ ፲፮፡፡

፳፭፡ ይህችን፡ ነገርኋችሁ፡ ከላንት፡ጋራ፡ ሳለሁ።

፳፮፡ *የሚያጽናው፡ ግን፡ እርሱም፡ መንፈስ፡ቅዱስ፡አብ፡የሚሰደው፡በስሜ፡እርሱ፡ሁሉን፡ያስተምራችኋል፡ ያልኋችሁንም፡ ሁሉ፡ ያሳስባችኋል። *ቍ፡ ፲፮፡፡ ም፡ ፲፭፡ ፳፮፡፡

፳፯፡ ሰላምን፡እተውላችኋለሁ። ሰላሜን፡ እሰጣችኋለሁ። እኔ፡የምሰጣችሁ፡ አይደለም፡ዓለም፡ እንደ፡ሰጥ ። ልባችሁ፡ አይደንግጥ፡ አይፍራም። ፊል፡ ፬፡ ፯፡፡

፳፰፡ ሰማችሁ፡እንዳልኋችሁ፡ እሔዳለሁ፡ ወደላንትም፡ እመጣለሁ። ብትወዱኝስ፡ ደስ፡ ባላችሁ፡ ነበር፡ስላልኋችሁ፡ ወደ፡አብ፡ እሔዳለሁ። አባቴ፡ እርሱ፡ ከኔ፡ ይበልጣልና።

፳፱፡ አሁንም፡አልኋችሁ፡ አስቀድሞ፡ሳይሆን። በሆነ፡ ጊዜ፡ ታምኑ፡ዘንድ።

፴፡ ደግሞ፡ከላንት፡ ጋራ፡ እጅግ፡ አልናገርም። የዚህ፡ዓለም፡ገዥ፡ይመጣልና፡ ለርሱም፡በኔ፡ አንዳች፡ የለውም። ም፡ ፲፪፡ ፴፩፡፡ ዕብ፡ ፯፡ ፳፮፡፡

፴፩፡ ነገር፡ግን፡ዓለም፡ያውቅ፡ ዘንድ፡ ነው፡ እኔ፡ አብን፡እንድወድ፡ አብም፡ እንዳዘዘኝ፡ እንዲሁ፡ አደርጋለሁ።ተነሡ፡ እንሒድ፡ ከዚህ። ም፡ ፲፡ ፲፰፡፡

## ምዕራፍ፡ ፲፭፡

፩፡ እኔ፡ነኝ፡ የወይን፡ጕንድ፡ እውነተኛ። ተካዩም፡ አባቴ፡ነው። መዝ፡ ፹፡ ፲፮፡፡

፪፡ ዱፋን፡ ሁሉ፡ በኔ፡ የማያፈራውን፡ ያስወግደዋል። የሚያፈራውን፡ዱፍ፡ግን፡ያጸራዋል፡እጅግ፡ያፈራ፡ዘንድ።

፫፡ እላንት ፡ አሁን፡ ንጹሓን፡ ናችሁ፡ ስለ፡ ነገርኋችሁ፡ነገር።

፬፡ በኔ፡ጽኑ፡እኔም፡በላንት። ዱፍም፡እንደይችል፡ ያፈራ፡ዘንድ፡ብቻውን፡ በወይኑ፡ ዛፍ፡ ከሌለ። እንደሁም፡ እላንት፡ በኔ፡ ካልጸናችሁ። ም፡ ፲፫፡ ፲፡፡

፭፡ እኔ፡ የወይን፡ ጕንድ፡ ነኝ፡ እላንትም ፡ ዱፎች።

በኔ፡የሚጸና፡እኔም፡በርሱ፡እርሱ፡እጅግ፡ፍሬ፡ ያፈራ ል።*ያለኔ፡ አትችሉምና፡ አንዳች፡ ታደርጉ፡ ዘንድ።
*፪፡ ቆሮ፡ ፫፡ ፭።

፮፤ ማንም፡በኔ፡ባይጸና፡እንደ፡ጫፍ፡ወደ፡ሜዳ፡ይ ጣላል፡ ይደርቅማል። ይሰበስቡታልም፡ ወደሳትም፡ ይጥሉታል፡ ይቃጠልማል።

፯፤ በኔ፡ብትጸኑ፡ ነገሬም፡ በላንት፡ ቢጸና፡ የምትሹ ትን፡ ሁሉ፡ ትለምናላችሁ፡ ይሆንላችሁማል።
ማር፡ ፲፩፡ ፳፬።

፰፤ በዚህ፡አባቴ፡ ይመሰገናል፡ እጅግ፡ ፍሬ፡ታፈሩ፡ ዘንድ። ደቀ፡ መዛሙርቴም፡ ትሆናላችሁ።

፱፤ አብ፡እንደ፡ ወደደኝ፡ እንደሁ፡እኔ፡ ወደድኋች ሁ።በውዴ፡ጽኑ። ሮሜ፡ ፰፡ ፴፭፡ ፴፱።

፲፤ ትእዛዛቴን፡የጠበቃችሁ፡እንደሆን፡በውዴ፡ ት ጸናላችሁ፡እኔ፡ያባቴን፡ ትእዛዛት፡ እንደ፡ ጠበቅሁ፡በ ውዱም፡እንደ፡ጸናሁ። ም፡ ፲፬፡ ፲፭። ፩፡ ዮሐ፡ ፭፡ ፫።

፲፩፤ ይህችን፡ ነገርኋችሁ፡ ደስታዬ፡ በላንት፡ ይጸና፡ ዘንድ፡ደስታችሁም፡ ይፈጸም፡ ዘንድ። ም፡ ፲፯፡ ፲፫።

፲፪፤ ይህች፡ትእዛዜ፡ናት፡ እርሱ፡ በርሳችሁ፡ ትዋደ ዱ፡ዘንድ፡ እኔ፡እንደ፡ ወደድኋችሁ። ም፡ ፲፫፡ ፴፬።

፲፫፤ ከዚህ፡ የበለጠ፡ ፍቅር፡የለም፡ ማንም፡ ነፍሱ ን፡ ይለውጥ፡ዘንድ፡ ስለ፡ ወዳጆቹ። ፩፡ ዮሐ፡ ፫፡ ፲፮።

፲፬፤ እላንት፡ወዳጆቼ፡ናችሁ፡ያዘዝኋችሁን፡ሁሉ፡ ያደረጋችሁ፡ እንደሆን። ም፡ ፳፡ ፴፩።

፲፭፤ ደግሞ፡ባሮች፡ አልላችሁም። *ባርያ፡አያውቅ ምና፡ጌታው፡የሚያደርገውን። እኔ፡ግን፡ ወዳጆቼ፡ አ ልኋችሁ። †ካባቴ፡ የሰማሁትን፡ ሁሉ፡ አስተምራች ኋለሁና። *ሮሜ፡ ፰፡ ፲፭። †ም፡ ፲፬፡ ፲።
ኢሳ፡ ፵፩፡ ፰።

፲፮፤ እላንት፡ አልመረጣችሁኝም። *እኔ፡ እላንት ን፡ መረጥኋችሁ፤ እንጂ፡ አስነሣኋችሁም፡ ትሔዱ፡ ዘንድ፡ፍሬም፡ታፈሩ፡ዘንድ፡ፍሬያችሁም፡ ይኖር፡ዘን ድ። †በስሜ፡የለመናችሁትን፡ሁሉ፡ አብ፡ይሰጣችሁ፡ ዘንድ። *፩፡ ዮሐ፡ ፬፡ ፲። †ም፡ ፲፮፡ ፳፫።

፲፯፤ ይህቺን፡ አዝዝኋችሁ፡ እርሱ፡ በርሳችሁ፡ ትዋ ደዱ፡ ዘንድ።

፲፰፤ ዓለም፡ ቢጸላችሁ፡ አወቃችሁ፡ ከላንት፡ በፊ ት፡እኔ፡ እንደጸላኝ። ም፡ ፯፡ ፯።

፲፱፤ ከዓለምስ፡ ብትሆኑ፡ ዓለም፡ ከርሱ፡ ወገን፡ የ ሆነውን፡ይወድ፡ነበረ። ነገር፡ግን፡ ከዓለም፡ አይደላች ሁምና፡እኔ፡ከዓለም፡መረጥኋችሁ፡እንጂ።ስለዚህ፡ ዓለም፡ይጸላችኋል። ፩፡ ዮሐ፡ ፬፡ ፭። ዮሐ፡ ፲፯፡ ፲፬።

፳፤ እኔ፡ የነገርኋችሁን፡ ነገር፡አስቡ። ባርያ፡ ከጌታ ው፡አይበልጥም፡ብዬ። እኔን፡ አሳደውኝ፡ እንደሆን፡ እላንትንም፡ ያሳድዋችኋል። ቃሌን፡ ጠብቀው፡ እን ደ፡ሆኑ፡ቃላችሁንም፡ ይጠብቃሉ። ም፡ ፲፫፡ ፲፮።

፳፩፤ ነገር፡ ግን፡ ይህነን፡ ሁሉ፡ ያደርጉባችኋል፡ ስለ፡ ስሜ። የላከኝን፡ አያውቁምና። ም፡ ፲፮፡ ፫።

፳፪፤ ባልመጣሁም፡ ባልነገርኋቸውምም፡ ኃጢአ ት፡ባልሆነባቸውም።አሁን፡ግን፡ ምክንያት፡ የላቸው ም፡ ለኃጢአታቸው።

፳፫፤ የሚጸላኝ፡ አባቴን፡ ደግሞ፡ ይጸላል።
ም፡ ፭፡ ፲፫፥

፳፬፤ ባላደረግሁላቸውስ፡አንድ፡ ሰው፡ሌላ፡ ያላደ ረጋትን፡ስራ፡ኃጢአት፡ ባልሆነባቸውም። አሁን፡ ግን፡ እኔን፡ አዩኝ፡ ጸሉኝም፡ አባቴንም።

፳፭፤ ነገር፡ግን፡ ይህ፡ ሆነ፡በኦሪታቸው፡ የተጻፈው፡ ነገር፡ ለመፈጸም፡ እንዲህ፡ ሲል። በከንቱ፡ ጸሉኝ።
መዝ፡ ፷፱፡ ፬፥

፳፮፤ የሚያጸና፡ግን፡ *ጰራቅሊጦስ፡ በመጣ፡ ጊዜ፡ እኔ፡ለላንት፡የምሰደው፡ከአብ፡ዘንድ። የውነት፡መን ፈስ፡ከአብ፡የሚወጣ። †እርሱ፡ ስለኔ፡ ይመሰክራል።
*ም፡ ፲፬፡ ፳፮። †ኢዮ፡ ፫፡ ፩፥

፳፯፤ እላንትም፡ ደግሞ፡ ትመሰክራላችሁ፡ ከጥን ት፡ ከኔ፡ ጋራ፡ ነበራችሁና።

## ምዕራፍ፡ ፲፮፤

፩፤ ይህቺን፡ ነገርኋችሁ፡ እንዳትጠራጠሩ።

፪፤ ከመስጊደቸው፡ያወጥዋችኋል። ነገር፡ግን፡ጊዜ፡ ትመጣለች፡የገደላችሁ፡ሁሉ፡ለእግዚአብሔር፡ የሚ ያገለግል፡ እንዲመስለው። ማቴ፡ ፳፬፡ ፱፥
የሐዋ፡ ፰፡ ፩፥

፫፤ ይህቺንም፡ያደርጉባችኋል፡አብን፡ አያውቁም ና፡ እኔንም። ም፡ ፲፭፡ ፳፩፥

፬፤ ነገር፡ግን፡ይህቺን፡ነገርኋችሁ፡ ሰዓቱ፡ በደረሰ፡ጊ ዜ፡እንድታስበዋት፡ እንደልኋችሁ። ይህቺንም፡ ከጥ ንት፡አልነገርኋችሁም፡ ከላንት፡ ጋራ፡ ነበርሁና።

፭፤ ዛሬ፡ግን፡ወደ፡ላከኝ፡እሔደለሁ፡ከላንት፡ማን ም፡አይጠይቀኝም፡ ወዴት፡ ትሔደለህ፡ብሎ።
ም፡ ፯፡ ፴፫፥

፮፤ ነገር፡ ግን፡ ይህነን፡ ብላችሁ፡ አዘን፡ መላ፡ በልባ ችሁ።

፯፤ ነገር፡ግን፡ እውነት፡ እላችኋለሁ፡ መሔዴ፡ እን ዲሻላችሁ።እኔ፡ባልሔድ፡ጰራቅሊጦስ፡አይመጣላች ሁምና። የሔድሁ፡እንደሆን፡ግን፡ እርሱን፡ እሰድላች ኋለሁ። ም፡ ፲፬፡ ፳፮፥

፰፤ ያም፡በመጣ፡ጊዜ፡ዓለሙን፡ይዘልፈዋል፡ስለ፡ ኃጢአት፡ ስለ፡ጽድቅም፡ ስለ፡ፍርድም።

፱፤ ስለ፡ኃጢአት፡ግን፡ በኔ፡ አላመኑብኝምና።
ም፡ ፫፡ ፲፰፥

፲፤ ስለ፡ጽድቅም።ወደ፡አባቴ፡እሔደለሁና፡ደግማች ሁም፡ አታዩኝምና። የሐዋ፡ ፭፡ ፴፩፥

፲፩፤ ስለ፡ፍርድም። የዚህ፡ዓለም፡ መኰንን፡ ይፈ ረድበታልና። ም፡ ፲፪፡ ፴፩። ፲፬፡ ፴፥

፲፪፤ ደግሞ፡ብዙ፡ሌላ፡ነገር፡ አለኝ፡የምናግራችሁ። ነገር፡ ግን፡ አትችሉትም፡ዛሬ፡ ትሸከሙት፡ ዘንድ።

፲፫፤ ያም፡ የውነት፡ መንፈስ፡ በመጣ፡ ጊዜ፡ እርሱ፡ ወደ፡ *እውነት፡ሁሉ፡ ይመራችኋል፡ ከራሱ፡ አይናገር

ቃምና። የሚሰማውን፡ይናገራል፡እንጂ፡ የሚመጣው
ንም፡ ይገልጠላችኋል። *ም፡ ፲፬፡ ፲፯፡ ፳፮።
፩፡ ዮሐ፡ ፪፡ ፳፯።
፲፬፡ ያም፡ያመሰግነኛል። ከኔ፡ ይወስዷልና፡ ይነግራ
ችሁማል። ም፡ ፲፯፡ ፩።
፲፭፡ ለአብ፡ ያለ፡ ሁሉ፡ ለኔ፡ ነው። ስለዚህም፡ አል
ሁ።ያ፡ከኔ፡ይወስዷል፡ ይነግራችሁማል። ም፡ ፲፯፡ ፲።
፲፮፡ ጥቂት፡አታዩኝምም። ደግሞም፡ ጥቂት፡ ታዩ
ኛላችሁም፡ ወደ፡አብ፡ እሔዳለሁና። ም፡ ፲፬፡ ፲፱።
፲፯፡ ደቀ፡መዛሙርቱም፡ እርሱ፡ብርሳቸው፡አሉ።
ምንድር፡ ነው፡ ይህ፡ እርሱ፡ የሚለን። ጥቂት፡ አታዩኝ
ምም። ደግሞም፡ ጥቂት፡ ታዩኛላችሁ፡ወደ፡ አብም፡
እሔዳለሁና።
፲፰፡ አሉም፡ ምንድር፡ ነው፡ ይህ፡ ጥቂት፡ የሚለ
ው። አናውቅም፡ የሚናገርበትን።
፲፱፡ የሱስም፡አወቀ፡ ይጠይቁት፡ ዘንድ፡ እንዲወ
ዱ። አላቸውም። ስለዚህን፡ እርሱ፡ በርሳችሁ፡ ትመ
ራመራላችሁ፡ስላልሁ። ጥቂት፡ አታዩኝምም፡ ደግሞ
ም፡ ጥቂት፡ ታዩኛላችሁም።
፳፡ እውነት፡ እውነት፡ እላችኋለሁ። እላንተ፡ እን
ድታለቅሱ፡ እንድታዝኑም፡ ዓለም፡ ግን፡ ደስ፡ ይለዋ
ል።እላንተም፡ታዝናላችሁ፡ነገር፡ግን፡አዘናችሁ፡ወደ፡
*ደስታ፡ይለወጣል። *መዝ፡ ፴፡ ፲፪። ኤር፡ ፴፩፡ ፲፫።
፳፩፡ ሴት፡ በምትወልድበት፡ጊዜ፡ ታዝናለች፡ ጊዜ
ዋ፡ደርሶዋልና። ወንድ፡ልጅ፡ ግን፡በወለደች፡ ጊዜ፡ መ
ከራዋን፡ኋላ፡አታስበውም፡ስለ፡ደስታ።*ሰው፡በዓለ
ም፡ተወልዶዋልና። *ዘፍ፡ ፫፡ ፲፮። ኢሳ፡ ፳፮፡ ፲፯።
፳፪፡ እላንተም፡ ዛሬ፡አዘንተኞች፡ ናችሁ። ነገር፡ግ
ን፡ደግሞ፡አያችኋለሁ፡ልባችሁም፡ደስ፡ይለዋል።ደስ
ታችሁንም፡ ከላንተ፡ የሚወስደው፡ የለም።
ኢሳ፡ ፴፭፡ ፲። ፷፮፡ ፲፬።
፳፫፡ በዚያም፡ ቀን፡ አንዳች፡ አትጠይቁኝም። እ
ውነት፡እውነት፡ እላችኋለሁ። *ከአብ፡ የምትለምኑ
ትን፡ሁሉ፡በስሜ፡ እንዲሰጣችሁ። *ማር፡ ፲፩፡ ፳፬።
፳፬፡ እስከ፡ ዛሬ፡ አንዳች፡ አለመናችሁም፡ በስ
ሜ። ለምኑ፡ ይሰጣችኋልም፡ ደስታችሁ፡ እንዲፈጸ
ም። ም፡ ፲፭፡ ፲፩።
፳፭፡ ይህነን፡ነገርኋችሁ፡በምሳሌ። ነገር፡ ግን፡ ጊዜ፡
ይመጣል፡ ደግሞ፡ በምሳሌ፡ እንዳልነግራችሁ፡ ነገር፡
ግን፡ ስለ፡አብ፡ በግልጽ፡ እነግራችኋለሁ።
፳፮፡ በዚያ፡ቀን፡በስሜ፡ ትለምናላችሁ። የምላች
ሁም፡ አይደለሁም፡ አብን፡ ስለላንተ፡ እንድለምን።
፳፯፡ እርሱ፡አብ፡*ይወዳችኋልና። እላንተ፡ወዳች
ሁኛልና፡ †አምናችኋልምና፡ እኔ፡ ከእግዚአብሔር፡
እንደ፡ወጣሁ። *ም፡ ፲፬፡ ፳፩። †ም፡ ፲፯፡ ፰፡ ፳፭።
፳፰፡ ከአብ፡ወጣሁ። ወደ፡ዓለምም፡መጣሁ፡ደግ
ሞ፡ ዓለምን፡ እተዋለሁ፡ ወደ፡ አብም፡ እሔዳለሁ።
ም፡ ፲፫፡ ፫።
፳፱፡ ደቀ፡መዛሙርቱም፡ አሉት። እነሆ፡ ዛሬ፡ በ
ግልጥ፡ ትናገራለህ፡ አንድ፡ ምሳሌም፡ ስንኳ፡ አት
ልም። ቍ፡ ፳፭።
፴፡ ዛሬ፡አወቅነ፡በሁሉ፡ እንድታውቅ፡ ማንም፡ይ
ጠይቅህ፡ ዘንድ፡ አትሻም።በዚህ፡እናምናለን፡ከእግ
ዚአብሔር፡ እንደ፡ ወጣህ። ም፡ ፳፩፡ ፲፯።
፴፩፡ የሱስም፡ መለሰላቸው፡ አላቸውም። አሁን
ን፡ ታምናላችሁ።
፴፪፡ እነሆ፡ጊዜው፡ ይደርሳል፡ዛሬም፡ደረሰ፡ *ትበ
ተኑበት፡ዘንድ፡ከላንተ፡ኢያንዳንዱ፡ወደ፡ስፍራው።
ብቻዬንም፡ ትተውኛላችሁ። †ብቻዬንም፡ አይደለ
ሁም፡ አብ፡ ከኔ፡ ጋራ፡ነውና። *ዘካ፡ ፲፫፡ ፯።
†ም፡ ፰፡ ፲፮፡ ፳፱።
፴፫፡ ይህን፡ነገርኋችሁ፡ *በኔ፡ ሰላም፡ ይሆንላችሁ፡
ዘንድ።በዓለም፡ መከራ፡ያገኛችኋል። ነገር፡ግን፡ ጽኑ፡
እኔ፡ ዓለምን፡ †አሸነፍሁ። *ም፡ ፲፬፡ ፳፯።
ሮሚ፡ ፭፡ ፩። †ቆል፡ ፩፡ ፳። ፩፡ ዮሐ፡ ፭፡ ፬፡ ፭።

## ምዕራፍ፡ ፲፯፡

፩፡ ይህነን፡ ነገር፡ ተናገረ፡የሱስ፡ዓይኑንም፡ ወደ፡ሰ
ማይ፡አነሣ፡ አለም። አባት፡ ሆይ፡ጊዜው፡ አሁን፡ደረ
ሰ።ልጅህን፡ አመስግን፡ ልጅህም፡ ደግሞ፡ ያመሰግን
ህ፡ዘንድ። ም፡ ፲፩፡ ፵፩።
፪፡ *እንዲስገዛቸው፡ በሥጋ፡ ሁሉ፡ ላይ፡ የዘላለም፡
ሕይወት፡ ይሰጥ፡ ዘንድ፡ †ለሰጠኸው፡ ሁሉ።
*መዝ፡ ፰፡ ፯። ማቴ፡ ፲፩፡ ፳፯። †ም፡ ፮፡ ፴፯።
፫፡ የዘላለም፡ ሕይወትም፡ ይህች፡ናት። ያውቁህ፡
ዘንድ፡አንተ፡ብቻህ፡እውነተኛ፡*አምላክ፡ እንደሆን
ህ፡ የላክኸውም፡ የሱስ፡ ክርስቶስ።
ኤር፡ ፱፡ ፳፬። ፩፡ ዮሐ፡ ፭፡ ፳።
፬፡ እኔ፡ አመሰገንሁህ፡ በምድር፡ ላይ። የሰጠኸኝ
ን፡ ስራ፡አደርገው፡ ዘንድ፡ ፈጸምሁ። ም፡ ፬፡ ፴፬።
፭፡ አሁንም፡ አመስግነኝ፡ አንተ፡ አባት፡ ሆይ፡ ባን
ተ፡ዘንድ፡ከጥንት፡ወዳንተ፡ ዘንድ፡በነበረኝ፡ ምስጋና፡
ዓለም፡ ሳይፈጠር። ሚካ፡ ፭፡ ፩። ፊል፡ ፪፡ ፮።
፮፡ ስምህን፡ ገለጥሁ፡ ከዓለም፡ ለሰጠኸኝ፡ ሰዎ
ች። ላንተ፡ ነበሩ፡ ለኔም፡ ሰጠኻቸው፡ ቃልህንም፡ ጠ
በቁ። *ም፡ ፲፭፡ ፲፱።
፯፡ ዛሬ፡አወቁ፡የሰጠኸኝ፡ሁሉ፡ካንተ፡ዘንድ፡እን
ደ፡ሆነ።
፰፡ የሰጠኸኝን፡ነገር፡ሰጥቻቸዋለሁና። እርሳቸው
ም፡ተቀበሉት፡ በውነትም፡አወቁ፡እኔ፡ካንተ፡ ዘንድ፡
እንደ፡ ወጣሁ፡ አንተም፡እንደ፡ ላክኸኝ፡ አመኑ።
፱፡ እኔ፡ስለርሳቸው፡እለምናለሁ። ስለ፡ዓለም፡አ
ለምንም፡ ስለ፡ ሰጠኸኝ፡ እንጂ፡ ያንተ፡ ናቸውና።
ም፡ ፮፡ ፴፯፡ ፵፬።
፲፡ ለኔም፡ የሆነ፡ ሁሉ፡እርሱ፡ላንተ፡ ነው። ያንተው
ም፡ እርሱ፡ ለኔ፡ ነው። እኔም፡ በርሳቸው፡ ተመሰገኘ
ለሁ። ም፡ ፲፮፡ ፲፭።
፲፩፡ እኔም፡ ደግሞ፡ በዓለም፡ አልኖርም። እርሳቸ

ው፡ግን፡በዓለም፡ ናቸው፡ እኔም፡ ወደ ንተ፡ እመጣለ
ሁ። ቅዱስ፡ አባቴ፡ ሆይ፡ በስምህ፡ ጠብቃቸው፡ እሌ
ላህን፡ የሰጠኸኝን፡ አንድ፡ ይሆኑ፡ ዘንድ፡ እንደኛ።
ም፡ ፲፡ ፴።

፲፪፡ ከርሳቸው፡ጋራ፡ በዓለም፡ ሳለሁ፡ በስምህ፡ እ
ጠብቃቸው፡ነበርሁ፡እሌህን፡የሰጠህኝን፡ ፈጽሜ፡ጠ
ብቅኋቸው። ከርሳቸውም፡ አንድ፡ የጠፋ፡ የለም፡ከ
ጥፋት፡ ልጅ፡ በቀር፡ መጽሐፍ፡ ይፈጸም፡ ዘንድ።
ም፡ ፮፡ ፴፱። መዝ፡ ፵፩፡ ፲። ፻፱፡ ፰።

፲፫፡ ዛሬም፡ወደ ንተ፡ እመጣለሁ። ይህነንም፡ በዓ
ለም፡እናገራለሁ፡ደስታዬ፡በርሳቸው፡እንዲፈጸም።
ም፡ ፲፭፡ ፲፩።

፲፬፡ እኔ፡ ቃልህን፡ ሰጠኋቸው፡ ዓለምም፡ ጸላቸ
ው፡ ከዓለም፡ አይደሉምና፡ እኔ፡ ከዓለም፡ እንደይ
ደለሁ።

፲፭፡ ከዓለም፡ታወጣቸው፡ ዘንድ፡ አለምንም፡ ከ
ክፉ፡ ትጠብቃቸው፡ ዘንድ፡ እንጂ። ፪፡ ተሰ፡ ፫፡ ፫።

፲፮፡ ከዓለም፡አይደሉም። እኔ፡ከዓለም፡ እንደይ
ደለሁ።

፲፯፡ በውነትህ፡ቀድሳቸው። ቃልህ፡እርሱዋ፡እውነ
ት፡ ናት። ም፡ ፯፡ ፳፫።

፲፰፡ ወደ፡ዓለም፡ እንደ፡ ላክኸኝ፡ እኔ፡ ደግሞ፡ ወ
ደ፡ ዓለም፡ ላክኋቸው። ም፡ ፳፡ ፳፩።

፲፱፡ ስለርሳቸውም፡ ራሴን፡ እቀድሳለሁ፡ እርሳቸ
ውም፡ ደግሞ፡ የተቀደሱ፡ ይሆኑ፡ዘንድ፡ በውነት።
ዕብ፡ ፲፡ ፲።

፳፡ ስለ ለዚህም፡ብቻ፡ የምለምን፡አይደለሁም።
ደግሞ፡ በቃላቸውም፡ ስለሚያምኑብኝ፡ እንጂ።

፳፩፡ ሁሉ፡ *አንድ፡እንዲሆኑ። አንተ፡በኔ፡ እንደለ
ህ፡ አባት፡ ሆይ፡እኔም፡ ባንተ። እርሳቸውም፡ ደግሞ፡
አንድ፡ይሆኑ፡ ዘንድ፡በኛ። ዓለም፡ያምን፡ ዘንድ፡ አን
ተ፡እንደ፡ ላክኸኝ። *ገላ፡ ፫፡ ፳፰።

፳፪፡ እኔም፡ የሰጠኸኝን፡ መስጋና፡ ሰጠኋቸው፡አ
ንድ፡ ይሆኑ፡ ዘንድ፡ እኛ፡ አንድ፡ እንደ፡ ሆነ።
የሐዋ፡ ፬፡ ፴፪።

፳፫፡ እኔ፡በርሳቸው፡ አንተም፡በኔ። ባንድ፡ የተፈጸ
ሙ፡ይሆን፡ዘንድ። ዓለምም፡ያውቅ፡ዘንድ፡እንደ፡ላ
ክኸኝ፡እርሳቸውንም፡ እንደወደድኻቸው፡ እኔን፡እ
ንደ፡ ወደድኸኝ። ፩፡ ቀር፡ ፯፡ ፲፫፡

፳፬፡ አባት፡ሆይ፡እለዚህ፡የሰጠኸኝ፡ እወዳለሁ፡
እኔ፡ወዳለሁበት፡እርሳቸውም፡ደግሞ፡ከኔ፡ ጋራ፡ ይኖ
ሩ፡ ዘንድ፡ የሰጠኸኝን፡ክብር፡ያዩ፡ ዘንድ። ዓለም፡ ሳ
ይፀመር፡ ወደኸኛልና። ም፡ ፲፪፡ ፳፯።

፳፭፡ ጻድቅ፡ አባት፡ ሆይ፡ ዓለም፡ አያውቅህም።
እኔ፡ግን፡ አውቅሃለሁ። እሌህም፡ አወቁ፡ አንተ፡ እን
ደ፡ላክህኝ።

፳፮፡ ስምህንም፡ አስታወቅኋቸው፡ ደግሞም፡ አ
ስታውቃቸዋለሁ። የወደድህኝ፡ ውድ፡ በርሳቸው፡ ይ
ሆን፡ዘንድ፡ እኔም፡ በርሳቸው።

ምዕራፍ፡ ፲፰፡

፩፡ ይህነን፡ብሎ፡ የሱስ፡ ከደቀ፡ መዛሙርቱ፡ ጋራ፡
ወጣ፡እታክልት፡ወዳለበት፡ ስፍራ፡በቄድሮን፡ወንዝ፡
ማዶ። ወደርሱዋም፡ ገባ፡ ከደቀ፡ መዛሙርቱ፡ ጋራ።
ማቴ፡ ፳፮፡ ፴፮። ፪፡ ሳሙ፡ ፲፭፡ ፳፫።
ማቴ፡ ፳፮፡ ፵፯፡—፶፯።
ማር፡ ፲፬፡ ፵፫፡—፶፪። ሉቃ፡ ፳፪፡ ፵፯፡—፶፫።

፪፡ ይሁዳም፡ያስያዘው፡ደግሞ፡ያነን፡ስፍራ፡ ያው
ቅ፡ነበረ። *የሱስ፡ ብዙ፡ጊዜ፡ ወደዚያ፡ይሔድ፡ ነበርና፡
ከደቀ፡ መዛሙርቱ፡ ጋራ። *ሉቃ፡ ፳፩፡ ፴፯።

፫፡ ይሁዳም፡ ጭፍራ፡ ወስዶ፡ ወታደርም፡ ከካህና
ት፡አለቆች፡ ከፈሪሳውያንም፡ወደዚያም፡ መጡ፡ ፋ
ኑስና፡ ፋና፡ ይዘው፡ ጋሻና፡ ጦርም።

፬፡ *የሱስም፡ የሚመጣበትን፡ ሁሉ፡ ባወቀ፡ ጊዜ፡
ወጣ፡አላቸውም። ማነን፡ትሻላችሁ። *ም፡ ፲፱፡ ፳፰።

፭፡ መለሱለት፡አሉትም። የሱስን፡የናዝሬቱን። የ
ሱስም፡አላቸው። *እኔ፡ነኚ። ይሁዳም፡ያስያዘው፡ከር
ሳቸው፡ ጋራ፡ ቁሞ፡ ነበረ። ም፡ ፯፡ ፳።

፮፡ ባላቸውም፡ጊዜ። እኔ፡ነኝ። ወደ፡ኋላቸው፡ተመ
ለሱ፡ በምድር፡ ላይም፡ ወደቁ።

፯፡ ደግሞም፡ ጠየቃቸው፡ እንደሁ፡ ሲል ። ማነን፡
ትሻላችሁ። እርሳቸውም፡ አሉ። የሱስን፡የናዝሬቱን።

፰፡ የሱስም፡መለሰ፡ አላቸውም። አልኋችሁ፡እኔ፡
ነኝ። እኔንም፡ ትሹኝ፡ እንደ፡ ሆናችሁ፡ ተው፡ እለዚህ፡
ይሒዱ።

፱፡ ያላት፡ ነገር፡ትፈጸም፡ ዘንድ። እርሳቸውን፡ የሰ
ጠኸኝን፡ ከርሳቸው፡ አንድ፡ ስንኳ፡ አላጠፋሁም።
ም፡ ፲፯፡ ፲፪።

፲፡ ከሲሞን፡ ጴጥሮስ፡ ጋራም፡ ሰይፍ፡ ነበረ፡ መዘዘ
ውም፡የካህናቱን፡አለቃ፡ባርያም፡መታ፡ ቀኝ፡ጆሮው
ንም፡ቈረጠ። የባርያውም፡ ስም፡ ማልኮስ፡ ነበር።

፲፩፡ የሱስም፡ ጴጥሮስን፡ አለው ። ሰይፍህን፡ ወደ
ፎቱ፡ ክተተው። አባቴ፡ የሰጠኝን፡ *ጽዋ፡ አልጠጣት
ምን። *ማቴ፡ ፳፮፡ ፶፪።
ማቴ፡ ፳፮፡ ፶፯፡—፷፰። ማር፡ ፲፬፡ ፶፫፡—፷፪።
ሉቃ፡ ፳፪፡ ፶፬፡—፷፩።

፲፪፡ ጭፍራም፡የሻለቃም፡የአይሁድም፡ሎሌልት፡
የሱስን፡ ያዙ፡ አሠሩትም።

፲፫፡ አስቀድሞም፡ ወደ፡ ሐና፡ አመጡት። በዚያ፡
አመት፡የካህናት፡አለቃ፡የነበረው፡ የቀያፋ፡ አማች፡
ነበርና።

፲፬፡ *ቀያፋም፡ ለአይሁድ፡ የመከራቸው፡ ነው፡አ
ንድ፡ሰው፡ ስለ፡ሕዝብ፡ ይሞት፡ ዘንድ፡እንዲሻል።
*ም፡ ፲፩፡ ፶።

፲፭፡ ሲሞን፡ጴጥሮስም፡ የሱስን፡ይከተል፡ ነበር፡ሌ
ላውም፡ደቀ፡መዝሙር። ያ፡ግን፡ደቀ፡መዝሙር፡በካ
ህናቱ፡ አለቃ፡ ዘንድ፡ የታወቀ፡ ነበረ፡ ከየሱስ፡ ጋራም፡
ገባ፡ ወደ፡ ካህናቱ፡ አለቃ፡ ቤት። ም፡ ፳፡ ፪፡—፰።

፲፮፤ ጴጥሮስ፡ግን፡ወደ፡ በር፡ቁሞ፡ነበረ፡በሚደ። ሌ ላውም፡ደቀ፡መዝሙር፡ ወጣ፡ በካህናቱ፡ አለቃ፡ ዘን ድ፡ታውቀ፡የነበረው።ለበረኞዪቱም፡ ነገራት፡ጴጥሮስ ንም፡ አስገባው።

፲፯፤ በረኞዪቱም፡ገርደ፡ጴጥሮስን፡አለችው፡አንተ ምን፡ ደግሞ፡ የዚያ፡ ሰው፡ ደቀ፡ መዛሙርት፡ ወገን፡ ነህ። ያም፡ አለ፡ እኔ፡ አይደለሁም።

፲፰፤ ሎሌልትም ፡ ጭፍሮችም፡ እሳት፡ አንድደው፡ ይሞቁም፡ ነበሩ፡ ብርድ፡ ነበርና። ጴጥሮስም፡ ከርሳቸ ው፡ጋራ፡ቁሞ፡ይሞቅ፡ ነበር። ሉቃ፡ ፳፪፡ ፶፭።

፲፱፤ የካህናት፡ አለቃ፡ ግን፡ የሱስን፡ ጠየቀ፡ ስለ፡ደ ቀ፡መዛሙርቱ፡ ስለ፡ ትምህርቱም።

፳፤ የሱስም፡ መለሰ፡ አለም። እኔ፡ለዓለም፡ በግል ጥ፡ተናገርሁ።እኔ፡አስተማርሁ፡ዕለት፡ዕለት፡በመስጊ ድ፡በመቅደስም፡አይሁድ፡ሁለግዜ፡ወደሚከማቹበ ት። ምንም፡ *በሥውር፡ አልተናገርሁም።

ም፡ ፯፡ ፳፮። *ኢሳ፡ ፵፭፡ ፲፱።

፳፩፤ ምናግደህ፡ትጠይቀኛለህ። ነገሬን፡ የሰሙት ን፡ ጠይቅ ። እነሆ፡ እሌህ፡ የነገርኋቸውን፡ ያውቃሉ።

፳፪፤ ይህነንም፡ባለ፡ጊዜ፡ ከሎሌልት፡ አንዱ፡ ከዚ ያ፡ቁሞ፡የነበረው፡ የሱስን፡በጥፊ፡መታው፡ እንደህ፡ ሲል። እንዴህን፡ ትመልሳለህ፡ ለካህናቱ፡ አለቃ።

ኢሳ፡ ፶፡ ፮። ሚክ፡ ፭፡ ፲፭።

፳፫፤ የሱስም፡ መለሰለት፡ አለውም። ክፉ፡ ተናግ ሬ፡ እንደ፡ ሆንሁ፡ በክፉ፡ መስክር ። መልካምም ፡ ከ ሆነ፡ ለምን፡ ትመታኛለህ። ፩፡ ጴጥ፡ ፫፡ ፲፭፡ ፲፮።

፳፬፤ ሐናም፡ወደ፡ ቀያፋ፡ ወደ፡ካህናት፡ አለቃ፡ እ ንደ ፡ ታሠረ ፡ ሰደደው።

፳፭፤ ሲሞን፡ጴጥሮስም፡ቁሞ፡እሳት፡ ይሞቅ፡ ነበ ረ።አሉትም።አንተምን፡ደግሞ፡ከደቀ፡መዛሙርቱ፡ ነህ። እርሱም፡ ካደ፡ አለም፡ እኔ፡ አይደለሁም።

ቍ፡ ፲፰።

፳፮፤ ከካህናት፡ አለቃ ፡ ሎሌልትም ፡ አንዱ ፡ አለ፡ ጴጥሮስ፡ጆሮውን፡ የቈረጠው፡ ዘመድ። እኔ፡ አላየሁ ህምን፡ ከርሱ፡ ጋራ፡ ባታክልት።

፳፯፤ ጴጥሮስም፡ ደግሞ፡ ካደ። በዚያን፡ጊዜም፡ዶ ሮ፡ጮኸ።

ማቴ፡ ፳፯፡ ፪—፴፩። ማር፡ ፲፭፡ ፩—፳፡ ሉቃ፡ ፳፫፡ ፩—፳፭።

፳፰፤ የሱስንም፡ ከቀያፋ፡ ወደ፡ ፍርድ፡ ሸንጎ፡ወሰ ዱት።ማልደም፡ነበረ።እርሳቸውም፡ወደ፡ፍርድ፡ሸን ጎ፡ አልገቡም፡ እንዳይረክሱ፡ ፋሲካን፡ እንዲበሉት፡ እንጂ።

፳፱፤ ጲላጦስም፡ ወደርሳቸው፡ወጣ፡ አለም። ም ን፡ ኃጢአት፡ትናገሩላችሁ፡ በዚህ፡ ሰው።

፴፤ መለሱ፡ አሉትም። ይህ፡ ክፉ፡ ያደረገ፡ ባይሆን ስ፡ ወደንተ፡ ባላመጣነውም።

፴፩፤ ጲላጦስም ፡ አላቸው ። ውሰዱት ፡ እላንት፡ ፍረዱበትም፡ እንደ፡ ሕጋችሁ ። አይሁድም፡ አሉ። ሌ ኛ፡ አይገባንም ፡ ማንንም፡ እንገድል፡ ዘንድ።

ም፡ ፲፱፡ ፯፡ ፰።

፴፪፤ የየሱስ፡ቃል፡ይፈጸም፡ዘንድ፡ ያለው፡ በማና ቸው፡ ሞት፡ እንዲሞት፡ አመልክቶ።

ም፡ ፲፪፡ ፴፪፡ ፴፫። ማቴ፡ ፳፡ ፲፱።

፴፫፤ ጲላጦስም፡ ደግሞ፡ወደ፡ፍርድ፡ ሸንጎ፡ገባ፡ የ ሱስንም፡ጸራ፡አለውም። አንተን፡ ነህ፡ የአይሁድ፡ ን ጉሥ።

፴፬፤ የሱስም፡ መለሰለት፡ አለውም። አንተን፡ከ ልብህ፡ ይህነን፡ ትናገራለህ ፡ ወይስ፡ ሌሎች ፡ ስለኔ፡ አ ሉህ።

፴፭፤ መለሰ፡ጲላጦስ፡አለም። በውኑ፡እኔ፡ አይሁ ደዊ፡ ነኝ። ወገኖችህ፡ የካህናትም፡ አለቆች፡ ወደኔ፡አ መጡህ። ምን፡ አድርገሃል።

፴፮፤ መለሰ፡ የሱስ፡ አለውም ። መንግሥቴ ፡ ከዚ ህ፡ ዓለም ፡ አይደለችም ። መንግሥቴስ፡ ከዚህ፡ ዓለ ም፡ ብትሆን፡ ሎሌልቴ፡ ይዋጉልኝ፡ ነበሩ፡ ወደ፡ አይሁ ድ፡እንዳልሰጥ።አሁን፡ግን፡መንግሥቴ፡ከዚህ፡አይደ ለችም።

፴፯፤ ጲላጦስም ፡ አለው ። እንኪያስ፡ አንተ፡ ንጉ ሥ፡ ነህ። መለሰ፡የሱስ፡አለም። *አንተ፡ትላለህ፡ እኔ፡ ንጉሥ፡ እንደ፡ ሆንሁ። እኔ፡ ስለዚህ፡ ተወለድሁ፡ ስለ ዚህም ፡ ወደ፡ ዓለም፡ መጣሁ፡ ለውነት፡ እመሰክር፡ ዘንድ።†ከውነት፡ የሆነ፡ ሁሉ፡ ቃሌን፡ ይሰማል።

*፩፡ ጢሞ፡ ፮፡ ፲፫። †ም፡ ፰፡ ፵፡ ፵፯።

፴፰፤ ጲላጦስ፡አለው። እውነት፡ምንድር፡ነው።ይ ህነንም፡ ብሎ፡ደግሞ፡ወደ፡ አይሁድ፡ ወጣ፡ አላቸው ም ። እኔስ፡ አንዲት ፡ ኃጢአት ፡ ስንኳ ፡ አላገኘሁበ ትም። ሉቃ፡ ፳፫፡ ፬፡ ፲፬።

፴፱፤ ለላንት ፡ ግን፡ ልማድ፡ አላችሁ፡ አንድ፡ ሰው፡ በየፋሲካው፡እተውላችሁ፡ዘንድ። የአይሁድን፡ ንጉ ሥ፡ እተውላችሁ ፡ ዘንድ፡ ትወዳላችሁን።

ማቴ፡ ፳፯፡ ፲፭።

፵፤ ሁሉም፡ ደግሞ፡ ጮሁ፡ እንዴህ፡ ሲሉ። ይህነን፡ አይደለም ፡ በርባንን ፡ እንጂ ። በርባንም ፡ ወንበዴ፡ ነበር። የሐ፡ ፫፡ ፲፬።

## ምዕራፍ፡ ፲፱፤

፩፤ የዚያን፡ጊዜ፡ጲላጦስ፡ የሱስን፡ወስደው፡ገረፈ ውም።

፪፤ ጭፍሮችም ፡ የሾህ፡ አክሊል ፡ ጐነጐኑ ፡ በራሱ ም፡ አኖሩት፡ቀይ፡ ልብስም፡ አለበሱት።

፫፤ አሉትም።እንዴት፡ነህ፡የአይሁድ፡ንጉሥ። በጥ ፊም፡ ይመቱት፡ ነበር።

፬፤ ጲላጦስም፡ ደግሞ፡ወደ፡ ሜደ፡ወጣ፡ አላቸው ም። እነሆ፡ይህነን፡ ሰው፡ ሜደ፡ አወጣላችኋለሁ። ታ ውቁ፡ዘንድ፡እንዳላገኘሁበት፡ አንዲት፡ ስንኳ፡ኃጢ አት።

፭፤ የሱስም፡ ወደ፡ ሜደ፡ ወጣ፡ የሾህ፡ አክሊል፡ቀደ፡ልብስም፡ለብሶ። አላቸውም ። እነሆት፡ ያ፡ ሰው።

መዝ፡ ፳፪፡ ፯፡፡ ኢሳ፡ ፶፫፡ ፫፡፡

፮፤ ባዩትም፡ጊዜ፡የካህናቱ፡ አለቆች፡ ሎሌልትም፡ ጮሁ፡ እንደህ፡ ሲሉ ። ስቀለው ። ጲላጦስም ፡ አላቸው። እላንት፡ወስዳችሁ፡ ስቀሉት፡ እኔ፡ኃጢአት፡ አላገኘሁበትምና።

፯፤ አይሁድም፡መለሱለት፡አሉትም።ሕግ፡አለነ፡ በሕጋችንም ፡ እንደ፡ ተጻፈው፡ ለርሱ፡ ሞት፡ ይገባዋል፡ ራሱን፡ የእግዚአብሔር፡ ልጅ፡ አድርጓልና።

ዘሌዋ፡ ፳፬፡ ፲፭፡ ፲፮፡፡

፰፤ ጲላጦስም፡ ይህነን፡ ነገር ፡ በሰማ፡ ጊዜ፡ አብዝቶ፡ፈራ።

፱፤ ደግሞም፡ወደ፡ ፍርድ፡ ሸንጎ፡ገባ፡ የሱስንም፡አለው። አንተ፡ ከወዴት፡ ነህ። *የሱስ፡ ግን፡ምላሽ፡ አልሰጠውም።

*ማቴ፡ ፳፯፡ ፲፪፡፡

፲፤ ጲላጦስም፡አለው። አትነግረኝምን። አታውቅምን ፡ እንዲቻለኝ፡ እሰቅልህ ፡ ዘንድ ፡ እተውህም፡ ዘንድ።

፲፩፤ መለሰ፡የሱስ፡አለም። በኔ፡አይቻልህም፡ ከሰማይ፡ ካልተሰጠህ። ስለዚህም፡ ላንተ፡ አሳልፎ፡ የሰጠኝ፡ ኃጢአቱ፡ የሚበልጥ፡ ነው።

፲፪፤ ስለዚህም፡ጲላጦስ፡ይተወው፡ዘንድ፡ወደደ፡ አይሁድ፡ግን፡ይጮሁ፡ነበሩ፡እንደህ፡ ሲሉ። ይህነንስ፡ ብትተወው፡ የቄሣር፡ ወዳጅ ፡ አይደለህም ። ራሱን፡ ንጉሥ፡ የሚያደርግ፡ ሁሉ፡ እርሱ፡ የቄሣርን፡ ነገር ፡ ይሽራል።

፲፫፤ ጲላጦስም፡ይህነን፡ነገር፡በሰማ፡ጊዜ፡የሱስን፡ ወደ፡ሜደ፡አወጣው። በወንበርም፡ተቀመጠ፡ ጸፍጸፍ፡ በሚሉት፡ ስፍራ፡ በዕብራይስጥም፡ ገበታ።

፲፬፤ ለፋሲካ፡ መሰናዳትም፡ነበረ፡ ጊዜውም፡ ስድስት፡ሰዓት፡ነበረ።አይሁድንም፡ አላቸው። እነሆ፡ንጉሣችሁ።

፲፭፤ እርሳቸው፡ግን፡ጮሁ፡እንደህ፡ ሲሉ። አስወግደው፡አስወግደው፡ስቀለው። ጲላጦስም፡አላቸው። ንጉሣችሁን፡ ልስቀለው ። የካህናቱ፡ አለቆች፡ መለሱ፡ አሉትም ። ንጉሥ፡ የለነም፡ ከቄሣር፡ በቀር።

፲፮፤ የዚያን፡ጊዜም፡አሳልፎ፡ ሰጣቸው፡ ሊሰቀል። የሱስንም ፡ ተቀበሉት ፡ ይዘውትም ፡ ሔደ።

ማቴ፡ ፳፯፡ ፴፩፡—፵፡፡ ማር፡ ፲፭፡ ፳፡—፴፩፡፡
ሉቃ፡ ፳፫፡ ፳፮፡—፵፮፡፡

፲፯፤ መስቀሉንም፡ ተሸክሞ፡ ወጣ፡የራስ፡ቅል፡ ወደሚሉት፡ ስፍራ፡ በዕብራይስጥ፡ ጎልጎታ፡ የሚባል።

ዘፍ፡ ፳፪፡ ፮፡፡

፲፰፤ ከዚያም፡ ሰቀሉት፡ ከርሱም ፡ ጋራ፡ ሌሎችን፡ ሁለት፡ በዚህና፡ በዚያ፡ የሱስንም፡ በመካከላቸው።

ማር፡ ፲፭፡ ፳፯፡፡

፲፱፤ ጲላጦስም፡ ጽፈትን፡ ጻፈ፡ በመስቀሉም፡አኖራት።ተጽፎም፡ ነበረ፡ እንደህ፡ ሲል። የሱስ፡ የናዝሬቱ፡ የአይሁድ፡ ንጉሥ።

፳፤ ይህነንም፡ ጽፈት፡ ከአይሁድ፡ብዙ፡ አነበቡት፡ የሱስ፡ የተሰቀለበት፡ ስፍራ፡ ላገር ፡ ቅርብ፡ ነበርና ። ተጽፎም ፡ ነበረ ፡ በዕብራይስጥ ፡ ልሳን፡ በፅርዕም ፡ በሮምም።

፳፩፤ የአይሁድም፡ ካህናት ፡ አለቆች፡ ጲላጦስን፡ አሉት።አትጻፍ፡እርሱ፡የአይሁድ፡ንጉሥ፡እንደ፡ሆነ፡ ነገር፡ ግን ፡ እርሱ ፡ አለ፡ እኔ ፡ የአይሁድ ፡ ንጉሥ፡ ነኝ።

፳፪፤መለሰ፡ጲላጦስ፡አለም።የጻፍሁትን፡ጻፍሁ።

፳፫፤ ጭፍሮች፡ ግን ፡ የሱስን ፡ በሰቀሉት፡ ጊዜ፡ ልብሶቹን፡ ወሰዱ ፡ ላራት፡ ክፍልም ፡ አደረጉት፡ ከጭፍሮች፡ለያንዳንዱ፡ ክፍል። *ቀሚሱንም፡ ደግሞ። ቀሚሱም፡ያልተሰፋ፡ ነበረ። የተሰራ፡ ነበር፡ እንጂ፡ሁሉ፡ከላይ፡ ጀምሮ።

*መዝ፡ ፳፪፡ ፲፰፡፡

፳፬፤እርሱ፡በርሳቸውም፡አሉ።አንቅደደው፡ነገር፡ ግን፡ዕፃ፡ እንጣጣልበት፡ ስለርሱ፡ ለማንም፡ ይድረሰው። ይፈጸም፡ ዘንድ፡ መጽሐፍ፡ ያለው ። ልብሶቼን፡ እርሱ፡በርሳቸው፡ተካፈሉ፡ በቀሚሴም፡ላይ፡ ዕፃ፡ተጣጣሉ። ጭፍሮችም፡ እንደህ፡ አደረጉ።

፳፭፤ ከየሱስ ፡ መስቀል ፡ አጠገብም፡ ቁመው፡ ነበሩ፡እናቱ፡የናቱም፡እኅት፡ማርያም፡የቀሌዮጳ፡ምሽት፡ ማርያምም፡ የመግደላዊቱ።

፳፮፤ የሱስም፡ እናቱን፡ ባየ፡ ጊዜ ፡ የቀመውንም፡ ደቀ፡መዝሙሩን፡ *ይወደው፡ የነበረውን፡እናቱን፡ አላት። አንቺ፡ ሴት፡ እነሆት፡ ልጅሽ።

*ም፡ ፲፫፡ ፳፫፡፡

፳፯፤ ደቀ፡መዝሙሩንም፡አለው። እነኋት፡እናትህ። ከዚያችም፡ሰዓት፡ጀምሮ፡ደቀ፡መዝሙሩ፡ወደ፡ ቤቱ፡ ወሰዳት።

፳፰፤ ከዚህም፡ በኋላ፡ *የሱስ፡ ባወቀ፡ ጉዜ፡ ሁሉ፡ እንደ፡ ተፈጸመ ፡ በመጽሐፍ፡ ያላው፡ ይፈጸም፡ ዘንድ፡ አለ። እኔ፡ ተጸማሁ።

*ም፡ ፲፯፡ ፬፡፡
መዝ፡ ፳፪፡ ፲፮፡፡

፳፱፤ ከዚያም፡እቃ፡ ተቀምጦ፡ ነበረ፡መጻጻ፡ የመላበት። እርሳቸውም፡ *መጻጻውን ፡ በስፍነጉ፡ መሉ፡ በስምዕዛ፡ ዘንግም፡ አኖሩት፡ ወደ፡አፉም፡ አቀረቡት።

*መዝ፡ ፷፱፡ ፳፪፡፡

፴፤ የሱስም፡ መጻጻውን፡ በቀመሰ፡ጊዜ፡አለ። *ተፈጸመ። ራሱንም፡ አዘነበለ፡ ነፍሱንም፡ ሰጠ።

ዕብ፡ ፭፡ ፱፡፡

፴፩፤ አይሁድ፡ግን፡ሥጋቸው፡ በመስቀል፡ላይ፡እንዳያድር፡በሰንበት። ዓርብ፡ቀን፡ነበረና። የዚያም፡ ሰንበት፡ቀን፡ ታላቅ፡ ነበረና። ጲላጦስን፡ ለመኑት፡ ጭናቸውን፡ይሰብሩ፡ ዘንድ ፡ ያወርድዋቸውም፡ ዘንድ።

ዘፀአ፡ ፴፬፡ ፳፭፡፡ ዘዳግ፡ ፳፩፡ ፳፫፡፡

፴፪፤ ጭፍሮችም፡ መጡ ፡ የፊተኛውንም ፡ ጭን፡ ሰበሩ፡ የሌላውንም፡ ከርሱ፡ ጋራ፡ የተሰቀለውን።

፴፫፤ ወደ፡የሱስ፡ግን፡ በመጡ፡ጊዜ፡ እርሱም፡ እንደ፡ ሞተ፡ ባዩ፡ጊዜ፡ ጭኑን፡ አልሰበሩም።

፴፬፡ ነገር፡ግን፡አንድ፡ ከጭፍሮች፡ጐኑን፡ በጦር፡ ወጋው። የዚያን፡ ጊዜም፡ ወጣ፡ ደምና፡ ውኃ።

፴፭፡ ያየውም፡መሰከረ፡ ምስክሩም፡ እውነት፡ ነ ት። እርሱም፡ያውቃል፡እውነት፡እንደ፡ተናገረ፡እላን ት፡ ታምኑ፡ ዘንድ።

፴፮፡ ይህም፡የሆነ፡ይፈጸም፡ዘንድ፡ *መጽሐፉ፡ያለው፡ አጥንቱን፡ ከርሱ፡ አይሰብሩም።

*ዘፀአ፡ ፲፪፡ ፵፮፡፡

፴፯፡ ደግሞም፡ሌላ፡መጽሐፉ፡ይላል። የወጉትን፡ ያዩታል። ዘካ፡ ፲፪፡ ፲፡፡ ራእ፡ ፩፡ ፯፡፡

፴፰፡ ከዚህም፡በኋላ፡ ዮሴፉ፡ ያርማቴሙ፡ለየሱስ፡ደቀ፡መዝሙር፡ የነበረው፡ተሠውሮ፡ግን፡አይሁድን፡ስለ፡ ፈራ። ጲላጦስን፡ ለመነው፡ የየሱስን፡ ሥጋ፡ይወስድ፡ ዘንድ፡ ጲላጦስም፡አዘዘው። መጣም፡ የየሱስንም፡ ሥጋ፡ ወሰደ። ማቴ፡ ፳፯፡ ፶፯፡—፷፩፡፡

ማር፡ ፲፭፡ ፵፪፡—፵፯፡፡ ሉቃ፡ ፳፫፡ ፶፡—፶፭፡፡

፴፱፡ ኒቆዲሞስም፡ ደግሞ፡ መጣ፡ ወደ፡ የሱስ፡ *ከሌት፡አስቀድሞ፡ የመጣው፡ †የከርቤና፡ የሰብር፡ ቅልቅል፡ መቶ፡ ረጥል፡ የሚያህል፡ አመጣ።

*ም፡ ፲፡ ፪፡፡ *ማቴ፡ ፪፡ ፲፩፡፡

፵፡ የየሱስንም፡ ሥጋ፡ ወሰዱ፡ በበፍታም፡ ጠቀለሉት፡ ከሽቱ፡ ጋራ፡ እንደ፡ አይሁድ፡ ልማድ፡ በመቃብራቸው።

፵፩፡ በተሰቀለበቱም፡ ቦታ፡ አታክልት፡ ነበረ፡ ባታክልቱም፡ አዲስ፡ መቃብር፡ነበረ፡ ማንም፡ ከቶ፡ ያልገባበት። ኢሳ፡ ፶፫፡ ፱፡

፵፪፡ ከዚያም፡የሱስን፡አኖሩት፡ስላርብ፡ማዘጋጀት፡ለአይሁድ። መቃብሩ፡ቅርብ፡ ነበርና።

ምዕራፍ፡ ፳፡

፩፡ ከሰንበትም፡ በመጀመርያው፡ ቀን፡ መጣች፡ ማርያም፡ የመግደላዊቱ፡ማልዶ፡ወደ፡ መቃብር፡ገና፡ ጨለማ፡ ሳለ። ደንጊያውንም፡ ከመቃብር፡ ተፈንቅሎ፡ አየች። ማቴ፡ ፳፰፡ ፩፡—፲፡፡ ማር፡ ፲፮፡ ፩፡—፲፩፡፡ ሉቃ፡ ፳፬፡ ፩፡—፲፪፡፡

፪፡ እርስዋም፡ፈጠነች፡ ወደ፡ ሲሞን፡ ጴጥሮስም፡ መጣች፡ ወደ፡ ሁለተኛውም፡ደቀ፡መዝሙር፡የሱስ፡ ይወደው፡የነበረው፡አለቻቸውም። ጌታን፡ከመቃብር፡ አነሡት፡ ወዴትም፡ እንደ፡ተውት፡ አናውቅም።

ም፡ ፲፫፡ ፳፫፡፡

፫፡ ጴጥሮስም፡ወጣ፡ሁለተኛውም፡ደቀ፡መዝሙር፡ ወደ፡ መቃብርም፡ መጡ።

፬፡ እርሳቸውም፡ ሁለቱ፡ባንድ፡ ይሮጡ፡ ነበሩ። ሁለተኛውም፡ ደቀ፡ መዝሙር፡ ጴጥሮስን፡ ቀደመው፡ አስቀድሞም፡ ወደ፡ መቃብር፡ መጣ።

፭፡ ዝቅም፡ አለ፡ ከፈኑንም፡ ተቀምጦ፡ አየ፡ነገር፡ ግን፡ አልገባም። ም፡ ፲፱፡ ፵፡፡

፮፡ ሲሞን፡ ጴጥሮስም፡ ሲከተለው፡ መጣ፡ ወደ፡ መቃብርም፡ገባ፡ ከፈኑንም፡ተቀምጦ፡ አየ።

፯፡ በራሱ፡ላይም፡የነበረ፡ *መጠምጠምያ፡ከከፈኑ፡ ጋራ፡ አልነበረም፡ ነገር፡ግን፡ለብቻው፡ ተጠቅልሎ፡ ነበረ። *ም፡ ፲፩፡ ፵፬፡፡

፰፡ የዚያን፡ ጊዜም፡ ደግሞ፡ ገባ፡ሁለተኛው፡ደቀ፡ መዝሙር፡ አስቀድሞ፡ ወደ፡ መቃብር፡ የመጣው፡ አየም፡ አመነም።

፱፡ በመጽሐፉ፡ያለውን፡ገና፡አላወቁምና፡ *ከሙታን፡ ይነሣ፡ ዘንድ፡ እንደለው። *መዝ፡ ፲፮፡ ፲፡፡

፩፡ ቆሮ፡ ፲፭፡ ፬፡፡

፲፡ ደቀ፡ መዛሙርትም፡ ደግሞ፡ ወደ፡ ቤታቸው፡ ሔዱ።

፲፩፡ ማርያም፡ ግን፡ ወደ፡ መቃብር፡ ቁማ፡ ቀረች፡ በሚያ፡ኢያለቀሰች። እርስዋም፡ስታለቅስ፡ወደ፡ መቃብር፡ ጐበኘች።

፲፪፡ ሁለት፡ መላእክትም፡ ነጭ፡ ልብስ፡ ለብሰው፡ አየች። ተቀምጠው፡ አንዱ፡በራሱጌ፡ሁለተኛውም፡ በግርጌ፡ የየሱስ፡ ሥጋ፡ ተቀምጦበት፡ ወደ፡ ነበረው።

፲፫፡ እሊያም፡ አልዋት። አንች፡ ሴት፡ ምነው፡ታለቅሻለሽ። አለቻቸውም። ጌታዬን፡ወስደውታልና፡ ወዴት፡ እንደ፡ ተውትም፡ አላውቅም።

፲፬፡ ይህነንም፡ ብላ፡ ወደ፡ ኋላዋ፡ ተመለሰች፡ የሱስንም፡ ቁሞ፡ አየች፡ የሱስም፡ እንደ፡ ሆነ፡ አላወቀችም። ማቴ፡ ፳፰፡ ፱፡፡

፲፭፡ የሱስም፡ አላት። አንች፡ሴት፡ ለምን፡ ታለቅሻለሽ። ማነንስ፡ ትሻለሽ። እርስዋም፡ መሰላት፡ አታክልት፡ ጠባቂ፡ እንደ፡ ሆነ፡ አለችውም። ጌታ፡ ሆይ። አንተ፡ አንስተህውም፡እንደ፡ሆንህ፡ ንገረኝ፡ወዴት፡ ተውህው፡ እኔም፡ ልውሰደው።

፲፮፡ የሱስም፡አላት። ማርያም። እርስዋም፡ተመለሰች፡ አለችውም። ረቡኒ፡ ትርጓሚውም፡ መምህር፡ ሆይ። ማር፡ ፲፡ ፶፩፡፡

፲፯፡ የሱስም፡ አላት። *አትንኪኝ፡ገና፡ ወደ፡ አባቴ፡ አልወጣሁምና። ነገር፡ ግን፡ ወደ፡ ወንድሞቼ፡ ሒጂ፡ በያቸውም። እወጣለሁ፡ወደ፡አባቴ፡አባታችሁም። ወ ደ፡አምላኬም፡ አምላካችሁም። *ማቴ፡ ፳፰፡ ፱፡ ፲፡፡

ም፡ ፲፮፡ ፳፰፡፡ ዕብ፡ ፪፡ ፲፩፡ ፲፪፡፡

፲፰፡ ማርያም፡የመግደላዊቱም፡ መጣች፡ ለደቀ፡ መዛሙርትም፡ ነገረች፡ ጌታን፡ እንዳየች፡ ይህነንም፡ እንዳላት።

፲፱፡ ያም፡ ቀን፡ በመሸ፡ ጊዜ፡እርሱም፡ የሳምንት፡ መጀመርያ። ደጁም፡ ተቈልፎ፡ ሳለ፡ ደቀ፡ መዛሙርት፡ ወደ፡ተከማቹበት፡አይሁድን፡ስለ፡ፈሩ። መጣ፡ የሱስ፡መካከላቸውም፡ቆመ፡አላቸውም። *ሰላም፡ ለላንተ፡ ይሁን። ማር፡ ፲፮፡ ፲፬፡—፲፰፡፡

ሉቃ፡ ፳፬፡ ፴፮፡—፵፪፡፡ ኢሳ፡ ፶፪፡ ፯፡፡ ፶፯፡ ፲፱፡፡

፳፡ ይህነንም፡ ባለ፡ ጊዜ፡ እጁንና፡ ጐኑን፡ አሳያቸው። ደቀ፡ መዛሙርትም፡ ደስ፡አላቸው፡ጌታን፡ባዩ፡ ጊዜ። ም፡ ፲፱፡ ፴፬፡፡ ፩፡ ዮሐ፡ ፩፡ ፩፡፡

፳፩፡ የሱስም፡ ደግሞ፡አላቸው፡ ሰላም፡ ለላንተ፡

ይሁን። *አብ፡ እንደ፡ ላከኝ፡ እንዲሁም፡ እኔ፡ እልካ
ችኋለሁ። *ዮሐ፡ ፲፯፡ ፲፰።

፳፪፤ ይህነንም፡ ብሎ፡ እፍ፡ አለባቸው፡ አላቸው
ም። መንፈስ፡ ቅዱስን፡ ተቀበሉ።

፳፫፤ *ኃጢአቱን፡ የተዋችሁለት፡ ቀረችለት። የያ
ዛችሁበትም፡ ሰው፡ ተያዘችበት። ማቴ፡ ፲፮፡ ፲፱።
ም፡ ፲፰፡ ፲፰።

፳፬፤ *ቶማስ፡ ግን፡ ካሥራ፡ሁለቱ፡አንዱ፡ዲዲሞ
ስ፡ የሚሉት፡ ከርሳቸው፡ ጋራ፡ አልነበረም፡ የሱስ፡ በ
መጣ፡ ጊዜ። *ማቴ፡ ፲፡ ፫።

፳፭፤ ሌሎችም፡ደቀ፡መዛሙርት፡አሉት። ጌታን፡
አየነው። እርሱም፡አላቸው። የችንካሩን፡ምልክት፡
በጁ፡ ካላየሁ፡ ጸቴንም፡ ወደ፡ ችንካሩ፡ *ፍለጋ፡ካላገ
ባሁ፡ እጄንም፡ በጐኑ፡ ካላኖርሁ፡ አላምንም።
*ም፡ ፲፱፡ ፴፬።

፳፮፤ ከስምንት፡ ቀንም፡በኋላ፡ደቀ፡መዛሙርት፡
ደግሞ፡ በውሥጥ፡ ነበሩ፡ ቶማስም፡ ከርሳቸው፡ጋራ።
የሱስም፡ መጣ፡ ደጁ፡ም፡ ተቈልፎ፡ ነበር። በመካከ
ልም፡ ቆመ፡ አለም። ሰላም፡ ለላንተ፡ ይሁን።
ቍ፡ ፲፱።

፳፯፤ ቶማስንም፡ አለው። ጸትህግ፡ ወደዚህ፡ አ
ምጣ፡ እጄንም፡ እይ። እጅህነም፡ አምጣና፡ ወደ፡
ጐኔ፡ አግባት። ያላመንህም፡ አትሁን፡ ያመንህ፡ አ
ንጅ።

፳፰፤ ቶማስም፡ መለሰ፡ አለም። ጌታዬ፡አምላኬ
ም። *ም፡ ፩፡ ፩።

፳፱፤ የሱስም፡ አለው። ቶማስ፡ሆይ፡ሰላየኸኝን፡
አመንህ። ምስጋና፡ ይገባቸዋል፡ *ሳያዩ፡ለሚያምኑ፡
*፩፡ ጴጥ፡ ፩፡ ፰።

፴፤ የሱስም፡ ብዙ፡ ሌላ፡ተአምራት፡ አደረገ፡ በደ
ቀ፡ መዛሙርቱ፡ ፊት፡ በዚህ፡ መጽሐፍ፡ ያልተጻፈ።

፴፩፤ ይህም፡ ተጻፈ፡ታምኑ፡ ዘንድ፡ የሱስ፡እርሱ፡
ክርስቶስ፡ የእግዚአብሔር፡ ልጅ፡ እንደ፡ ሆነ። ባመና
ችሁም፡ ጊዜ፡ ሕይወት፡ ይሆንላችሁ፡ዘንድ፡በስሙ።
፩፡ ዮሐ፡ ፭፡ ፲፫።

## ምዕራፍ፡ ፳፩፤

፩፤ ከዚህም፡ በኋላ፡ የሱስ፡ ደግሞ፡ ለደቀ፡ መዛ
ሙርቱ፡ ራሱን፡ ገለጠ፡ በጥብርያደስ፡ ባሕር፡ አጠገ
ብ። እንዲህም፡ ታያቸው።

፪፤ ባንድ፡ ነበሩ፡ሲሞን፡ ጴጥሮስ፡ ቶማስም፡ ዲዲ
ሞስ፡ የሚባለው። ናትናኤልም፡ የቃና፡ ገሊላው። የ
ዘብዴዎስም፡ ልጆች። ሁለትም፡ ሌሎች፡ከደቀ፡ መ
ዛሙርቱ።

፫፤ ሲሞን፡ ጴጥሮስም፡ አላቸው። እኔ፡ እሔደላ
ሁ፡ ዓሣ፡ ላጸምድ። አሉትም። እኛም፡ ካንተ፡ጋራ፡
እንመጣለን። ወጡም፡ ወደ፡ መርከብም፡ገቡ። በዚ
ያችም፡ ሌሊት፡ ምንም፡ አላጸመዱም።

፬፤ በጸባም፡ ጊዜ፡ የሱስ፡ በደር፡ ቆመ፡ ደቀ፡ መዛ
ሙርትም፡ አላወቁም፡ የሱስ፡ እንደ፡ ሆነ።
ም፡ ፳፡ ፲፬። ሉቃ፡ ፳፬፡ ፲፮።

፭፤ የሱስም፡ አላቸው፡ እላንት፡ ልጆች፡ አንዳች፡
አላችሁን፡ የሚበላ። መለሱ፡ አሉትም፡ የለም።
ሉቃ፡ ፳፬፡ ፵፩።

፮፤ እርሱም፡ አላቸው። ወጽመዱን፡ጣሉት፡በመ
ርከቡ፡ ቀኝ፡ አጠገብ፡ ታገኙማላችሁ። ጣሉም፡ ሊስ
ቡትም፡ አልቻሉም፡ ካሣው፡ ብዛት፡ የተነሣ።
ሉቃ፡ ፭፡ ፬።

፯፤ ያም፡ ደቀ፡ መዝሙር፡ የሱስ፡ ይወደው፡ የነበ
ረው፡ ጴጥሮስን፡ አለው። ጌታ፡ ነው። ሲሞን፡ ጴጥሮ
ስም፡ በሰማ፡ ጊዜ፡ ጌታ፡ እንደ፡ ሆነ፡ ቀሚሱን፡ ታጠ
ቀ፡ ዕራቁቱን፡ ነበርና፡ ወደ፡ ባሕርም፡ ወደቀ።
ም፡ ፲፫፡ ፳፫።

፰፤ ሌሎች፡ ደቀ፡ መዛሙርት፡ ግን፡ በታናሺቱ፡ መ
ርከብ፡ መጡ። ከምድር፡ ርቀው፡ አልነበሩምና፡ ሁሌ
ት፡ መቶ፡ ክንድ፡ የሚያህል፡ እንጅ፡ እርሳቸውም፡
ያሣውን፡ ወጽመድ፡ ሲስቡ።

፱፤ ወደ፡ ምድርም፡ በወረዱ፡ ጊዜ፡ ፍም፡ ተቀም
ጦ፡ አዩ። ዓሣም፡ በላዩ፡ ነበረበት፡ እንጀራም።

፲፤ የሱስም፡ አላቸው። አሁን፡ ከጸመዳችሁት፡ ዓ
ሣ፡ አምጡ።

፲፩፤ ሲሞን፡ ጴጥሮስም፡ ወጣ፡ ወጽመዱንም፡ ወ
ደ፡ ምድር፡ ጐተተው። እርስዋም፡ታላላቅ፡ዓሣ፡ መ
ልታ፡ ነበረች፡ መቶ፡ አምሳ፡ ሶስት። ከዚህም፡ ሁሉ፡
ጋራ፡ ወጽመዱ፡አልተቀደደም።

፲፪፤ የሱስም፡ አላቸው። ኑ፡ ምሳችሁን፡ ብሉ። አ
ንድም፡ ከደቀ፡ መዛሙርቱ፡የደፈረ፡የለም፡ይለው፡
ዘንድ። አንተ፡ ማነህ። እርሱ፡ጌታ፡ እንደ፡ ሆነ፡ አው
ቀዋልና።

፲፫፤ የሱስም፡መጣ፡ እንጀራም፡ ወሰደ፡ ሰጣቸው
ም። ዓሣውንም፡ እንዲሁ። ም፡ ፮፡ ፲።

፲፬፤ ይህችም፡ ሶስተኛው፡ ናት፡ የሱስ፡ ለደቀ፡ መ
ዛሙርቱ፡ የተገለጠባት፡ ከሙታን፡ ከተነሣ፡ በኋላ።

፲፭፤ ምሳቸውንም፡ከበሉ፡ በኋላ፡ የሱስ፡ ሲሞን፡
ጴጥሮስን፡ አለው። ሲሞን፡ ሆይ፡ የዮና፡ልጅ፡ ትወደ
ኛለህን፡ከለዚህ፡ይልቅ። አለውም። አዎን፡ አቤቱ።
አንተ፡ ታውቃለህ፡ እንድወድህ። አለውም። ጥቦቶ
ቼን፡ ጠብቅ። ም፡ ፩፡ ፵፪።

፲፮፤ ደግሞ፡ ሁለተኛ፡ አለው። ሲሞን፡ ሆይ፡ የዮ
ና፡ ልጅ፡ ትወደኛለህን። አለውም፡ አዎን፡ አቤቱ።
አንተ፡ ታውቃለህ፡ እንድወድህ። አለው። *በጎቼን፡
ጠብቅ። *፩፡ ጴጥ፡ ፭፡ ፪፡ ፬።

፲፯፤ ሶስተኛም፡አለው። ሲሞን፡ሆይ፡የዮና፡ልጅ፡
ትወደኛለህን። ጴጥሮስም፡አዘነ፡ ሶስተኛ፡ ስላለው፡
ትወደኛለህን፡ አለውም። አቤቱ፡ አንተ፡ ሁሉን፡ ታ
ውቃለህ። አንተ፡ታውቃለህ፡እንድወድህ። አለው፡
የሱስ። በጎቼን፡ ጠብቅ። ም፡ ፲፫፡ ፴፯።

፲፰፤ እውነት፡እውነት፡ እልሃለሁ። አንተ፡ ጕልማ ሳ፡ ሳለህ፡አንተ፡ወገብህን፡ታጥቀህ፡ወደምትወደው ም፡ ሒደህ፡ ነበርህ። በሸመገልህም፡ ጊዜ፡ እጅህን፡ ታነሣለህ፡ሌላውም፡ያስታጥቅሃል፡ወደማትወደው ም፡ ይወስድሃል።

፲፱፤ ይህነንም፡አለ፡ሲያመለክት፡በምንም፡ሞት፡ እግዚአብሔርን፡ ያመሰግን፡ ዘንድ፡እንደሆነ ው። ይህ ንንም፡ ባለ፡ ጊዜ፡ አለው። ተከተለኝ።

፳፤ ጴጥሮስም፡ ተመለሶ፡ ደቀ፡ መዝሙሩንም፡ ኢየ፡ የሱስ፡ ይወደው፡ የነበረውን፡ ሲከተለው። እር ሱም፡በእራት፡ጊዜ፡ባጠገቡ፡ የተቀመጠው፡አለም። ጌታ፡ሆይ፡ማነው፡አሳልፎ፡የሚሰጥህ። ም፡ ፲፫፡ ፴፫፡፡

፳፩፤ ይህነን፡ ባየ፡ ጊዜ፡ ጴጥሮስ፡ የሱስን፡ አለው። ጌታ። ይህስ፡ እንዴት፡ ነው።

፳፪፤ የሱስም፡አለው።፡ብወድስ፡ይቀመጥ፡ዘንድ፡ እስከመጣ፡ድረስ፡ምን፡ አግደህ። አንተ፡ተከተለኝ።

፳፫፤ ስለዚህም፡ ይህ፡ ነገር፡ በወንድሞች፡ ዘንድ፡ ወጣ፡ ያ፡ ደቀ፡ መዝሙር፡ እንዳይሞት። የሱስም፡ አላለውም፡ እንዳይሞት፡ ብወድስ፡ ቢቀመጥ፡ እስ ክመጣ፡ ድረስ፡ ምን፡ አግደህ፡ እንጂ።

፳፬፤ ይህ፡ ደቀ፡ መዝሙር፡ነው፡ በዚህ፡ ስራ፡የመ ሰከረ፡የጻፈውም። ምስክሩም፡እውነት፡ እንደ፡ሆነ፡ እናውቃለን። ም፡ ፲፱፡ ፴፭፡፡ ራእ፡ ፩፡ ፪፡፡

፳፭፤ እጅግ፡ነገርም፡ ሌላ፡ ደግሞ፡ አደረገ፡ የሱስ። እርሱም፡ በያንዳንዱ፡ ቢጻፍ፡ በመሰለኝ፡ ዓለም፡ ስ ንኳ፡ባልቻለውም፡የተጻፈውን፡መጽሐፍ። አሜን። ም፡ ፳፡ ፴፡፡

ተፈጸመ ፡ የዮሐንስ ፡ ወንጌል።

# የ ሐ ዋ ር ያ ት ፡ ስ ራ ።

ምዕራፍ፤ ፩፤

፩፤ መጀመርያው፡ ነገር፡ ግን፡ ቴዎፍሎስ፡ ሆይ፡ ጻ ፍሁት፡ በስራው፡ ሁሉ፡ የሱስ፡ ያስተምርና፡ ያደርግ፡ ዘንድ፡ በጀመረው። ሉቃ፡ ፩፡ ፫፡፡

፪፤ ወደ፡ ሰማይ፡ እስከ፡ ወጣበት፡ቀን፡ድረስ፡የመ ረጻቸውን፡ ሐዋርያቱን፡ በመንፈስ፡ ቅዱስ፡ ካዘዛቸ ው፡ በኋላ።

፫፤ ደግሞም፡ ራሱን፡ ያሳያቸው፡ ሕማማት፡ ከተ ቀበለ፡ በኋላ፡ ሕያው፡ ሁኖ፡ በብዙ፡ በታመነ፡ ተአም ራት። ሲታያቸው፡ አርባ፡ ቀን፡ ነገርም፡ ቢነግራቸው፡ ስለ፡ *እግዚአብሔር፡ መንግሥት።

*ሉቃ፡ ፲፯፡ ፳፡ ፳፩፡፡ ሮሜ፡ ፲፬፡ ፲፯፡፡

፬፤ ከርሳቸውም፡ ጋራ፡ ተሰብስቦ፡ ሳለ፡ አዘዛቸው፡ ከየሩሳሌም፡ እንዳይወጡ። የአብን፡ ተስፋ፡ ደጅ፡ ደጽኑ፡ እንጂ፡ ከኔ፡ *የሰማችሁትን።

*ዮሐ፡ ፲፭፡ ፳፮፡፡ ሉቃ፡ ፳፬፡ ፵፱፡፡

፭፤ *ዮሐንስ፡ በውኃ፡ ያጠምቅ፡ ነበርና። እላንት፡ ግን፡ በመንፈስ፡ ቅዱስ፡ ትጠመቃላችሁ፡ከጥቂት፡ ቀ ን፡ በኋላ። *ም፡ ፲፩፡ ፲፮፡፡ ፲፫፡ ፳፬፡፡ ማቴ፡ ፫፡ ፲፩፡፡

፮፤ በተከማቹም፡ ጊዜ፡ ጠየቁት፡ አሉትም። አቤ ቱ፡ በዚህ፡ ወራት፡ *መንግሥት፡ ለእሥራኤል፡ ትመ ልሳለህ። *ሉቃ፡ ፳፬፡ ፳፩፡፡

፯፤ አላቸውም። ለላንት፡ አልተሰጣችሁም፡ ዘመ ኑን፡ ጊዜውንም፡ ታውቁ፡ ዘንድ፡ አብ፡ በሥልጣኑ፡ ያ ደረጋትን።

፰፤ ነገር፡ ግን፡ ኃይል፡ ትቀበላላችሁ፡ መንፈስ፡ቅዱ ስ፡ በወረደባችሁ፡ ጊዜ። ለኔም፡ ትመሰክራላችሁ፡ በ የሩሳሌም፡ በይሁዳም፡ ሁሉ፡ በሰማርያም፡ እስከ፡ ምድር፡ ዳርም፡ድረስ።

፱፤ ይህነንም፡ ባለ፡ ጊዜ፡ ከርሳቸው፡ ከፍ፡ ከፍ፡ አ ለ፡ እርሳቸውም፡ኢያዩት። ደመናም፡ ተቀበለችው፡ ካይናቸውም፡ ተሠወረ። ማር፡ ፲፮፡ ፲፱፡፡

ሉቃ፡ ፳፬፡ ፶፩፡፡

፲፤ እርሳቸውም፡ወደ፡ ሰማይ፡ በጽኑ፡ሲመለከቱ፡ እርሱ፡ ሲወጣ። እነሆ፡ *ሁለት፡ ሰዎች፡ ባጠገባቸው፡ ቁመው፡ነበሩ፡ነጭ፡ልብስ፡ለብሰው። *ሉቃ፡ ፳፬፡ ፬፡፡

፲፩፤ ሲልዋቸውም። እላንት፡የገሊላ፡ ሰዎች፡ለም ን፡ ቁማችኋል፡ ወደ፡ ሰማይ፡ ኢያያችሁ። ይህ፡ የሱ ስ፡ ከላንት፡ ወደ፡ ሰማይ፡ የወጣው፡ እንደሁ፡ *ይመ ጣል፡ እንዳያችሁት፡ ወደ፡ ሰማይ፡ ሲወጣ።

*ሉቃ፡ ፳፩፡ ፳፯፡፡

፲፪፤ የዚያን፡ ጊዜም፡ ወደ፡ የሩሳሌም፡ ተመለሱ፡ ደብረ፡ዘይት፡ከሚባለው፡ *ተራራ። እርሱ፡ ለየሩሳሌ ም፡ የቀረበ፡ የሰንበት፡ መንገድ፡ የሚያህል።

*ሉቃ፡ ፳፬፡ ፶፡፡

፲፫፤ በገቡም፡ ጊዜ፡ ወደ፡ ቤተ፡ ንጉሥ፡ ወጡ፡ *ጴጥ ሮስ፡ ያዕቆብም፡ ወደ፡ ነበሩባት፡ ዮሐንስም፡ እንድር ያስም፡ ፊልጶስ፡ ቶማስም። በርተሎሜዎስ፡ ማቴዎ ስም። ያዕቆብ፡ የእልፍዮስ፡ ልጅ፡ ሲሞንም፡ ቀናዒ ው። ይሁዳም፡ የያዕቆብ፡ ወንድም። *ማቴ፡ ፲፡ ፪፡፡

ሉቃ፡ ፮፡ ፲፫፡—፲፮፡፡

፲፬፤ እለዚህ፡ ሁሉ፡ *ባንድ፡ለጸሎት፡ተጸምደው፡
ነበሩ። ከሴቶች፡ ጋራ፡ ማርያምም፡ ከየሱስ፡ እናት፡
†ከወንድሞቹም፡ ጋራ። *ም፡ ፪፤ ፩፤፤
†ዮሐ፡ ፯፤ ፫፤፤
፲፭፤ በዚያም፡ ወራት፡ ጴጥሮስ፡ በደቀ፡ መዛሙር
ት፡ መካከል፡ ተነሣ፡ (ከዚያም፡ ሰዎች፡ ተከማችተ
ው፡ ነበሩ፡ መቶ፡ ሀያ፡ ስም፡ ይሆን፡) አለም።
፲፮፤ እላንት፡ወንድማማች፡ሰዎች፡ ይህ፡ *መጽሐ
ፍ፡ ይፈጸም፡ ዘንድ፡ ይገባ፡ ነበር፡ መንፈስ፡ ቅዱስ፡ በ
ደዊት፡ አፍ፡ አስቀድሞ፡ የተናገረው፡ ስለ፡ ይሁዳ፡
መሪ፡ የሆናቸው፡የሱስን፡ ለያዙት። *መዝ፡ ፵፩፤ ፲፤፤
፲፯፤ ከኛ፡ጋራ፡ ተቈጥሮ፡ ነበረና፡ ለዚህም፡ማገልገ
ል፡ ታድሎ፡ ነበረ።
፲፰፤ ይህ፡እርሱ፡ ገዛ፡በዓመፃ፡ ዋጋ። በግምባሩም፡
ወደቀ፡ ከመካከሉም፡ተቀደደ፡ አንጀቱም፡ ሁሉ፡ ፈ
ሰሰ። ማቴ፡ ፳፯፤ ፫፤—፲፤፤
፲፱፤ ወሬውም፡ ታወቀ፡ በየሩሳሌም፡በተቀመጡ
ት፡ ሁሉ፡ ዘንድ። ያ፡እርሻ፡በቋንቋቸው፡አኬልደማ፡
እስኪጸራ፡ ድረስ። እርሱ፡ የደም፡ እርሻ፡ የሚሆን።
፳፤ *በመዝሙር፡መጽሐፍ፡ተጽፎዋልና። አገሩ፡
ምድረ፡ በዳ፡ ትሁን፡ የሚኖርባትም፡ አይኑር። ሹመ
ቱንም፡ሌላ፡ይውሰደት። *መዝ፡ ፷፱፤ ፳፮፤፤ ፻፱፤ ፰፤፤
፳፩፤ እንጊዲህም፡ ይገባል፡ አንድ፡እንመርጥ፡ ዘን
ድ፡ ከለዚህ፡ ሰዎች፡ ከኛ፡ጋራ፡ አብረው፡ ከነበሩት፡ የ
ሱስ፡ ጌታችን፡ ወደኛ፡ በገባው፡ ዘመን፡ ሁሉ፡ በወጣ
ውም። ዮሐ፡ ፲፭፤ ፳፯፤፤
፳፪፤ ከዮሐንስ፡ ጥምቀት፡ ጀምሮ፡ ከኛ፡ እስከወ
ጣበት፡ ቀን፡ ድረስ፡ከለዚህ፡ አንዱ፡ምስክር፡ ይሆን፡
ዘንድ፡ ከኛ፡ ጋራ፡ በትንሣኤው።
፳፫፤ ሁለትም፡ አቀሙ፡ በፊታቸው። ዮሴፍን፡ በ
ርስባ፡ የሚባለውን፡ ዮስጦስም፡ የተጸራ። ማትያስ
ንም።
፳፬፤ በጸለዩም፡ ጊዜ. አሉ። አንተ፡ጌታ፡ ሆይ፡የሁ
ሉን፡ *ልብ፡ የምታውቅ። ከለዚህ፡ከሁለቱ፡አንዱን፡
ግለጥ፡ የመረጥኸውን። *መዝ፡ ፯፤ ፲፤፤
፳፭፤ የዚቺን፡ማገልገል፡ የመልእክቲቱም፡ስፍራ፡
ይወስድ፡ ዘንድ፡ ይሁዳ፡ የተዋትን፡ ወደ፡ ስፍራው፡
ይሔድ፡ ዘንድ።
፳፮፤ ዕፃም፡ ተጣጣሉ፡ዕፃውም፡ በማትያስ፡ላይ፡
ወደቀ። ካሥራ፡አንዱ፡ሐዋርያት፡ጋራም፡ተቈጠረ።
ምሳ፡ ፲፮፤ ፴፫፤፤

## ምዕራፍ፡ ፪፤

፩፤ አምሳውም፡ *ቀን፡ በተፈጸመ፡ ጊዜ፡ በጰንጤ
ቆስቴ፡ ቀን፡ †ሁሉ፡ ባንድ፡ ነበሩ፡ በስፍራቸው።
*ዘሌዋ፡ ፳፫፤ ፲፭፤—፳፪፤፤ †ም፡ ፩፤ ፲፬፤፤
፪፤ ድንገትም፡ከሰማይ፡ ድምጽ፡ሆነ፡ እንደ፡ዓው
ሎ፡ ነፋስ። ተቀምጠውበት፡ የነበሩትንም፡ ቤት፡ ሁ
ሉ፡ መላው።
፫፤ የተከፋፈለችም፡ የሳት፡ ልሳን፡ ታዮቻቸው፡ ከ
ርሳቸውም፡ በያንዳንዱ፡ ተቀመጠችባቸው።
ማቴ፡ ፫፤ ፲፩፤፤
፬፤ በሁሉም፡ መንፈስ፡ ቅዱስ፡ መላባቸው፡ በሌላ
ም፡ ቋንቋ፡ ይናገሩ፡ ዘንድ፡ ጀመሩ፡ መንፈስ፡ ቅዱስ፡
እንደ፡ ሰጣቸው፡ ይናገሩ፡ ዘንድ። ም፡ ፲፤ ፵፬፤፤
፭፤ በየሩሳሌምም፡ የተቀመጡ፡ ሰዎች፡ ነበሩ፡ አ
ይሁድ፡ *በጎ፡ ሰዎች፡ ከሰማይ፡ በታች፡ ካሉ፡ ከአሕዛ
ብ፡ ሁሉ። *ም፡ ፲፫፤ ፳፮፤፤
፮፤ ይህም፡ ወሬ፡ በሆነ፡ ጊዜ፡ ሁሉ፡ ባንድ፡ ተሰበሰ
ቡ፡ ተደነቁም። ከርሳቸው፡ኢያንዳንዱ፡ይሰማቸው፡
ነበርና፡ በቋንቋው፡ ሲናገሩ።
፯፤ ሁሉም፡ ደነገጡ፡ አደነቁም፡ እንደህ፡ ሲሉ፡ እ
ርሱ፡ በርሳቸው። እሌህ፡ ሁሉ፡ የሚናገሩት፡ የገሊላ፡
ሰዎች፡ አይደሉምን።
፰፤ እንደት፡ እኛ፡ኢያንዳንዳችን፡ እንሰማቸዋለ
ን፡ በተወለድነበት፡ በአነጋገሩ፡ ሲናገሩ፡
፱፤ እኛ፡ ጰርቴ፡ሜድያንም፡ ኤላሚጡኒም። በወ
ንዞች፡ መካከልም፡ የታቀመጥነ። በይሁዳም፡ በቀጰ
ደቅያም። በጰንጦስም፡በእስያም።
፲፤ በፈሪጊያም። በጰምፌልያም። ከምሥርም።
በደወለ፡ ሊብያም፡ ወደ፡ ቄሬኔን፡ የቀረበች። የሮሚ
ም፡ ሰዎች፡ ከዚህ፡ የሚኖሩ። አይሁድም፡ ስደተኖ
ችም።
፲፩፤ ከቀረጢስም፡ በዓረብ፡ ምድርም፡ ያሉ፡ ሰዎ
ች። እንሰማቸዋለን፡ የእግዚአብሔርን፡ ታላቅነት፡
ሲናገሩ፡ በቋንቋችን።
፲፪፤ ሁሉም፡ ተደነቁ፡ቸገራቸውም፡እንደህ፡ሲሉ፡
እርሱ፡ በርሳቸው። እንጀ፡ ይህ፡ ምን፡ ይሆን።
፲፫፤ ሌሎችም፡ ኢያፈዙ፡ ይሉ፡ ነበሩ፡ እሌህ፡ጉሽ፡
ጸጅ፡ ጸግበዋል።
፲፬፤ ጴጥሮስም፡ ቀመ፡ ካሥራ፡ አንዱ፡ ጋራ፡ ድም
ጹንም፡ ከፍ፡አደረገ፡እንደህም፡ሲል፡ ተናገራቸው።
እላንተ፡ ሰዎች፡ አይሁድ፡ በየሩሳሌምም፡ የምትኖ
ሩ፡ ሁላችሁ። ይህ፡ በላንተ፡ ዘንድ፡ የታወቀ፡ ይሁን፡
ነገሬንም፡ አድምጹ።
፲፭፤ እሌህ፡ የሰከሩ፡ አይደሉምና፡እላንተ፡ እንደ
መሰላችሁ። ከቀኑ፡ ሶስተኛ፡ ሰዓት፡ ናትና።
፲፮፤ ነገር፡ ግን፡ ይህ፡ በነቢዩ፡ በዮኤል፡ የተባለው፡
ነው። ኢዮ፡ ፫፤ ፩፤፤
፲፯፤ በኋለኛዪቱም፡ቀን፡ይሆናል።እግዚአብሔር፡
ይላል። ከመንፈሴ፡ አፈሳለሁ፡ ሥጋ፡ በለበሰ፡ ሁሉ፡
ላይ። ወንደችም፡*ሴቶችም፡ልጆቻችሁ፡ትንቢት፡ ይ
ናገራሉ። ጕበዛዝታችሁም፡ ራእይ፡ ያያሉ፡ ሽማግሌ
ቻችሁም፡ ሕልም፡ ያልማሉ። *ም፡ ፳፩፤ ፱፤፤
፲፰፤ በወንደችም፡ በሴቶችም፡ ባሮቼ፡ላይ፡ደግሞ፡
በዚያች፡ ወራት፡ ከመንፈሴ፡ አፈሳለሁ፡ትንቢትም፡
ይናገራሉ።
፲፱፤ ተአምራትም፡ እሰጣለሁ፡ ከሰማይ፡ በላይ።

ምልክትም፡ ከምድር፡ በታች። ደምም፡ እሳትም፡ የጢስም፡ ጭጋግ።

፳፤ ጸሓይ፡ ወደ፡ ጨለማ፡ ትለወጣለች፡ ጨረቃውም፡ ወደ፡ ደም። የእግዚአብሔር፡ቀን፡ታላቁ፡ለሁሉም፡ የሚገለጠው፡ ሳይመጣ።

፳፩፤ ይሆናልም፡ የእግዚአብሔርን፡ ስም፡ የጸራ፡ ሁሉ፡ ይድናል። ሮሜ፡ ፲፡ ፲፫።

፳፪፤ እላንት፡ የእሥራኤል፡ሰዎች፡ ይህን፡ ነገር፡ ስሙ። የሱስ፡ የናዝሬቱ፡ *ከእግዚአብሔር፡ የሆነ፡ ሰው። በላንት፡ ዘንድ፡ የተገለጠ፡ በተአምራት፡ በኃይልም፡ በምልክትም፡እግዚአብሔር፡በርሱ፡ያደረጋት፡ በመካከላችሁ።እላንት፡እንድታውቁ።*ም፡፲፡፴፰።

፳፫፤ ይህነን፡በተወሰነው፡በእግዚአብሔር፡ *ምክር፡ በተቀደመውም፡ እውቀቱ፡የተሰጣችሁን፡ እላንት፡ ወሰዳችሁ፡ በኃጢአተኞችም፡እጅ፡ ሰቀላችሁት፡ ገደላችሁትም። *ም፡ ፬፡ ፳፰።

፳፬፤ *ይህነንም፡ እግዚአብሔር፡ አስነሣው፡ የሞትን፡ ማሠርያ፡ ፈትቶ። እርሱ፡ ይይዘው፡ ዘንድ፡ አይቻልምና። *ም፡ ፫፡ ፲፭።

፳፭፤ ዳዊት፡ ስለርሱ፡ ይላልና። እግዚአብሔርን፡ ሁሉግዜ፡ በፊቴ፡ አየሁ፡በቀኜ፡ነውና፡እንዳልታወክ። *መዝ፡ ፲፮፡ ፰።

፳፮፤ ስለዚህ፡ ልቤን፡ ደስ፡ አለው፡ ልሳኔም፡ ሐሤት፡ አደረገ። ሥጋዬም፡ ደግሞ፡ በተስፋ፡ ያድራል።

፳፯፤ ነፍሴን፡ በሲኦል፡ አትተዋትምና። ወዳጅህንም፡ ጥፋት፡ ያይ፡ ዘንድ፡ አትተወውምና።

፳፰፤ የሕይወትን፡መንገድ፡ አሳየኸኝ። ደስታ፡ አጠገብኸኝ፡ ከፊትህ፡ ጋራ።

፳፱፤ እላንት፡ ሰዎች፡ ወንድማማች፡ ፈቀዱልኝ፡ ስለ፡ዳዊት፡ ያባቶች፡ አለቃ፡ለላንት፡ በግልጥ፡እናገር፡ ዘንድ፡ እንደ፡ ሞተ፡እንደ፡ተቀበረም። መቃብሩም፡ ከኛ፡ ዘንድ፡ ነው፡ እስከ፡ ዛሬ። ም፡ ፲፫፡ ፴፮። ፩፡ ነገሥ፡ ፪፡ ፲።

፴፤ ነቢይ፡ ግን፡ነበርና፡ባወቀም፡ጊዜ፡እግዚአብሔር፡ መሐላ፡እንደ፡ ማለለት፡ ክርስቶስን፡ እንዲያስነሣ፡ ከወገቡ፡ ፍሬ፡ እንደ፡ ሥጋ፡ በዙፋኑ፡ ይቀመጥ፡ ዘንድ። መዝ፡ ፻፴፪፡ ፲፩። ፪፡ ሳሙ፡ ፯፡ ፲፪፡ ፲፫።

፴፩፤ እርሱ፡ ያነን፡ አስቀድሞ፡ ባየ፡ ጊዜ፡ ስለ፡ ክርስቶስ፡ ትንሣኤ፡ ተናገረ፡ ነፍሱ፡ በሲኦል፡ እንዳልቀረች፡ ሥጋውም፡ ጥፋት፡ እንዳላየው።

፴፪፤ ይህነን፡ የሱስን፡ እግዚአብሔር፡ አስነሣው። እኛም፡ ሁላችን፡ ለርሱ፡ እንመሰክራለን።

፴፫፤ አሁን፡ግን፡በእግዚአብሔር፡ቀኝ፡ ከፍ፡ከፍ፡ ባለ፡ ጊዜ፡ የመንፈስ፡ ቅዱስንም፡ ተስፋ፡ ከአብ፡በወሰደ፡ ጊዜ፡ እርሱ፡ ይህነን፡ አፈሰሰው፡ እላንት፡ ዛሬ፡ የምታዩትን፡ የምትሰሙትንም።

፴፬፤ ዳዊት፡ ወደ፡ ሰማይ፡ አልወጣምና፡ *እርሱ፡ አለ፡እንጂ። ጌታ፡ጌታዬን፡ በቀኜ፡ተቀመጥ፡አለው። *መዝ፡ ፻፲፡ ፩።

፴፭፤ ጸላቶችህን፡ለእግርህ፡ድኳ፡እስካደርግልህ፡ ድረስ።

፴፮፤ እንግዴህ፡ በውነት፡ይወቅ፡የእሥራኤል፡ ወገን፡ ሁሉ። እግዚአብሔር፡ ይህነን፡ የሱስን፡እላንት፡ የሰቀላችሁትን፡ ጌታ፡ መሢሕም፡ እንዳደረገው። ም፡ ፭፡ ፴፩።

፴፯፤ ይህነንም፡ በሰሙ፡ ጊዜ፡ ልባቸው፡ ታወከ። ጴጥሮስንም፡ አሉት፡ የቀሩትንም፡ ሐዋርያት። *ምን፡ እንስራ፡ እላንት፡ ሰዎች፡ ወንድሞች። *ም፡ ፲፮፡ ፴።

፴፰፤ ጴጥሮስም፡ አላቸው። ንስሐ፡ ግቡ፡ ከላንትም፡ ሁሉ፡ ኢያንዳንዳችሁ፡ በየሱስ፡ ክርስቶስ፡ ስም፡ ይጠመቅ፡ኃጢአት፡ ለማስተስረይ። የመንፈስ፡ቅዱስንም፡ ጸጋ፡ ትወስዳላችሁ። ም፡ ፫፡ ፲፱። ሉቃ፡ ፳፬።

፴፱፤ ተስፋው፡ ለላንት፡ ነውና፡ ለልጆቻችሁም፡ *በሩቅም፡ ላሉ፡ ሁሉ፡ እግዚአብሔር፡ አምላካችን፡ ለጸራቸውም፡ ሁሉ። *ኢዮ፡ ፫፡ ፭።

፵፤ በሌላም፡ ነገር፡ እጅግ፡ መሰከረባቸው፡ እንዲህም፡ ሲል፡ለመናቸው። ዳኑ፡ ከዚህ፡ዓመፀኛ፡ ትውልድ።

፵፩፤ ከርሳቸውም፡ ነገሩን፡ደስ፡በልዋቸው፡ የተቀበሉ፡ ተጠመቁ። በዚያም፡ ቀን፡ ከምእመናን፡ ተጨመረ፡ ሦስት፡ ሺህ፡ ነፍስ፡ የሚያህል።

፵፪፤ የሐዋርያትንም፡ትምህርት፡ አጽንተው፡ ይዘው፡ ነበሩ፡ አንድነትም፡ እንጀራም፡ *መቍረስ፡ ጸሎትም። ም፡ ፳፡ ፯።

፵፫፤ በሰውም፡ሁሉ፡ፍርሃት፡ሆነ። ተአምራትም፡ እጅግም፡ ድንቅ፡ በሐዋርያት፡ ዘንድ፡ ተደረገ።

፵፬፤ ያመኑትም፡ሁሉ፡ባንድ፡ ነበሩ። ያላቸውም፡ ሁሉ፡ ባንድነት፡ ነበረ። ም፡ ፬፡ ፴፪።

፵፭፤ ግዛታቸውንም፡ ጥሪታቸውንም፡ይሸጡ፡ነበሩ፡ ለሁሉም፡ ይከፍሉት፡ ነበሩ፡ በያንዳንዱ፡ የሚሹትን፡ ያህል።

፵፮፤ ዕለት፡ዕለትም፡ባንድ፡በመቅደስ፡ ጸንተው፡ ይኖሩ፡ነበሩ።እንጀራም፡በየቤቱ፡ይቈርሱ፡ነበሩ። ምግባቸውንም፡ይበሉ፡ነበሩ፡በደስታ፡ በጽሩም፡ ልቡና። ቍ፡ ፵፪።

፵፯፤ እግዚአብሔርን፡ ኢያመሰገኑ። ጸጋም፡ ነበራቸው፡በሕዝቡ፡ፊት፡ሁሉ።እግዚአብሔርም፡ ዕለት፡ *ዕለት፡ የሚድኑትን፡ ለቤተ፡ ክርስቲያን፡ ይጨምር፡ ነበረ። *ም፡ ፬፡ ፬። ፭፡ ፲፬። ፲፩፡ ፳፩። ፲፬፡ ፩።

## ምዕራፍ፡ ፫፤

፩፤ ጴጥሮስና፡ ዮሐንስም፡ወደ፡መቅደስ፡ባንድ፡ወጡ፡ በጸሎት፡ ጊዜ፡ በዘጠኝ፡ ሰዓት።

፪፤ አንድ፡ ሰውም፡ነበረ፡ ከናቱ፡ ማሕፀን፡ ጀምሮ፡ *ያነከሰ። ተሸክመውም፡ ሁሌግዜ፡ በመቅደስ፡ ደጅ፡ መልካም፡ደጅ፡የሚሉት፡ ያስቀምጡት፡ ነበር፡ ምጽዋት፡ሊለምን፡ወደ፡መቅደስ፡ከሚገቡ።*ም፡፲፬፡፰።

፫፡ ይህ፡ ጴጥሮስን፡ዮሐንስ፡ወደ፡ መቅደስ፡ሲገቡ፡ ባየ፡ ጊዜ፡ ለመናቸው፡ ምጽዋት፡ ከርሳቸው፡ ሊወስድ።

፬፡ ጴጥሮስም፡ ከዮሐንስ፡ ጋራ፡አጽንቶ፡ ተመለከተው፡ አለውም። ወደኛ፡ ተመልከት።

፭፡ እርሱም፡ወደርሳቸው፡ አየ፡ተስፋ፡ አድርጎ፡ከርሳቸውም፡ ምጽዋት፡ የሚወስድ፡ መሰለው።

፮፡ ጴጥሮስም፡ አለው። ወርቅና፡ብር፡ ወደኔ፡ አይገኝም። ወደኔ፡ያለውን፡ ግን፡ እርሱን፡ እሰጥሃለሁ። በየሱስ፡ ክርስቶስ፡ በናዝሬቱ፡ ስም፡ *ተነሣና፡ ሒድ።
*ም፡ ፲፬፡ ፱፡ ፲፡፡

፯፡ በቀኝ፡እጁም፡ *ያዘው፡ አስነሣውም። በዚያን፡ ጊዜም፡ ተረከዙ፡ ቍርጭምጭሚቱም፡ ጸና።
*ማቴ፡ ፰፡ ፲፭፡፡

፰፡ ቁሞም፡ *ተነሣ፡ ሔደም፡ ከርሳቸውም፡ ጋራ፡ ወደ፡ መቅደስ፡ ገባ፡ ኢየሮጠ፡እግዚአብሔርንም፡ ኢያመሰገነ።
*ኢሳ፡ ፴፭፡ ፮፡፡

፱፡ ሕዝብም፡ ሁሉ፡ አዩት፡ ሲሔድ፡ እግዚአብሔርን፡ ኢያመሰገነ።

፲፡ አወቁትም፡እርሱ፡እንደ፡ሆነ፡ያ፡ተቀምጦ፡ ምጽዋት፡ ይለምን፡ የነበረው፡ መልካም፡ በሚባለው፡ በመቅደስ፡ደጅ። ፍርሃትም፡መደነቅም፡መላባቸው፡ በርሱ፡ከሆነው፡የተነሣ።

፲፩፡ የተፈወሰውም፡ እንካሳ፡ በጴጥሮስና፡ በዮሐንስ፡ ተደዞ፡ ሳለ፡ ሕዝቡ፡ ሁሉ፡ ወደርሳቸው፡ መጡ፡ ወደ፡ ወለሉ፡ የሰሎሞን፡ *ወለል፡ የሚባል፡ ተደንቀው።
*ም፡ ፭፡ ፲፪፡፡

፲፪፡ ጴጥሮስም፡ ባያቸው፡ ጊዜ፡ ሕዝቡን፡ አላቸው። እላንተ፡ሰወች፡የእሥራኤል፡ወገን፡ለምን፡ በዚህ፡ትደነቃላችሁ። ወይስ፡ለምን፡ ታዩናላችሁ፡ በኃይላችን፡ወይም፡በቅድስነታችን፡ እንደደረገነ፡ ይህ፡ ይሔድ፡ዘንድ።

፲፫፡ የአብርሃም፡ *አምላክ፡የይስሐቅም፡ የያዕቆብም፡ያባቶቻችን፡ አምላክ፡ልጁን፡ አከበረው፡የሱስን። እላንተ፡ †አሳልፋችሁ፡የሰጣችሁትን፡ካዳችሁትም፡ በጲላጦስ፡ፊት፡ እርሱ፡ ሊተወው፡ በፈረደ፡ጊዜ።
*ም፡ ፭፡ ፴፡፡ ዘፀአ፡ ፫፡ ፮፡ ፲፭፡ ፲፮፡፡ †የሐዋ፡ ፪፡ ፳፫፡፡

፲፬፡ እላንተ፡ ግን፡ ቅዱሱን፡ ጻድቁንም፡ ካዳችሁ፡ *ለመናችሁም፡ ነፍሰ፡ገዳይ፡ ሰው፡ ይተውላችሁ፡ ዘንድ።
*ማቴ፡ ፳፯፡ ፳፡ ፳፩፡፡

፲፭፡ የሕይወትን፡ ራስ፡ ግን፡ ገደላችሁ፡ እግዚአብሔር፡ከሙታን፡*ያስነሣውን። እኛ፡ምስክሮች፡ የሆንለትን።
*ም፡ ፪፡ ፳፬፡ ፴፪፡፡ ፬፡ ፲፡፡
ሮሜ፡ ፬፡ ፳፬፡፡ ፰፡ ፲፩፡፡ ፩፡ ቆሮ፡ ፲፭፡ ፬፡ ፲፭፡፡

፲፮፡ በስሙም፡ሃይማኖት፡ይህነ፡ የምታዩትን፡ የምታውቁትንም፡ ስሙ፡ አጸናው። በርሱ፡ የሆነችም፡ ሃይማኖት፡ይህነ፡ ፈጹም፡ ጤና፡ ሰጠችው፡ በሁላችሁ፡ፊት።

፲፯፡ አሁንም፡ወንድሞቼ፡ሆይ፡ አውቃለሁ፡ያደረጋችሁትን፡ባለ፡ ማወቅ፡ እንደደረጋችሁ፡እንደ፡ለቆቻችሁ።
ሉቃ፡ ፳፫፡ ፴፬፡፡

፲፰፡ እግዚአብሔር፡ ግን፡ *በነቢያት፡ ሁሉ፡ አፍ፡ ሰለ፡ክርስቶስ፡ ሕማማት፡ የተናገረውን፡እንደሁ፡ ፈጸመው።
*ሉቃ፡ ፳፬፡ ፳፯፡፡

፲፱፡ አሁንም፡ ንስሐ፡ ግቡ፡ ተመለሱም፡ ኃጢአታችሁ፡እንድጠፋላችሁ፡*የዕረፍትም፡ዘመን፡ ትመጣላችሁ፡ዘንድ፡ከእግዚአብሔር፡ፊት።
ም፡ ፪፡ ፴፰፡፡
*ኢሳ፡ ፴፭፡ ፲፡፡

፳፡ የሱስ፡ክርስቶስንም፡ ይሰድላችሁ፡ ዘንድ፡ከጥንት፡ ያዘጋጀላችሁን።
ደን፡ ፯፡ ፳፪፡ ፳፯፡፡
ሮሜ፡ ፰፡ ፳፩፡፡ ራእ፡ ፰፡ ፯፡

፳፩፡ ሰማይ፡የተቀበለችው፡ ነገሩ፡ ሁሉ፡ እስከሚታደስበት፡ ጊዜ። እግዚአብሔር፡ የተናገረው፡ በቅዱሳን፡ በነቢያቱ፡ ሁሉ፡ አፍ፡ ከጥንት፡ የነበሩ።

፳፪፡ ሙሴም፡ላባቶች፡አለ። እግዚአብሔር፡ አምላካችሁ፡ ከወንድሞቻችሁ፡ *ነቢይ፡ ያስነሣላችኋል፡ እንደኔ፡ ያለውን። እርሱ፡ የሚነግራችሁን፡ ሁሉ፡ ስሙት።
*ዘዳግ፡ ፲፰፡ ፲፭፡—፲፰፡፡

፳፫፡ ያነን፡ነቢይ፡ግን፡የማትሰማ፡ነፍስ፡ ሁሉ፡ከሕዝብ፡ተለይታ፡ የምጠፋ፡ትሆናለች።

፳፬፡ ነቢያትም፡ ሁሉ፡ ከሳሙኤል፡ ጀምሮ፡ ከርሱም፡ በኋላ፡ የነበሩ፡ ሁሉ፡ ስለዚች፡ ቀን፡ ተናገሩ፡ አወሩም።

፳፭፡ እላንት፡ የነቢያት፡ልጆች፡ የኪዳንም፡ልጆች፡ እግዚአብሔር፡ ላባቶቻችን፡ የማለበት፡ እንደሁ፡ ሲል፡ለአብርሃም። *በዘርህ፡ ይባረካሉ፡ የምድር፡ አሕዛብ፡ ሁሉ።
ዘፍ፡ ፲፪፡ ፫፡፡ ፳፪፡ ፲፰፡፡

፳፮፡ ለላንት፡ አስቀድሞ፡ እግዚአብሔር፡ ልጁን፡ የሱስን፡ባስነሣ፡ጊዜ፡ሊባርካችሁ፡ሰደደው፡ ከላንት፡ ኢያንዳንዱን፡ ከክፋቱ፡ ሊመልስ።
ም፡ ፲፫፡ ፵፮፡፡

## ምዕራፍ፡ ፬፡

፩፡ እርሳቸውም፡ ለሕዝቡ፡ ሲነግሩ፡ ካህናቱ፡ ተነሡባቸው፡ የመቅደስም፡ *አለቃ፡ ሰዱቃውያንም።
ሉቃ፡ ፳፪፡ ፶፪፡፡

፪፡ ቢነደቸው፡ ሕዝብን፡ ስላስተማሩ፡ ከሙታን፡ በመነሣቱም፡ በየሱስ፡ ስላወሩ።

፫፡ እጃቸውንም፡ ጣሉባቸው፡ በግዞትም፡ አኖርዋቸው፡ እስከ፡ነጋ። ጊዜው፡ መሸት፡ነበረና።

፬፡ እጅግ፡ሰዎች፡ግን፡ ነገራቸውን፡ ከሰሙት፡ አመኑ። ያመኑትም፡ የሰዎች፡ ቍጥር፡ አምስት፡ ሽህ፡ ያህል።
ም፡ ፪፡ ፵፩፡፡

፭፡ በነጋውም፡ ተከማቹ፡ አለቆቻቸው፡ ሽማግሌቾም፡ ጸፎችም፡ በየሩሳሌም።

፮፡ *ሐናም፡ የካህናቱ፡ አለቃ፡ ቀያፋም፡ ዮሐንስም፡ እስክንድሮስም፡ ከካህናት፡ አለቅነትም፡ ወገን፡ የነበሩ፡ ሁሉ።
ም፡ ፭፡ ፲፯፡፡ ሉቃ፡ ፫፡ ፪፡፡

፯፡ በመካከልም፡ አቆምዋቸው፡መረመርዋቸው

ም፡ እንደህ፡ ሲሉ። በምን፡ ኃይል፡ በማንስ፡ ስም፡ እ
ላንት፡ ይህነን፡ አደረጋችሁ። ማቴ፡ ፳፩፡ ፳፫።

፰፡ የዚያን፡ጊዜ፡ጴጥሮስ፡መንፈስ፡ ቅዱስን፡መላ፡
አላቸውም። እላንት፡ የሕዝብ፡ አለቆች፡ የእሥራኤ
ልም፡ ሽማግሎች። ሉቃ፡ ፲፪፡ ፲፩።

፱፡ እኛ፡ *ዛሬ፡ ብንከሰስን፡ በድውይ፡ ሰው፡ በደረሰ
ው፡በጐነት፡ በምን፡ይህ፡ ደነ። *ዮሐ፡ ፲፡ ፴፪።

፲፡ በላንት፡በሁላችሁ፡የታወቀ፡ይሁን፡ በእሥራኤ
ልም፡ ሕዝብ፡ ሁሉ፡ ዘንድ። እላንት፡ በሰቀላችሁት፡
በናዝሬቱ፡ *በየሱስ፡ክርስቶስ፡ ስም፡ እግዚአብሔር፡
ከሙታን፡ ያስነሣው። በርሱ፡ይህ፡በፊታችሁ፡ ደህና፡
ሁኖ፡ ቆመ። *ምዕ፡ ፫፡ ፲፭።

፲፩፡ ይህ፡ነው፡ *ደንጊያው፡ እላንት፡ አናጾች፡የናቃ
ችሁት፡ ይህም፡ የማዝን፡ ራስ፡ሆነ።
*ማቴ፡ ፳፩፡ ፵፪። መዝ፡ ፻፲፰፡ ፳፪።

፲፪፡ በማንም፡ይህንነት፡ የለም፡በሌላው። ሌላ፡ ስ
ም፡የለምና፡ በሰማይ፡ ታች፡ ለሰው፡ የተሰጠ፡ በርሱ፡
ይድን፡ዘንድ፡ የሚገባ። ማቴ፡ ፩፡ ፳፩።

፲፫፡ የጴጥሮስንና፡ የዮሐንስን፡ ድፍረት፡ ባዩ፡ጊዜ፡
አወቁም፡ መጽሐፍ፡ የማያውቁ፡ ሰዎች፡ እንደሆኑ፡
ሕዝባውያንም። አደነቁ፡ አወቅዋቸውም፡ ከየሱስ፡
ጋራ፡ እንደ፡ ነበሩ።

፲፬፡ *የተፈወሰውንም፡ ሰው፡ ከርሳቸው፡ ጋራ፡ ቁ
ሞ፡ባዩ፡ጊዜ፡ምክንያትም፡ባጡ፡ጊዜ፡ይህነን፡ የሚያ
ፈርሱበት። *ምዕ፡ ፫፡ ፰፡ ፱።

፲፭፡ አዘዙ፡ ከጉባዔ፡ ወደ፡ ሜዳ፡ ይወጡ፡ ዘንድ፡
እርሱ፡ በርሳቸውም፡ ተማከሩ።

፲፮፡ እንደህ፡ሲሉ። ምን፡እንስራ፡በለዚህ፡ሰዎች።
የታወቀች፡ ተአምራት፡ በርሳቸው፡ ተደርጋለችና። ይ
ህም፡የሩሳሌም፡ በሚኖሩ፡ሁሉ፡ ተገልጥዋል። እንክ
ደትም፡ ዘንድ፡ አይቻለነም። ዮሐ፡ ፲፩፡ ፵፯።

፲፯፡ ነገር፡ግን፡ ወሬዋ፡ በሕዝብ፡ እጅግ፡ እንደይወ
ጣ፡ፈጽመን፡*እንንገራቸው፡ለማንም፡ሰው፡በዚህ፡
ስም፡እንደይናገሩ። *ምዕ፡ ፭፡ ፳፰።

፲፰፡ ደግሞም፡ ጸርዋቸው፡ አዘዝዋቸውም፡ ፈጽ
መው፡ እንደይነግሩ፡ እንደያስተምሩም፡ በየሱስ፡
ስም።

፲፱፡ ጴጥሮስና፡ ዮሐንስ፡ ግን፡ መለሱ፡ አልዋቸው
ም። በእግዚአብሔር፡ ፊት፡ ይገባ፡ እንደ፡ ሆነ፡*እላን
ትን፡ እንሰማ፡ ዘንድ፡ እግዚአብሔርን፡ ከመስማት፡
ይልቅ፡እላንት፡ ፍረዱ። *ምዕ፡ ፭፡ ፳፱።

፳፡ እኛ፡ ግን፡ አይቻለነም፡ ባየነው፡ በሰማነውም፡
ሁሉ፡ ዝም፡ እንል፡ ዘንድ።

፳፩፡ እርሳቸው፡ ግን፡ ገሠጽዋቸውና፡ ተውዋቸ
ው፡ ምክንያት፡ ባያገኙባቸው፡ እንደ፡ ምን፡ይሣቅይ
ዋቸው፡ ዘንድ፡ ስለ፡ሕዝቡ። ሁሉ፡ እግዚአብሔርን፡
አመስግነዋልና፡ በተደረገው፡ ስራ።

፳፪፡ የዚህች፡ፈውስ፡ተአመራት፡የተደረገችለት፡
ሰው፡ካርባ፡ አመት፡ይበልጠው፡ ነበረና።

፳፫፡ በተለቀቁም፡ ጊዜ፡ ወደ፡ ባልንጀሮቻቸው፡
መጡ፡የካህናትም፡አለቆች፡ሽማግሎችም፡ያልዋቸ
ውን፡ ነገርዋቸው።

፳፬፡ እርሳቸውም፡ይህነን፡በሰሙ፡ጊዜ፡ወደ፡ እግ
ዚአብሔር፡ ቃላቸውን፡ ከፍ፡ ከፍ፡ አደረጉ፡ ተጉብረ
ው፡አሉም። ጌታ፡ ሆይ፡አንተ፡ አምላክ፡ ነህ፡ ሰማዩን
ና፡ምድሩን፡ባሕሩንም፡ የፈጠርህ፡ በርስዋ፡ የሚኖረ
ውንም፡ ሁሉ።

፳፭፡ በባርያህ፡ *በዳዊት፡አፍ፡ያልህ። ለምን፡ ተሰ
በሰቡ፡ አሕዛብ፡ ሕዝብም፡ በከንቱ፡ ተናገሩ።
*መዝ፡ ፪፡ ፩፡ ፪።

፳፮፡ የምድር፡ ነገሥታት፡ ተነሡ፡ አለቆችም፡ ባን
ድ፡ ተከማቹ፡ በእግዚአብሔር፡ ላይ፡ በመሢሑም።

፳፯፡ በውነት፡በቅዱስ፡ልጅህ፡ በየሱስ፡ላይ፡ የቀባ
ኸው፡*ሄሮድስ፡ ጲላጦስም፡የጴንጤኑ፡ ተሰብስበዋ
ልና፡ ከአሕዛብ፡ ከእሥራኤልም፡ ወገን፡ ጋራ።
*ሉቃ፡ ፳፫፡ ፲፪።

፳፰፡ ያደርጉ፡ ዘንድ፡ እጅህ፡ ምክርህም፡ አስቀድ
ማ፡ ያዘጋጀችውን፡ ይሆን፡ ዘንድ። ምዕ፡ ፪፡ ፳፫።

፳፱፡ አሁንም፡ አቤቱ፡ ወደ፡ ቍጣቸው፡ ተመልከ
ት፡ለባሮችህም፡ስጥ፡በድፍረት፡ሁሉ፡ይናገሩ፡ዘንድ።
ኤፌ፡ ፮፡ ፲፱።

፴፡ እጅህን፡ ዘርግተህ፡ ለመፈወስ። ተአምራት
ም፡ድንቅም፡ይሁን፡በየሱስ፡ በቅዱስ፡ ልጅህ፡ ስም።

፴፩፡ በለመኑም፡ጌዜ፡ ተከማቹበት፡ የነበሩበት፡
ስፍራ፡ተናወጠ። ሁሉም፡ መንፈስ፡ቅዱስን፡መሉ፡ የ
እግዚአብሔርንም፡ ነገር፡ በድፍረት፡ ተናገሩ።

፴፪፡ ላመኑትም፡ሁሉ፡አንድ፡ልብ፡ አንዲት፡ነፍስ
ም፡ነበራቸው። አንድም፡ከከብቱ፡ይህ፡ገንዘቤ፡ነው፡
የሚል፡ አልነበረም። ሁሉ፡ ለርሳቸው፡ ለባልንጀሮቻ
ቸውም፡ ባንድነት፡ ነበረ፡ እንጂ። ምዕ፡ ፪፡ ፵፬።

፴፫፡ ሐዋርያትም፡ በየሱስ፡ በጌታ፡ ትንሣኤ፡ ምስ
ክርነት፡ ይገልጡ፡ ነበሩ፡ በታላቅ፡ኃይል። ታላቅም፡*ጸ
ጋ፡ በሁሉ፡ ላይ፡ ነበረባቸው። *ምዕ፡ ፪፡ ፵፯።

፴፬፡ የሚያሻቸውም፡ ነገር፡ አልነበረም። የሚገ
ዙ፡ሁሉ፡ምድርም፡ሆነ፡እርሻም፡ ቤትም፡ ሸጠው፡ የ
ሸያጩን፡ ዋጋ፡ ያመጡ፡ ነበሩና። ምዕ፡ ፪፡ ፵፭።

፴፭፡ በሐዋርያትም፡እግር፡ታች፡ይጥሉት፡ነበርና።
ይሰጡም፡ ነበር፡ *ለያንዳንዱ፡ የሚሻውን፡ ያህል።
ዘዳግ፡ ፲፭፡ ፲፩። ኢሳ፡ ፶፰፡ ፯።

፴፮፡ ዮሴፍም፡ሐዋርያት፡ በርናባስ፡ያሉት (ትርጓ
ሜውም፡ የደስታ፡ ልጅ)፡ ከሌዊ፡ ወገን፡ አገሩም፡ ቆ
ጵሮስ።

፴፯፡ ለርሱ፡አገር፡ነበረው። ሸጠውም፡ ከብቱንም፡
አምጥቶ፡ ከሐዋርያት፡ እግር፡ ዘንድ፡ አኖረው።

ምዕራፍ፡ ፭፡

፩፡ አንድ፡ሰውም፡ስሙን፡ሐናንያ፡ የሚሉት፡ከሰ
ጲራ፡ ከምሽቱ፡ ጋራ፡ አገር፡ሸጠ።

፪፤ ከዋጋውም፡ከፊሉ፡ሸሽጎ፡በምሽቱ፡አውቀት። የቀረውንም፡ አመጣ ፡*በሐዋርያትም፡ እግር፡ ታች፡ አኖረው። *ምዕ፡ ፬፡ ፴፯፡፡

፫፤ ጴጥሮስም፡ አለው። ሐናንያ፡ ሆይ፡ ለምን፡ መላ፡ ሰይጣን፡በልብህ፡በመንፈስ፡ ቅዱስ፡ ላይ፡ ትዋሽ፡ ዘንድ፡ካገሩም፡ሸያጭ፡ትሰርቅ፡ዘንድ። ዮሐ፡ ፲፫፡ ፪፡፡

፬፤ ከጥንቱ፡ሳይሸጥ፡ላንተ፡አልነበረምን።ከተሸጠም፡በኋላ፡በትእዛዝህ፡ሆነ። ይህነን፡ነገር፡ ለምን፡ በልብህ፡አሰብህ። በሰው፡አስተኛ፡አልሆንህም፡ በእግዚአብሔር፡ እንጂ።

፭፤ ሐናንያም፡ ይህነን፡ ነገር ፡ በሰማ፡ ጊዜ ፡ ወደቀ፡ ሞተም ። ታላቅም፡ ፍርሃት፡ ሆነ፡ ይህነን፡ በሰሙ፡ ሁሉ፡ላይ።

፮፤ ጐበዛዝትም፡ *ተነሥተው፡ ከፈኑት፡ አውጥተውም፡ ቀበሩት። *ዘሌዋ፡ ፲፡ ፬፡ ፭፡፡

፯፤ ሶስት፡ ሰዓትም፡ ያህል፡ በሆነ፡ጊዜ፡ ገባች፡ ምሽቱ፡ የሆነውን፡ ሳታውቅ።

፰፤ ጴጥሮስም፡ መለሰላት፡ አላትም። ንገሪኝ፡ ይህን፡በሚያህልን፡ምድራችሁን፡ሸጣችሁ። እርስዋም፡ አለች፡ አዎን፡ በዚህን፡ ያህል።

፱፤ ጴጥሮስም፡አላት።ለምን፡በዚህ፡ ስራ፡ተባበራችሁ፡የእግዚአብሔርን፡መንፈስ፡ ትፈታተኑ፡ ዘንድ። እነሆ፡ባልሽን፡የቀበሩ፡ ሰዎች፡ በደጅ፡ ናቸው፡አንቺንም፡ያወጡሻል።

፲፤ የዚያን፡ ጊዜውም፡ ከግሩ፡ በታች፡ ወደቀች፡ ሞተችም።ጐበዛዝትም፡ በገቡ፡ ጊዜ፡ ሙታ፡ አገኙዋት፡ ተሸክምዋትም ፡ ከባልዋም ፡ አጠገብ ፡ ቀበርዋት።

፲፩፤ ታላቅም፡ፍርሃት፡በቤተ፡ ክርስቲያን፡ ሁሉ፡ ላይ፡ ሆነ፡ ይህነንም፡ በሰሙ፡ ሁሉ፡ ላይ።

፲፪፤ በሐዋርያትም ፡ እጅ፡ ተአምራት፡ እጅግም፡ ድንቅ፡ሆነ፡በሕዝቡ፡መካከል። ሁሉም፡ ባንድ፡ ነበሩ፡ *በሰሎሞን፡አደራሽ። *ምዕ፡ ፫፡ ፲፩፤

፲፫፤ ከሌሎችም፡አንድ፡ደቀርባቸው፡ ዘንድ፡ የሚደፍር፡ አልነበረም፡ ሕዝቡ፡ ግን፡ ያከብራቸው፡ ነበር።

፲፬፤ በጌታም፡ የሚያምኑ፡ ይበዙ፡ ነበሩ፡ ወንዶች፡ ሴቶችም። ምዕ፡ ፪፡ ፵፯፡፡ ፬፡ ፬፡፡ ፮፡ ፯፡፡

፲፭፤ ድውያንን፡ ባደባባይ፡ እስኪያመጡ፡ ድረስ፡ ባልጋም፡በቃሬዛም፡ያደርጓቸው፡ነበሩ። ጴጥሮስ፡ባለፈ፡ጊዜ፡ ከርሳቸው፡ ባንዱ፡ ጽላው፡ ይወድቅበት፡ ዘንድ። ምዕ፡ ፲፱፡ ፲፩፡ ፲፪፤

፲፮፤ እጅግም፡ ሰዎች፡ በየሩሳሌም፡ ዙርያ፡ ካላችው፡ አገር፡ ይመጡ፡ ነበር። ድውያንንም፡ ርኩስ፡ ጋኔንም፡ ያለባቸውን፡ ያመጡ፡ ነበር፡ ሁሉም፡ ይፈወሱ፡ ነበሩ።

፲፯፤ የካህናት፡አለቃም፡ *ተነሣ፡ ከርሱ፡ ጋራ፡ም፡ የነበሩ፡ ከሰዱቃውያን፡ ወገን። ቅናትም፡ መላባቸው። *ምዕ፡ ፬፡ ፩፡ ፮፡፡

፲፰፤ በሐዋርያትም፡ላይ፡እጃቸውን፡ ጫኑባቸው፡ በሕዝቡም ፡ ግዞት ፡ አኖርዋቸው።

፲፱፤ የእግዚአብሔር፡ *መልአክ፡ግን፡በሌት፡ የግዞቱን፡ደጅ፡ከፈተ፡ከርሱም፡አወጣቸው፡አላቸውም። *ምዕ፡ ፲፪፡ ፯፡፡

፳፤ ሒዱ፡ በመቅደስም፡ ቁሙ፡ የዚህችንም፡ *ሕይወት፡ ነገር፡ ሁሉ፡ ለሕዝብ፡ንገሩ። *ዮሐ፡ ፲፪፡ ፶፡፡

፳፩፤ በሰሙም፡ጊዜ፡እጅግ፡ ማልደው፡ ወደ፡ መቅደስ፡ገቡ፡አስተማሩም።የካህናትም፡አለቃ፡ በመጣ፡ ጊዜ፡ከርሱም፡ጋራ፡የነበሩ፡ ጉባዔውን፡ ጸሩ፡ ሽማግሌችንም፡ሁሉ፡ ከእሥራኤል፡ልጆች። ወደ፡ ግዞትም፡ ሰደዱ፡ ያመጥዋቸው፡ ዘንድ። ምዕ፡ ፬፡ ፭፡፡

፳፪፤ መልክተኞች፡ ግን፡ መጥተው፡ በግዞት፡ ቤት፡ አላገኙዋቸውም፡ ወደርሳቸውም፡ ተመለሱ ፡ ነገርዋቸውም፡ እንደዚህ፡ ሲሉ።

፳፫፤ የግዞቱን፡ ቤት ፡ ተቈልፎ፡ አገኘነ፡ በቍልፍ፡ ሁሉ፡ጠባቂችም፡በደጅ፡ፊት፡በሰከ፡ሚያ፡ቁመው። በከፈትነ፡ጊዜ፡ግን፡ማንንም፡በውሥጡ፡አላገኘነም።

፳፬፤ ይህነንም፡ነገር፡በሰሙ፡ ጊዜ፡ካህኑ፡ የመቅደሱም፡አለቃ፡የካህናቱም፡ አለቆች፡ በነገራቸው፡ ተደነቁ፡ እንደዚህ፡ ሲሉ። እንጃ፡ ይህ፡ ምን፡ ይሆን።

፳፭፤ አንድ፡ሰውም፡መጣ፡እንደዚህ፡ ሲልም፡ ነገራቸው። እነሆ ፡ እለዚያ ፡ ሰዎች ፡ በግዞት ፡ ያኖራችኋቸው፡እርሳቸው፡ በመቅደስ፡ ቁመዋል፡ ሕዝብንም፡ያስተምራሉ።

፳፮፤ የዚያን፡ጊዜም፡ሔደ፡ አለቃው፡ ከሎላልቱ፡ ጋራ፡አመጥዋቸውም።በግድም፡ አይደለም፡ ሕዝቡን፡ ስለ፡ ፈሩ፡ እንዳይወግሮዋቸው።

፳፯፤ ባመጥዋቸውም፡ ጊዜ ፡ በጉባዔ፡ አቀምዋቸው፡ የካህናት፡ አለቃም፡ ጠየቃቸው።

፳፰፤ እንደዚህ፡ ሲል ። *ቍርጥ፡ ነገር ፡ አልነገርናችሁምን፡ እንዳታስተምሩ፡ በዚህ፡ ስም። እነሆም፡ የሩሳሌምን፡ ከትምህርታችሁ ፡ ፈጽማችሁ ፡ መላችኋት፡ የዚያንንም፡ሰው፡ ተደም፡ ታመጡብነ፡ ዘንድ፡ ትሻላችሁ። *ምዕ፡ ፬፡ ፲፰፡፡ ተማቴ፡ ፳፯፡ ፳፭፡፡

፳፱፤ ጴጥሮስም፡መለሰ፡ሐዋርያትም፡ አሉም። እግዚአብሔርን፡እንሰማ፡ ዘንድ፡ ይገባል፡ ከሰው፡ ይልቅ። ምዕ፡ ፬፡ ፲፱፡፡ ዳን፡ ፮፡ ፲፡፡

፴፤ ያባታችን፡አምላክ፡ የሱስን፡ አስነሣ፡ እላንተ፡ የገደላችሁትን ፡ በንጨት ፡ ላይ ፡ ሰቅላችሁ። ምዕ፡ ፫፡ ፲፭፡፡

፴፩፤ ይህነን፡እግዚአብሔር፡ በቀኙ ፡ *አስቀመጠው፡ራስ፡መድኃኒትም፡አድርጎ፡ለእሥራኤል፡ንስሐ፡ ይሰጥ፡ ዘንድ፡የኃጢአትም፡ ስርየት። *ምዕ፡ ፪፡ ፴፫፡፡

፴፪፤ እኛም፡ ለርሱ፡ *ምስክሮች፡ ነነ፡ በዚህ፡ ነገር። መንፈስ፡ ቅዱስም፡ ደግሞ፡ ምስክር፡ ነው፡ እግዚአብሔር፡ ለሚታዘዙት፡ የሰጠው። *ሉቃ፡ ፳፬፡ ፵፰፡፡ ዮሐ፡ ፲፭፡ ፳፮፡ ፳፯፡፡

፴፫፤ ይህነንም፡ በሰሙ፡ ጊዜ፡ ጥርሳቸውን፡ አፋጩ፡ ሊገልዋቸውም፡ ወደዱ። ምዕ፡ ፯፡ ፶፬፡፡

፴፬፤ አንድ፡ ሰውም፡ በሸንጎ፡ ተነሣ፡ ፈሪሳዊ፡ ስ

ሙ፡ *ገማልዬል፡ የኦሪት፡ መምህር፡ በሕዝቡ፡ ሁሉ፡
ዘንድ፡ የከበረ። ሐዋርያትንም፡ ወደ፡ሚደ፡ ጥቂት፡
ይወጡ፡ ዘንድ፡ አዘዘ። *ም፡ ፳፪፡ ፫፡፡

፴፭፡ አላቸውም፡ እላንተ፡ ሰዎች፡ የእሥራኤል፡
ወገን፡ በራሳችሁ፡ ተጠበቁ፡ በለዚህ፡ ሰዎች፡ በምታ
ደርጉት፡ ነገር።

፴፮፡ ከዚህም፡ ወራት፡ አስቀድሞ፡ ቱዳስ፡ ተነሥ
ተዋልና፡ እንደዚህ፡ ሲል፡ ስለ፡ ራሱ፡ እኔ፡ ታላቅ፡ ነኝ።
አራት፡ መቶ፡ የሚሆኑ፡ሰዎችም፡ተከተሉት። እርሱ
ም፡ ሞተ፡ የተከተሉትም፡ ሁሉ፡ ተፈቱ፡ እንደ፡ ምና
ምንም፡ ሆኑ።

፴፯፡ ከዚህም፡ በኋላ፡ ተነሣ፡ ይሁዳ፡የገሊላው፡ ግ
ብር፡በተጻፈበት፡ዘመን። እጅግ፡ሰዎችም፡በኋላው፡
ሳበ፡ እርሱም፡ ጠፋ፡ የታዘዙትም፡ ሁሉ፡ ተበተኑ።

፴፰፡ አሁንም፡ እላችኋለሁ፡ ከለዚህ፡ ሰዎች፡ ራ
ቁ፡ ተውዋቸውም። ይህ፡ *ምክር፡ ይህም፡ስራ፡ ከሰ
ው፡ እንደ፡ ሆነ፡ ይፈታልና። *ማቴ፡ ፲፭፡ ፲፫፡፡

፴፱፡ ከእግዚአብሔር፡ ግን፡ እንደ፡ ሆነ፡ አይቻላች
ሁም፡ ታፈርሱት፡ ዘንድ፡ ደግሞ፡ ከእግዚአብሔር፡
ጋራ፡ *ስትጣሉ፡ እንዳትገኙ። *ም፡ ፱፡ ፭፡፡

፵፡ ነገሩንም፡ ሰሙት፡ ሐዋርያትንም፡ ጸሩ፡ *ገረ
ፏዋቸውም፡ ነገሯቸውም፡ በየሱስ፡ ስም፡ እንዳይ
ናገሩ፡ ለቀቅዋቸውም። *ም፡ ፳፪፡ ፲፱፡፡

፵፩፡ እርሳቸው፡ግን፡ከሸንጎው፡ፊት፡*ደስ፡ብልዋ
ቸው፡ ሔደ፡ ስለ፡ ስሙ፡ይናቁ፡ዘንድ፡ ተገብተዋቸዋ
ልና። *ማቴ፡ ፭፡ ፲፡ ፲፪፡፡ ፩፡ ጴጥ፡ ፬፡ ፲፫፡፡

፵፪፡ ሁለግዜም፡ አይለዩም፡ ነበረ፡ በመቅደስ፡ በ
ቤትም፡ ሁሉ፡ ሲያስተምሩ፡ የምስራችም፡ ሲነግሩ፡
የሱስ፡እንደ፡ሆነ፡ክርስቶስ።

ምዕራፍ፡ ፮፡

፩፡ በዚያችም፡ ወራት፡ ደቀ፡ መዛሙርት፡ በበዙ፡
ጊዜ፡ ማንጕርጕር፡ ሆነ፡ በፅርዕ፡ ሰዎችና፡ በዕብራው
ያን፡ መካከል። ባልቴቶቻቸውን፡ትተው፡ነበሩና፡ የለ
ት፡ የለቱን፡ ማገልገል፡ ሲሰሩ። ም፡ ፬፡ ፴፭፡፡

፪፡ አሥራ፡ ሁለቱም፡ የደቀ፡ መዛሙርትን፡ወገን፡
ጸሩ፡አሉም።ይህ፡ነገር፡ደስ፡የሚያሰኝ፡አይደለም፡
የእግዚአብሔርን፡ ነገር፡ ትተን፡ ማዕድ፡ እናገለግል፡
ዘንድ።

፫፡ ከላንትም፡ሰባት፡ ሰዎች፡ምረጡ፡ወንድሞቼ፡
ሆይ፡ *በመልካም፡የተመሰከረላቸው። መንፈስ፡ ቅ
ዱስ፡ ጥበብም፡ የመላባቸው፡ ለዚህም፡ ስራ፡ እናቁ
ማቸው። *፩፡ ጢሞ፡ ፫፡ ፯፡ ፰፡፡

፬፡ እኛ፡ ግን፡ ለጸሎት፡ ነገሩንም፡ ለማስተማር፡
እንጸመድ።

፭፡ ነገሩም፡ ተወደደ፡በጉባዔው፡ ሁሉ፡ ፊት። እስ
ጢፋኖስንም፡ መረጡ፡ ሃይማኖት፡ መንፈስ፡ ቅዱስ
ም፡የመላበትን፡ሰው።ፊልጶስንም። ጵሮኮሮስንም፡
ኒቃኖርንም። ጢሞንንም፡ ጰርሜናስንም። ኒቆላ
ዎስንም፡ አረማዊነትን፡ ትቶ፡ ወደ፡ ይሁዳዊነት፡ የገ
ባውን፡ ሰው፡ አገሩም፡ አንጾኪያ።

፮፡ በሐዋርያትም፡ ፊት፡ አቆምዋቸው። *ከጸለ
ዩም፡ ጊዜ፡ እጃቸውን፡ ጫኑባቸው። *ም፡ ፩፡ ፳፬፡፡

፯፡ የእግዚአብሔርም፡ ነገር፡ ከፍ፡ ከፍ፡ አለ፡ የደ
ቀ፡መዛሙርትም፡ቍጥር፡እጅግ፡ በዛ፡በየሩሳሌም።
እጅግም፡ ሰዎች፡ ከካህናት፡ ወገን፡ ለሃይማኖት፡ ተ
ገዙ። ም፡ ፲፱፡ ፳፡፡

፰፡ እስጢፋኖስ፡ ግን፡ ሃይማኖት፡ ኃይልም፡ መል
ቶበት፡ ነበረና፡ ተአምራት፡ ታላቅም፡ ድንቅ፡ በሕዝ
ብ፡ ያደርግ፡ ነበረ።

፱፡ ሰዎችም፡ ተነሡ፡ከጉባዔ፡ለቤርጢኖን፡ የሚባ
ል፡ከቂሬናውያንም፡ከእስክንድርያንም፡ከቂልቂያ
ም፡ ወገን፡ ከእስያም፡ እስጢፋኖስንም፡ ይከራከሩ
ት፡ ነበር።

፲፡ ጥበቡንም፡ይናገርበትም፡የነበረውን፡መንፈስ፡
ይቋቋሙ፡ ዘንድ፡ አልቻለም። ሉቃ፡ ፳፩፡ ፲፭፡፡

፲፩፡ የዚያን፡ ጊዜም፡ ሰዎች፡ አመጡ፡ እንዲህ፡ የ
ሚሉ። እኛ፡ ሰማነ፡ የስድብ፡ ነገር፡ ሲናገር፡ በሙሴ፡
ላይ፡ በእግዚአብሔርም፡ ላይ። ማቴ፡ ፳፮፡ ፷፡፡

፲፪፡ ሕዝቡንም፡ አወኩ፡ ሽማግሎችንም፡ ጻፎች
ንም፡ ወደቁበትም፡ ነጠቁት፡ ወደ፡ ጉባዔም፡ አመ
ጡት።

፲፫፡ *ሃሰት፡ ምስክሮችም፡ አስነሡበት፡ እንዲህ፡
ሲሉ። ይህ፡ሰው፡የስድብ፡ነገር፡መናገር፡አይተውም፡
በዚህ፡ በተቀደሰ፡ ስፍራ፡ ላይ፡ በኦሪትም፡ ላይ።
*ኤር፡ ፳፮፡ ፲፩፡፡

፲፬፡ ሲል፡ ሰምተነዋልና። የሱስ፡ የናዝሬቱ፡ ይህነ
ን፡ ስፍራ፡ ያፈርሳል፡ ሙሴም፡የሰጠነን፡ሕግ፡ ይለው
ጣል።

፲፭፡ በጉባዔ፡ የተቀመጡትም፡ ሁሉ፡ ዓይናቸው
ን፡ ተክለው፡ ተመለከቱት፡ ፊቱንም፡ አዩት፡ እንደ፡
መልአክ፡ ፊት።

ምዕራፍ፡ ፯፡

፩፡ የካህናቱ፡አለቃም፡ አለው። በውኑ፡ይህ፡ነገር፡
እንዲህ፡ነው።

፪፡ እርሱም፡አለ። እላንተ፡ሰዎች፡ወንድማማች፡
አባቶችም፡ ስሙ። የምስጋና፡ አምላክ፡ ላባታችን፡ ለ
አብርሃም፡ ታየው፡ በሚሶጶታሚያ፡ ምድር፡ ሳለ፡ በ
ካራን፡ ሳይቀመጥ። ዘፍ፡ ፲፩፡ ፴፩፡፡ ፲፪፡ ፩፡፡

፫፡ አለውም። ካገርህ፡ ውጣ፡ ከዘመዶችህም፡ ና፡
እኔ፡ ወደማሳይህ፡ ምድር። ዘፍ፡ ፲፪፡ ፩—፲፪፡፡

፬፡ የዚያን፡ ጊዜ፡ ከከልደውያን፡ አገር፡ ወጣ፡ በካ
ራንም፡ ተቀመጠ። ከዚያም፡ አባቱ፡ ከሞተ፡ በኋላ፡
ወደዚች፡ አገር፡አወጣው፡ እላንተ፡ ዛሬ፡ተቀምጣች
ሁባት፡ ያላችሁ።

፭፡ ርስትም፡ አልሰጠውም፡ የግር፡ ጫማ፡ ስንኳ፡
ያህል። ተሰፋ፡ ሰጠው፡ እንጂ፡ይሰጣት፡ ዘንድ፡ ገንዘ

ብ፡ ለርሱ፡ልትሆነው፡ከርሱም፡ በኋላ፡ለልጆቹ። ልጅ
ም፡ አልነበረውም። ዘፍ፡ ፲፪፡ ፯።

፮፤ እንደዚህም፡ ተናገረ፡ እግዚአብሔር፡ ዘሩ፡ ስደ
ተኛ፡ ይሆናል፡ በሌላ፡ አገር፡ ባርያም፡ ያደርጉታል፡ መ
ከራም፡ ያስቀብሉታል፡ አራት፡ መቶ፡ አመት።
ዘፍ፡ ፲፭፡ ፲፫። ዘፀአ፡ ፲፪፡ ፵።

፯፤ ባሮችም፡ የሚሆኑላቸውን፡ ሕዝብ፡እኔ፡ እፈ
ርድባቸዋለሁ፡እግዚአብሔር፡አለ።ከዚህም፡በኋላ፡
ይወጣሉ፡ በዚህም፡ ስፍራ፡ ይገዙልኛል።

፰፤ የግዝረት፡*ኪዳንም፡ ሰጠው፡ እንደሁም፡ አ
ብርሃም፡ †ይስሐቅን፡ ወለደ፡ በስምንተኛውም፡ ቀ
ን፡ ገዘረው። **ይስሐቅም፡ያዕቆብን፡ወለደ። ††ያዕ
ቆብም፡ ወለደ፡አሥራ፡ሁለቱን፡ያባቶችን፡አለቆች።
*ዘፍ፡ ፲፯፡ ፲። †ዘፍ፡ ፳፩፡ ፪።
**ዘፍ፡ ፳፭፡ ፳፮። ††ዘፍ፡ ፳፱፡ ፴፩። ፴፡ ፳፭።

፱፤ ያባቶችም፡ አለቆች፡ በዮሴፍ፡ ቀኑበት፡ ወደ፡
ምሥርም፡ ሸጡት። እግዚአብሔርም፡ ከርሱ፡ ጋራ፡
ነበረ። ዘፍ፡ ፴፯፡ ፳፰።

፲፤ ከመከራው፡ ሁሉም፡ አዳነው፡ ጸጋም፡ ጥበብ
ም፡ ሰጠው፡ በፈርዖን፡ በምሥር፡ ንጉሥ፡ ፊት። መጋ
ቢውንም፡ አደረገው፡ በምሥር፡ላይ፡በቤቱም፡ሁሉ፡
ላይ። ዘፍ፡ ፵፩፡ ፵፡—፵፭።

፲፩፤ ራብም፡ መጣ፡ በምሥር፡ አገር፡ ሁሉ፡ በከነዓ
ንም። ታላቅም፡ ጭንቀት። አባቶቻችንም፡ ስንደ፡ አ
ላገኙም።

፲፪፤ ያዕቆብም፡ በሰማ፡ ጊዜ፡ በምሥር፡ ስንደ፡ እ
ንደለ፡አባቶቻችንን፡ በፊት፡ሰደደ። ዘፍ፡ ፵፪፡ ፩።

፲፫፤ በሁለተኛውም፡ ዮሴፍ፡ ታወቀ፡ በወንድሞ
ቹ፡ ዘንድ፡ ለፈርዖንም፡ የዮሴፍ፡ ዘመድ፡ የተገለጠ፡
ሆነ። ዘፍ፡ ፵፭፡ ፬።

፲፬፤ ዮሴፍም፡ ላከ፡ አባቱንም፡ ጸራ፡ ዘመዶቹን
ም፡ ሁሉ፡ ሰባ፡ አምስት፡ ነፍስ። ዘፍ፡ ፵፭፡ ፱፡ ፲።

፲፭፤ ያዕቆብም፡ ወደ፡ ምሥር፡ ወረደ። እርሱም፡
ሞተ፡ አባቶቻችንም። ዘፍ፡ ፵፮፡ ፩። ፵፱፡ ፴፫።

፲፮፤ ወደ፡ ሴኬምም፡ ፈለሱ፡ ተቀበሩም፡ አብር
ሃም፡ ብብር፡ ዋጋ፡በገዛው፡ መቃብር፡ ከሀሞር፡ልጆች፡
ከሴኬም፡ አባት። ዘፍ፡ ፳፫፡ ፲፯፡ ፲፰።
ኢያ፡ ፳፬፡ ፴፪።

፲፯፤ የተስፋውም፡ ጊዜ፡ በቀረበ፡ ዘመን፡ እግዚአ
ብሔር፡ስለርሱ፡ለአብርሃም፡የማለበት፡ ሕዝብ፡ መ
ላ፡ በምሥርም፡ እጅግ፡ በዛ። ዘፀአ፡ ፩፡ ፯።

፲፰፤ ሌላ፡ ንጉሥ፡ ዮሴፍን፡ የማያውቀው፡ እስኪ
ነሣ፡ ድረስ።

፲፱፤ ይህ፡ በዘመዶቻችን፡ ተነኰለ፡ አባቶቻችነን
ም፡ ጐዳቸው። ወንዶች፡ ልጆቻቸውንም፡ በወንዝ፡
ጣላቸው፡ እንደይድኑ። ዘፀአ፡ ፩፡ ፳፪።

፳፤ በዚያን፡ ጊዜም፡ ሙሴ፡ተወለደ፡ በእግዚአብ
ሔር፡ ዘንድም፡ የተወደደ፡ ሆነ። ሦስት፡ ወርም፡ ተቀ
መጠ፡ ባባቱ፡ ቤት። ዘፀአ፡ ፪፡ ፪። ዕብ፡ ፲፩፡ ፳፫።

፳፩፤ በተጣለም፡ ጊዜ፡የፈርዖን፡ልጅ፡ አነሣችው፡
ለርስዋም፡ ልጅ፡አድርጋ፡አሳደገችው። ዘፀአ፡ ፪፡ ፲።

፳፪፤ ሙሴም፡ የምሥሮችን፡ጥበብ፡ ሁሉ፡ ተማረ፤
የበረታም፡ ነበረ፡ በነገር፡ በማድረግም።

፳፫፤ አርባ፡ አመትም፡በተፈጸመለት፡ጊዜ፡በልቡ፡
አሰበ፡ ወንድሞቹን፡ የእሥራኤል፡ ልጆች፡ ይጐበኝ፡
ዘንድ። ዘፀአ፡ ፪፡ ፲፩።

፳፬፤ አንድም፡ግፍ፡የተደረገበት፡ባየ፡ጊዜ፡ለተበደ
ለው፡ ተበቀለ፡ ረዳውም፡ ምሥሪውንም፡ ገደለው።

፳፭፤ ወንድሞቹም፡ የሚያውቁ፡ይመስለው፡ነበ
ረ፡ እግዚአብሔር፡ በጁ፡ እንደያድናቸው። እርሳቸ
ው፡ ግን፡ አላወቁም።

፳፮፤ በሚመጣውም፡ ቀን፡ ለሌሎች፡ ታያቸው፡
ሲጣሉ። ሊያስታርቃቸውም፡ ወደደ፡እንዲህ፡ ሲል።
እላንተ፡ሰዎች፡እላንተ፡ወንድማማች፡ናችሁ። ለም
ን፡ ግፍ፡ ትሰራላችሁ፡ እርሱ፡ በርሳችሁ።

፳፯፤ ባልንጀራውንም፡ የበደለው፡ከርሱ፡ገፋው፡
እንዲህ፡ ሲል። ማነው፡ አንተን፡ የሾመህ፡ በኛ፡ ላይ፡
አለቃ፡ መኰንንስ፡አድርጎ።

፳፰፤ ወይስ፡ ልትገድለኝን፡ ትወዳለህ፡ ትላንት፡
ምሥሪውን፡እንደ፡ገደልህ።

፳፱፤ ሙሴም፡ ስለዚህ፡ ነገር፡ ኰበለለ፡ ስደተኛ
ም፡ ሆነ፡ በምድያም፡ አገር፡ ከዚያም፡ ሁለት፡ልጆች፡
ወለደ። ዘፀአ፡ ፪፡ ፲፭።

፴፤ አርባ፡ አመትም፡ በተፈጸመ፡ ጊዜ፡ የእግዚአ
ብሔር፡ መልአክ፡ተገለጠለት፡ በሲና፡ተራራ፡ምድረ፡
በደ፡ በእሳት፡ ነበልባል፡ በሾህ፡ ቍጥቋጦ፡ መካከል።
ዘፀአ፡ ፫፡ ፪። ዘዳግ፡ ፴፫፡ ፲፮።

፴፩፤ ሙሴም፡ ባየ፡ ጊዜ፡ ከማየቱ፡ ተደነቀ። በቀረ
በም፡ ጊዜ፡ ሲመለከታት፡ የእግዚአብሔር፡ቃል፡ ወደ
ርሱ፡ መጣ፡ እንዲህ፡ ሲል።

፴፪፤ እኔ፡ ያባቶችህ፡ አምላክ፡ ነኝ። የአብርሃም፡
አምላክ። የይስሐቅም፡ አምላክ። የያዕቆብም፡ አ
ምላክ። ሙሴም፡ ፈርቶ፡ ሊመለከት፡ አልደፈረም።
ዘፀአ፡ ፫፡ ፮።

፴፫፤ እግዚአብሔርም፡ አለው። የግርህን፡ጫማ፡
አውጣ፡ አንተ፡ ቁመህበት፡ ያለህ፡ ስፍራ፡ የተቀደሰ
ች፡ ምድር፡ ናትና።

፴፬፡ ፈጽሜ፡ አየሁ፡ የወገኖቼን፡ መከራ፡ በምሥ
ር፡ ያሉትን። ቍዘማቸውንም፡ ሰማሁ፡ ላድናቸው
ም፡ ወረድሁ። አሁንም፡ ና፡ ልላክህ፡ ወደ፡ምሥር።

፴፭፤ ይህም፡ ሙሴ፡ የካዱት፡ እንዲህ፡ ሲሉ። ማ
ን፡ ሾመህ፡ አለቃ፡ መኰንንስ፡ አድርጎ። ይህነን፡ እግ
ዚአብሔር፡ ሰደደው፡አለቃ፡ መድኃኒትም፡ አድርጎ፡
በቍጥቋጦ፡በታየው፡በመልአኩ፡እጅ። ዘፀአ፡ ፪፡ ፲፬።

፴፮፤ ይህ፡ አወጣቸው፡ ተአምራት፡ ድንቅም፡ በ
ምሥር፡ ምድር፡ ባደረገ፡ ጊዜ፡ በኤርትራ፡ ባሕርም፡
በምድረ፡ በደም፡ አርባ፡ አመት። ዘፀአ፡ ፯፡ ፲።
፲፬፡ ፳፩።

፴፯፤ ይህ፡ ሙሴ፡ነው፡ ለእሥራኤል፡ልጆች፡ ያለ። እግዚአብሔር፡ አምላካችሁ፡ነቢይ፡ ያስነሣላችኋል፡ ከወንድሞቻችሁ፡ እንደኔ፡ ያለ። እርሱን፡ ስሙት።
ዘዳግ፡ ፲፰፡ ፲፭።

፴፰፤ ይህ፡ ነው፡ በማኅበሩ፡ የነበረ፡ በምድረ፡በዳ፡ በደብረ፡ ሲና፡ ከሚናገረው፡ መልአክ፡ ጋራ፡ ካባቶቻችንም፡ ጋራ። ሕያው፡ የሆነውን፡ ነገር፡ ለተቀበለ፡ ሊሰጠን።
ዘፀአ፡ ፲፱፡ ፫።

፴፱፤ አባቶቻችን፡ ያልወደዱት፡ይሰሙት፡ ዘንድ፡ ነገር፡ ግን፡ አራቁት፡ በልባቸውም፡ወደ፡ምሥር፡ተመለሱ።

፵፤ ሐሮንን፡ እንደህ፡ ሲሉ። አማልክት፡ ስራልን፡ በፊታችን፡ የሚሔዱ። ይህ፡ ሙሴ፡ ከምሥር፡ ምድር፡ ያወጣን፡ አናውቅምና፡ ምን፡ እንደገኘው።
ዘፀአ፡ ፴፪፡ ፩—፬።

፵፩፤ በዚያ፡ ወራት፡ጥጃ፡አደረጉ፡መሥዋዕትም፡ ለጣዖቱ፡ አቀረቡ፡ በጃቸውም፡ ስራ፡ደስ፡አላቸው።

፵፪፤ እግዚአብሔርም፡ ከርሳቸው፡ተመለሰ፡ አሳልፎም፡ ሰጣቸው፡ *የሰማይን፡ ጭፍራ፡ ያመልኩ፡ ዘንድ። ተበነቢያት፡ መጽሐፍ፡ እንደ፡ ተጻፈ። በውኑ፡ በምድረ፡ በደ፡ አርባ፡ አመት፡ ምሉ፡ መሥዋዕትና፡ ቍርባን፡ አቀረባችሁልኝን፡ እላንት፡ የእሥራኤል፡ ቤት። *ኤር፡ ፲፱፡ ፲፫። †ዓሞ፡ ፭፡ ፳፭፡ ፳፯።

፵፫፤ የሞሎክንም፡ ድንኳን፡ወሰዳችሁ፡ ያምላካችሁንም፡ ኰከብ፡ ስሙን፡ ሬምፋን፡የሚሉት፡የመሰላችሁትን፡ ምሳሌ፡ ልሰግዱለት። እሰዳችሁማለሁ፡ ከባቢሎን፡ ወደሚርቅ፡ አገር።

፵፬፤ የምስክር፡ድንኳን፡ካባቶቻችን፡ጋራ፡በምድረ፡ በደ፡ ነበረች። የሚናገረው፡ ሙሴን፡ እንደዘዘው፡ ያደርጋት፡ ዘንድ፡ እንዳየው፡ ምሳሌ።
ዘፀአ፡ ፳፭፡ ፵። ፳፯፡ ፴።

፵፭፤ ይህችን፡ አባቶቻችን፡ ተቀበልዋት፡ ይዘዋትም፡ገቡ፡ከኢያሱ፡ከነዌ፡ልጅ፡ጋራ፡ወደ፡ አሕዛብ፡ አገር። እግዚአብሔር፡ ካባቶቻችን፡ ፊት፡ያወጣቸው፡እስከ፡ዳዊት፡ ዘመን። ኢያ፡ ፫፡ ፲፬።

፵፮፤ ሞገስ፡ያገኘ፡በእግዚአብሔር፡ ፊት፡ለያዕቆብም፡ አምላክ፡ ማደርያ፡ ያገኝ፡ ዘንድ፡ የተመኘ።
፪፡ ሳሙ፡ ፯፡ ፪። መዝ፡ ፻፴፪፡ ፭።

፵፯፤ ሰሎሞን፡ ቤት፡ ሰራለት፡ እንጂ።
፩፡ ነገሥ፡ ፮፡ ፩።

፵፰፤ ነገር፡ ግን፡ልዑል፡ አያድርም፡ እጅ፡ በሰራው፡ ቤት። ነቢዩ፡ እንደለ።

፵፱፤ ሰማይ፡ዙፋኔ፡ነው፡ምድሪቱም፡የግሬ፡ድኍፎት። ምን፡ ቤት፡ነው፡የምትሰሩልኝ፡ የማርፍበትስ፡ ምን፡ ስፍራ፡ ነው። ኢሳ፡ ፷፮፡ ፩፡

፶፤ እጄ፡ ይህን፡ ሁሉ፡ የፈጠረች፡ አይደለችምን፡ ይላል፡ እግዚአብሔር።

፶፩፤ እላንት፡አንገተ፡ደንደናች፡ልባችሁም፡ ያልተገዘረ፡ጆሮዋችሁም። እላንት፡ሁለግዜ፡መንፈስ፡ ቅዱስን፡ትጣላላችሁ። እላንት፡ ደግሞ፡እንደባቶቻችሁ።
ዘፀአ፡ ፴፪፡ ፱።

፶፪፤ ማነው፡ ከነቢያት፡አባቶቻችሁ፡ያላሳደዱት። ገደሉም፡አስቀድመው፡ የጻድቁን፡መምጣት፡ የተናገሩትን፡ ዛሬ፡ እላንት፡ አሳልፋችሁ፡ የሰጣችሁት፡ የገደላችሁትም። ፪፡ ዜና፡ ፴፮፡ ፲፮። ማቴ፡ ፳፫፡ ፴፩።

፶፫፤ ሕግ፡ የተቀበላችሁ፡ በመላእክት፡ ሥርዓት፡ አልጠበቃችኋትምም። ዘፀአ፡ ፳፡ ፩።
ገላ፡ ፫፡ ፲፱። ዕብ፡ ፪፡ ፪።

፶፬፤ ይህነንም፡በሰሙ፡ጊዜ፡በልባቸው፡ተንጣጡ፡ ጥርሳቸውንም፡ በርሱ፡ ላይ፡ አፋጩ። ም፡ ፭፡ ፴፫።

፶፭፤ መንፈስ፡ ቅዱስም፡ መልቶበት፡ነበረ፡ ወደ፡ሰማይም፡ተመለከተ፡ የእግዚአብሔርንም፡ ክብር፡አየ፡ የሱስም፡ ቁሞ፡ በእግዚአብሔር፡ ቀኝ።

፶፮፤ አለም። እነሆ፡ ሰማዮች፡ ተከፍተው፡ አያለሁ፡ የሰው፡ ልጅም፡ ቁሞ፡ በእግዚአብሔር፡ ቀኝ።

፶፯፤ እርሳቸውም፡በታላቅ፡ቃል፡ጮሁ፡ጆሮዋቸውንም፡ደፈኑ፡ አንደግዜም፡ ባንድ፡ተነሡበት።
ም፡ ፳፪፡ ፳።

፶፰፤ ካገርም፡ ወደ፡ ሜዳ፡ አወጡት፡ ወገሩትም። ምስክሮችም፡ልብሳቸውን፡አኖሩ፡ባንድ፡ጐበዝ፡ እግር፡ ስሙን፡ ሳውል፡ የሚሉት።

፶፱፤ እስጢፋኖስንም፡ ወገሩ፡ ሲጸልይ፡ሲልም። የሱስ፡ ሆይ፡አቤቱ፡ነፍሴን፡ተቀበል። መዝ፡ ፴፩፡ ፯።
ሉቃ፡ ፳፫፡ ፵፮።

፷፤ በጕልበቱም፡ ተንበረከከ፡በታላቅ፡ ቃልም፡ጮኸ፡እንደህ፡ሲል። አቤቱ፡ይህችን፡ኃጢአት፡ *አትቍጠርባቸው። ይህነንም፡ብሎ፡አንቀላፋ። †ሳውልም፡ ከርሳቸው፡ ጋራ፡ በሞቱ፡ ደስታውን፡ አየበት።
*ሉቃ፡ ፳፫፡ ፴፬። †ም፡ ፯፡ ፶፰።

ምዕራፍ፡ ፰፤

፩፤ በዚያም፡ቀን፡ ታላቅ፡ስደት፡ሆነ፡ በየሩሳሌም፡ ባሉቸው፡ ቤተ፡ ክርስቲያን፡ ላይ። ሁሉም፡ *ተበተኑ፡ ወደ፡ ይሁዳ፡ አገር፡ ወደ፡ ሰማርያም፡ ከሐዋርያት፡በቀር። *ም፡ ፲፩፡ ፲፱።

፪፤ እስጢፋኖስንም፡ ያመኑ፡ ሰዎች፡ አነሡት፡ታላቅም፡ ልቅሶ፡ አደረጉለት። ማቴ፡ ፲፬፡ ፲፪።

፫፤ ሳውል፡ ግን፡ቤተ፡ ክርስቲያንን፡ ያፈርስ፡ ነበረ። ወደ፡ቤት፡ሁሉም፡ይገባ፡ነበረ፡ወንዶችንም፡ ሴቶችንም፡ ጐትቶ፡ወደ፡ ግዞት፡ ይጨምራቸው፡ ነበረ።
ም፡ ፱፡ ፩። ፳፪፡ ፬።

፬፤ የተበተኑት፡ ግን፡ ነገሩን፡ ኢያስተማሩ፡ ይዞሩ፡ ነበሩ።

፭፤ *ፊልጶስም፡ ከሰማርያ፡አገሮች፡ወደአንዲቱ፡ አገር፡ ወረደ፡ በክርስቶስም፡ አስተማረ፡ በርሳቸው፡ ዘንድ። *ም፡ ፮፡ ፭።

፮፡ ሕዝቡም፡ሁሉ፡የፊልጶስን፡ ነገር፡ተቀበሉ፡ያደ
ርጋት፡ የነበረውን፡ ተአምራት፡ በሰሙና፡ ባዩ፡ ጊዜ።
፯፡ ብዙ፡ሰዎች፡ ነበሩና፡ አጋንንት፡ ርኩሳን፡የነበሩ
ባቸው።በታላቅ፡ቃልም፡ ይጮሁ፡ ይወጡም፡ ነበር፡ከ
ርሳቸው። ብዙም፡ድውያን፡አንካሶችም፡ተፈወሱ።
ማቴ፡ ፲፮፡ ፲፯፡
፰፡ በዚያች፡ አገርም፡ ታላቅ፡ ደስታ፡ ሆነ።
ዮሐ፡ ፬፡ ፵፡
፱፡ አንድ፡ ሰውም፡ ነበረ፡ ስሙን፡ ሲሞን፡ የሚሉ
ት፡ከብዙም፡ዘመን፡ጀምሮ፡በዚያች፡አገር፡ይኖር፡ነበ
ረ። አስማተኛም፡ ነበረ፡ የሰማርያንም፡ ወገን፡ አስደ
ንቆ፡ ይኖር፡ ነበር፡ በማለቱ፡ እኔ፡ ታላቅ፡ ነኝ።
፲፡ ሁሉም፡ ይታዘዙት፡ነበሩ፡ ከታላላቆች፡ ጀምሮ፡
እስከ፡ታናናሾች። እንዲህ፡ ሲሉ። ይህ፡ነው፡ ታላቁ፡ የ
እግዚአብሔር፡ኀይል።
፲፩፡ ከርሱ፡ጋራ፡ይጣበቁ፡ ነበሩ፡ብዙ፡ ዘመን፡ ስለ፡
ተቀመጠ፡ አስማት፡ ሲያደርግባቸው።
፲፪፡ ግመኑ፡ጊዜም፡ ፊልጶስ፡ በነገራቸው፡ በእግዚ
አብሔር፡መንግሥት፡ በየሱስ፡ ክርስቶስም፡ ስም፡ ወ
ንዶችም፡ ሴቶችም፡ *ተጠመቁ። ማቴ፡ ፳፰፡ ፲፱።
፲፫፡ ሲሞንም፡ ራሱ፡ ደግሞ፡ አመነ፡ ተጠመቀም፡
ፊልጶስንም፡ አይለየውም፡ ነበረ። ተአምራትም፡ ባ
የ፡ ጊዜ፡ ታላቅ፡ ኀይልም፡በጁ፡ የምትደረግ፡ ተደነቀ።
፲፬፡ በሰሙም፡ጊዜ፡በየሩሳሌም፡ የነበሩ፡ ሐዋርያ
ት፡የሰማርያ፡ሰዎች፡ የእግዚአብሔርን፡ ነገር፡ እንደ፡
ተቀበሉ፡ ጴጥሮስንና፡ ዮሐንስን፡ ሰደዱላቸው።
፲፭፡ እርሳቸውም፡ወደርሳቸው፡ በገቡ፡ጊዜ፡ ስለር
ሳቸው፡ጸለዩ፡መንፈስ፡ ቅዱስን፡ ይቀበሉ፡ ዘንድ።
፲፮፡ ገና፡አልወረደም፡ነበርና፡ ከርሳቸው፡ ባንድ፡ በ
ንኳ።በየሱስ፡ስም፡ብቻ፡ተጠምቀው፡ ነበሩ፡ እንጂ።
፲፯፡ በዚያን፡ጊዜም፡እጃቸውን፡ ጫኑባቸው፡መን
ፈስ፡ቅዱስንም፡ ተቀበሉ።
፲፰፡ ሲሞንም፡ባየ፡ጊዜ፡ በሐዋርያት፡እጅ፡ መጫ
ን፡ መንፈስ፡ ቅዱስ፡ እንዲሰጥ፡ ብር፡ አመጣላቸው፡
እንዲህ፡ ሲል።
፲፱፡ ለኔም፡ደግሞ፡ ይህነን፡ መዓርግ፡ ስጡኝ፡ እጁ
ን፡ የጫንሁበት፡ ሁሉ፡ መንፈስ፡ ቅዱስን፡ ይቀበል፡ ዘ
ንድ።
፳፡ ጴጥሮስም፡ አለው። ብርህ፡ካንተ፡ ጋራ፡ ለጥፋ
ት፡ይሁን፡የእግዚአብሔርን፡ ጸጋ፡በብር፡ አገዛው፡ ብ
ለህ፡ አስበሃልና።
፳፩፡ ከዚህ፡ ነገር፡ ክፍል፡ ርስትም፡ የለህም። ልብ
ህ፡በእግዚአብሔር፡ ፊት፡ የቀና፡ አይደለምና።
፳፪፡ አሁንም፡ ንስሐ፡ ግባ፡ ከዚህ፡ ክፋትህ፡ ወደ፡
እግዚአብሔርም፡ለምን፡ምን፡ አልባት፡የልብህን፡አ
ሳብ፡ ይተውልህ፡ እንደ፡ ሆነ።
፳፫፡ በኀጢአት፡መራርነት፡ በግፍም፡ ትብትብ፡ እ
ንደለህ፡ አይሃለሁና።
፳፬፡ ሲሞንም፡መለሰ፡አለም።እላንት፡ወደ፡እግ
ዚአብሔር፡ለምኑልኝ።እላንት፡ካላችሁት፡ አንዳች፡
እንዳያገኘኝ።
፳፭፡ እርሳቸውም፡ በመሰከሩ፡ የእግዚአብሔር
ንም፡ ነገር፡ በነገሯቸውም፡ ጊዜ፡ወደ፡ የሩሳሌም፡ ተ
መለሱ፡ በሰማርያም፡ ብዙ፡ መንደር፡ በወንጌል፡ አስ
ተማሩ።
፳፮፡ የእግዚአብሔርም፡መልአክ፡ ፊልጶስን፡ተና
ገረው፡እንዲህ፡ሲል።ተነሣና፡ሒድ፡ በደቡብ፡ከየሩሳ
ሌም፡እስከ፡ ጋዛ፡ በምታወርደው፡ መንገድ። እርስዋ
ም፡ ምድረ፡ በዳ፡ናት።
፳፯፡ ተነሥቶም፡ ሔደ። እነሆም፡ አንድ፡ የኢትዮ
ጵያ፡ ሰው፡ነበረ፡ ጃንደረባ፡ ከሕንደኬ፡ከኢትዮጵያ፡
ንግሥት፡ ከሹማምንቶዋ፡ የበለጠ፡ በከብትዋም፡ ሁ
ሉ፡ የሰለጠነ። ይህ፡ወደ፡ የሩሳሌም፡መጣ፡ ሊሰግድ።
፳፰፡ ተመለሰም፡ በሠረገላ፡ ተቀምጦ፡ የነቢዩን፡
የኢሳይያስን፡ መጽሐፍ፡ ኢያነበበ።
፳፱፡ መንፈስ፡ቅዱስም፡ፊልጶስን፡አለው።ሒድ፡
ለዚህም፡ ሠረገላ፡ ቅረብ፡ ተገናኘውም።
፴፡ ፊልጶስም፡በደረሰ፡ጊዜ፡ሰማው፡ኢሳይያስን፡
ነቢዩን፡ሲያነብ። አለውም። የምታነበውን፡ ታውቃለ
ህን።
፴፩፡ እርሱም፡ አለ። ይህ፡ እንዴት፡ ይቻለኛል፡ የ
ሚያስተምረኝ፡ ባይኖር። ፊልጶስንም፡ ለመነው፡ ወ
ደ፡ ሠረገላው፡ ወጥቶ፡ ከርሱ፡ ጋራ፡ ይቀመጥ፡ ዘንድ።
፴፪፡ የመጽሐፉ፡ግን፡ስፍራ፡ያነበው፡የነበረ፡ ይህ፡
ነበር።እንደ፡*በግ፡ወደ፡መታረድ፡ተነዳ፡እንደ፡ በግ፡ጥ
ቦትም፡በሸላቹ፡ፊት፡ዝም፡እንዲል፡እንደሁ፡አፉን፡
አልከፈተም። *ኢሳ፡ ፶፫፡ ፯።
፴፫፡ በውርደቱ፡ፍርዱ፡ወገደ።ትውልዱንም፡ ማ
ን፡ ይነግርበታል፡ ሕይወቱ፡ከምድር፡ ተቈርጣለችና።
፴፬፡ ጃንደረባውም፡ መለሰ፡ ፊልጶስንም፡ አለ
ው።እለምንሃለሁ፡ ትነግረኝ፡ ዘንድ፡ይህነን፡ ስለ፡ ማ
ን፡ይናገራል፡ ነቢዩ። ስለ፡ራሱን፡ ወይስ፡ ስለ፡ ሌላው።
፴፭፡ ፊልጶስም፡አፉን፡ከፈተ፡ከዚህም፡ መጽሐ
ፍ፡ ጀምሮ፡ ስለ፡ የሱስ፡ ያስተምረው፡ ነበር።
፴፮፡ እርሳቸውም፡ በመንገድ፡ ሲሔዱ፡ ወደ፡ ው
ኃ፡ደረሱ።ጃንደረባውም፡አለ። እነሆ፡ውኃ። ማነው፡
የሚከለክለኝ፡ እንዳልጠመቅ።
፴፯፡ ፊልጶስም፡አለ።በፍጹም፡ልብህ፡ ብታምን፡
ይገባልሃል።መለሰም፡አለም። እኔ፡አምናለሁ፡ *የሱ
ስ፡ ክርስቶስ፡ የእግዚአብሔር፡ ልጅ፡ እንደ፡ሆነ።
*ማቴ፡ ፲፮፡ ፲፮። ማር፡ ፲፮፡ ፲፮።
፴፰፡ ሠረገላውም፡ ይቆም፡ ዘንድ፡ አዘዘ። ፊልጶ
ስና፡ ጃንደረባውም፡ ወደ፡ ውኃ፡ ወረዱ፡ አጠመቀ
ውም።
፴፱፡ ከውኃውም፡በወጡ፡ጊዜ፡የእግዚአብሔር፡
*መንፈስ፡ ፊልጶስን፡ ነጠቀው፡ ጃንደረባውም፡ ደግ
ሞ፡ አላየውም። መንገዱን፡ ደስ፡ ብሎት፡ ሒድዋ
ልና። *፩፡ ነገሥ፡ ፲፰፡ ፲፪።

፵፡ ፊልጶስ፡ግን፡በአዛጦን፡ተገኘ። ሲዞርም፡አገሩ
ን፡ ሁሉ፡በወንጌል፡ ያስተምር፡ ነበር፡ ወደ፡*ቂሣርያ፡
እስኪመጣ፡ ድረስ። *ም፡ ፳፩፡ ፰፡ ፱።

ምዕራፍ፡ ፱፡

፩፡ ሳውል፡ግን፡ገና፡ቍጣና፡የጌታን፡ ደቀ፡ መዛሙ
ርት፡ ለመግደል፡ ኢያንፈነፈ፡ ወደ፡ ካህናቱ፡ አለቃ፡
መጣ። ም፡ ፰፡ ፫። ፳፪፡ ፫—፳፩፡
፪፡ ከርሱም፡ ጽፈት፡ለመነ፡በደማስቆ፡ ወዳለው፡
መስጊድው፡ሁሉ።በዚህ፡መንገድ፡ያሉን፡ሰዎች፡ቢያ
ገኝ፡ ወንዶችንም፡ ሴቶችንም፡ አሥሮ፡ ወደ፡ የሩሳሌ
ም፡ ያመጣቸው፡ ዘንድ።
፫፡ በሔደም፡ጊዜ፡ወደ፡ደማስቆም፡ በቀረበ፡ጊዜ፡
ድንገት፡ በርሱ፡ ላይ፡ ብርሃን፡ከሰማይ፡ በራ።
፩፡ ቆሮ፡ ፲፭፡ ፰።
፬፡ በምድር፡ ላይም፡ ወደቀ፡ ድምጽም፡ ሰማ፡የ
ሚል። ሳውል። ሳውል፡ ለምን፡ ታሳድደኛለህ።
፭፡ አለውም። አንተ፡ ማነህ፡ አቤቱ። ጌታም፡ አለ
ው።እኔ፡የሱስ፡ነኝ፡አንተ፡ የምታሳድደኝ። በተሳለ፡ብረ
ት፡ላይ፡ብትረግጥ፡ላንተ፡ ይብሰሃል። ም፡ ፭፡ ፴፱።
፮፡ ኢየፈራም፡ኢየተንቀጠቀጠም፡አለ።አቤቱ፡
ምን፡ ትሻለህ፡ አደርግ፡ ዘንድ። ጌታም፡አለው፡ ተነ
ሣና፡ወደ፡ከተማ፡ሒድ። ከዚያም፡ ትሰማለህ፡ ታደ
ርገው፡ ዘንድ፡ የሚገባህን።
፯፡ ሰዎች፡ግን፡ ከርሱ፡ ጋራ፡ ባንድ፡ የነበሩት፡ ተደን
ቀው፡ ቆሙ፡ ድምጽ፡ ኢየሰሙ፡ ማንንም፡ ሳያዩ።
፰፡ ሳውልም፡ ከምድር፡ ተነሣ፡ዓይኖቹም፡ በተከ
ፈቱ፡ ጊዜ፡ ማንንም፡ አላየም። መርተውም፡ ወደ፡ደ
ማስቆ፡ አገቡት።
፱፡ ሶስት፡ቀንም፡ ተቀመጠ፡ ሳያይ፡ ሳይበላም፡ ሳ
ይጠጣም።
፲፡ በደማስቆም፡ አንድ፡ ደቀ፡መዝሙር፡ ነበረ፡ ስ
ሙን፡ ሐናንያ፡የሚሉት። ጌታም፡ በራእይ፡ አለው።
ሐናንያ፡ ሆይ። እርሱም፡ አለ። እነሆኝ፡አቤቱ።
፲፩፡ ጌታም፡አለው። ተነሥተህ፡ ሒድ፡ በመንገድ፡
ቅን፡መንገድ፡በምትባል።በይሁዳ፡ ቤትም፡አንድ፡ ሰ
ው፡እሻ፡ስሙን፡ሳውል፡ የሚሉት፡ አገሩም፡ *ጠርሴ
ስ። እነሆ፡ ይጸልያልና። *ም፡ ፳፩፡ ፴፱።
፲፪፡ በራእይም፡ አንድ፡ ሰው፡ አየ፡ ስሙን፡ ሐናን
ያ፡የሚሉት፡ ሲገባ፡እጁንም፡በላዩ፡ ሲጭንበት፡ያይ፡
ዘንድ።
፲፫፡ ሐናንያም፡መለሰ፡ አለም። አቤቱ፡ ከብዙ፡ ሰ
ዎች፡የዚህን፡ሰው፡ነገር፡ፈጽሜ፡ ሰማሁ፡ስንት፡ክፉ፡
እንደደረገ፡ በቅዱሳንህ፡ በየሩሳሌም።
፲፬፡ ከዚህም፡ ከካህናት፡ አለቆች፡ ሥልጣን፡ አለ
ው፡ ስምህን፡ የሚጸሩን፡ ሁሉ፡ ያሥር፡ዘንድ።
፩፡ ቆሮ፡ ፩፡ ፪።
፲፭፡ ጌታም፡ አለው። ሒድ፡ይህ፡ ለኔ፡ የተመረጠ፡
እቃ፡ነውና፡ ስሜን፡ይሸከም፡ዘንድ፡በአሕዛብ፡ፊት፡
*በነገሥታትም፡ በእሥራኤል፡ ልጆችም።
*ም፡ ፳፭፡ ፲፫። ሮሜ፡ ፩፡ ፭።
፲፮፡ እኔም፡ስለ፡ስሜ፡ የሚቀበለውን፡ መከራ፡ አ
ሳታውቀዋለሁ። ቍ፡ ፳፫። ፪፡ ቆሮ፡ ፲፩፡ ፳፫።
፲፯፡ ሐናንያም፡ሔደ፡ወደ፡ቤትም፡ገባ፡እጁንም፡
ጫነበት፡ አለም። ወንድሜ፡ ሆይ፡ ሳውል። ጌታ፡ ወደ
ንተ፡ላከኝ።የሱስ፡በመንገድ፡የታየኸው፡ ስትመጣ።
ታይ፡ ዘንድ፡ መንፈስ፡ቅዱስም፡ ይመላብህ፡ ዘንድ።
፲፰፡ የዚያን፡ ጊዜም፡ ካይኑ፡ ወደቀ፡ እንደ፡ ቅርፊ
ት፡ ያለ። አየም፡ ተነሥቶም፡ ተጠመቀ።
፲፱፡ መብልም፡ በተቀበለ፡ ጊዜ፡በረታ። ሳውልም፡
በደማስቆ፡ካሉ፡ከደቀ፡መዛሙርት፡ጋራ፡ግንድ፡ ሆነ፡
ጥቂት፡ ቀን።
፳፡ የዚያን፡ ጊዜውም፡ በክርስቶስ፡ አስተማረ፡በ
መስጊዶች፡እርሱ፡የእግዚአብሔር፡ልጅ፡ እንደ፡ ሆነ።
፳፩፡ የሰሙትም፡ሁሉ፡ተደነቁ፡አሉም።ይህ፡*በየ
ሩሳሌም፡ይህነን፡ስም፡የሚጸሩን፡ሁሉ፡ ያጠፋ፡አይ
ደለምን። ስለዚህም፡ ወደዚህ፡ መጣ፡አሥሮ፡ ወደ፡
ካህናት፡ አለቆች፡ ሊወስዳቸው። *ቍ፡ ፩፡ ፲፬።
ም፡ ፰፡ ፩። ፳፮፡ ፲።
፳፪፡ ሳውልም፡ ኃይል፡ ይጨመርለት፡ ነበረ፡ በደ
ማስቆ፡ የተቀመጡትንም፡ አይሁድ፡ ያውክ፡ ነበረ።
ይህ፡ ክርስቶስ፡ እንደ፡ ሆነ፡ ሲገልጠላቸው።
ም፡ ፲፰፡ ፳፰።
፳፫፡ ብዙ፡ ቀንም፡ ከሆነ፡ በኋላ፡ አይሁድ፡ አንድ፡
ሁነው፡ ተማከሩ፡ ይገሉት፡ ዘንድ።
፳፬፡ ሳውልም፡ እንደ፡ተማከሩበት፡ አወቀ። ደጆ
ችንም፡ ይጠብቁ፡ ነበሩ፡ በሌት፡ በቀንም፡ ይገሉት፡ ዘ
ንድ።
፳፭፡ ደቀ፡መዛሙርቱ፡ግን፡ በሌት፡ ወሰዱት፡ በቅ
ጥርም፡ ላይ፡ በንቅብ፡ አወረዱት።
፪፡ ቆሮ፡ ፲፩፡ ፴፪፡ ፴፫።
፳፮፡ ሳውልም፡ ወደ፡ የሩሳሌም፡ በመጣ፡ ጊዜ፡ ከ
ደቀ፡ መዛሙርት፡ ጋራ፡ ባንድ፡ ይሆን፡ ዘንድ፡ ወደደ።
ሁሉም፡ ፈሩት፡ ባያምኑት፡ ደቀ፡ መዝሙር፡ እንደ፡
ሆነ። ገላት፡ ፩፡ ፲፯።
፳፯፡ በርናባስ፡ ግን፡ ወሰደው፡ወደ፡ ሐዋርያትም፡
አገባው፡ አጫወታቸውም፡ ጌታን፡ በመንገድ፡ እንደ
የው፡እንደ፡ ተናገረውም። በደማስቆም፡ እንደ፡ ተጋ
ደለ፡ በየሱስ፡ ስም። ቍ፡ ፳።
፳፰፡ ከርሳቸውም፡ጋራ፡ ተቀመጠ፡ ሲገባ፡ ሲወጣ
ም፡ በየሩሳሌም፡ በየሱስም፡ በጌታ፡ ስም፡ ሲጋደል።
፳፱፡ ለአይሁድም፡ ይናገር፡ነበረ፡ ከፅርዕ፡ አገር፡ ለ
ሚሆኑ፡ይከራከራቸውም፡ነበር። እርሳቸው፡ ግን፡ሊ
ገሉት፡ ወደዱ።
፴፡ ወንድሞችም፡ይህነን፡ባወቁ፡ ጊዜ፡ ወደ፡ ቂሣ
ርያ፡ ወሰዱት፡ ወደ፡ *ጠርሴስም፡ ሰደዱት።
*ም፡ ፲፩፡ ፳፭።
፴፩፡ ቤተ፡ክርስቲያኒቱ፡ሁሉ፡ግን፡ በይሁዳ፡ የነበረ

ችው፡በገሊላም፡ በሰማርያም፡ በይሁዳ፡ ነበረች። ተሰ
ርታ፡በእግዚአብሔር፡ፍርሃትም፡ጸንታ። በምንፈስ፡
ቅዱስም፡ጸጋ፡በዙ።
፴፪፡ ጴጥሮስም፡ በየስፍራው፡ ሲዞር፡ በልዳ፡ ወደ
ሚኖሩ፡ ቅዱሳን፡ ወረደ።
፴፫፡ ከዚያም፡አንድ፡ ሰው፡ ስሙን፡ ኤንያ፡ የሚ
ሉት፡ አገኘ። ባልጋ፡ ላይ፡ ወድቆ፡ ከስምንት፡ አመት፡
ጀምሮ፡ መፃጉዕም፡ ነበረ።
፴፬፡ ጴጥሮስም፡አለው። ኤንያ፡ ሆይ፡ የሱስ፡ ክር
ስቶስ፡ይፈውስሀ።ተነሣ፡ለራስህም፡አንጽፍ። የዚያ
ን፡ ጊዜውም፡ ተነሣ።
፴፭፡ በልዳም፡ የሚኖሩ፡ ሁሉ፡ በሰሮናም፡ አዩት፡
ወደ፡ እግዚአብሔርም፡ ተመለሱ።
፴፮፡ በኢዮጴም፡አንዲት፡ረድ፡ነበረች፡ስምዋን፡
ጣቢታ፡ የሚልዋት ። ስምዋም፡ ይተረጐማል ፡ ምዳ
ቋ፡ተብሎ።ይህቺም፡ መልካም፡ ነገር፡ መልተባት፡ነበ
ር፡*ምጽዋትም፡ታደርግ፡ነበረች። *መዝ፡ ፵፩፡ ፪፡፡
፴፯፡ በዚያቺም፡ ወራት፡ ታመመች ፡ ሞተችም።
አፀብዋትም፡ በደርብ፡ ላይም፡ አደረጏት።
፴፰፡ ልዳም፡ ለኢዮጴ፡ ቅርብ፡ ናትና፡ ደቀ፡ መዛ
ሙርት፡ ጴጥሮስ፡ ከዚያ፡ እንደ፡ለ፡ በሰሙ፡ ጊዜ፡ ሁለ
ት፡ሰዎች፡ወደርሱ፡ ላኩ፡ ይለምኑት፡ ዘንድ፡ እምቢ፡
እንዳይል፡ ወደርሳቸው፡ ከመምጣት።
፴፱፡ ጴጥሮስም ፡ ተነሣ ፡ ከርሳቸውም ፡ ጋራ ፡ መ
ጣ። ወደርሳቸውም፡ በደረሰ፡ ጊዜ፡ ወደ፡ ደርብ፡ አወ
ጡት። በፊቱም፡ቆሙ፡ ባልቴቶች፡ ሁሉ፡ እያለቀሱ፡
ቀሚሶችንም፡ልብሶችንም፡ እያሳዩት፡ ምዳቋ፡ ታደ
ርገው፡የነበረችውን፡ ከርሳቸው፡ ጋራ፡ ሳለች።
፵፡ ጴጥሮስም፡ሁሉን፡ወደ፡ሜዳ፡አወጣ፡ በተንበ
ረከከም፡ ጊዜ፡ ጸለየ፡ ወደ፡ በድንም፡ ተመለሰ፡ አለ
ም። ጣቢታ፡ ሆይ፡*ተነሺ። እርስዋም፡ ዓይንዋን፡ ገለ
ጠች፡ ጴጥሮስንም፡ ባየች፡ ጊዜ፡ ተቀመጠች።
*ማር፡ ፭፡ ፵፩፡፡ ሉቃ፡ ፰፡ ፲፬፡፡
፵፩፡ እጁንም፡ሰጣት፡አስነሣትም፡ቅዱሳንንም፡
ባልቴቶችንም፡ ጸራ፡ ደህናም፡ ሁና፡ በፊታቸው፡ አቀ
ማት።
፵፪፡ ይህም፡ ወሬ፡ የታወቀ፡ ሆነ፡ በኢዮጴ፡ ሁሉ።
*ብዙም፡ ሰዎች፡ በጌታ፡ አመኑ።
*ዮሐ፡ ፰፡ ፴፡፡ ፲፡ ፵፪፡፡
፵፫፡ አያሌ፡ቀንም፡በኢዮጴ፡ተቀመጠ፡ወደንድ፡
ሰው፡ ስምዖን፡የሚባል፡ቀርበት፡ ፋቂ። ም፡ ፲፡ ፯፡፡

## ምዕራፍ፡ ፲፡

፩፡ በቂሣርያም ፡ አንድ፡ሰው፡ ነበረ፡ ስሙን፡ ቆርኔ
ሌዎስ፡ የሚሉት፡ *የመቶ፡ አለቃ፡ ለጭፍራ፡ ኢጣሊ
ቄ፡ ለሚልዋት። *ማቴ፡ ፰፡ ፭፡፡
፪፡ መልካም፡ የሚሰራ፡እግዚአብሔርንም፡የሚ
ፈራ፡ ከቤቱ፡ ሰዎች፡ ሁሉ፡ጋራ። እጅግም፡ ምጽዋት፡
*ለሕዝብ፡ያደረገ፡ ወደ፡ እግዚአብሔርም፡ሁለግዜ፡
የለመነ። *ዳን፡ ፬፡ ፳፬፡፡
፫፡ እርሱም፡በግልጥ፡በቀኑ፡ በዘጠኝ፡ ሰዓት፡የእግ
ዚአብሔርን፡መልአክ፡በራእይ፡አየ፡ወደርሱ፡ ሲገባ፡
ሲለውም። ቆርኔሌዎስ፡ ሆይ።
፬፡ እርሱም ፡ በተመለከተው ፡ ጊዜ፡ ፈራ፡ አለው
ም።ምንድር፡ነገር፡ ነው፡ጌታ፡ሆይ። መልአኩም፡ አለ
ው። ጸሎትህ፡ምጽዋትህም፡በእግዚአብሔር፡ፊት፡
ለመታሰብ፡ ወጣ።
፭፡ አሁንም፡ ሰዎች፡ ላክ፡ ወደ፡ ኢዮጴ፡ ሲሞንን
ም፡ጴጥሮስ፡ የሚባለው፡ አስመጣ።
፮፡ እርሱም፡ እንግድነት፡ መጥትዋል፡ ወደንድ፡ ሰ
ው፡ ሲሞን፡*ቀርበት፡ ፋቂ፡ ወደሚሉት። ቤቱም፡ በ
ባሕር፡ አጠገብ ። እርሱ ፡ ይነግርሃል፡ †ታደርገው፡ ዘን
ድ፡የሚገባህን፡ነገር። *ም፡ ፱፡ ፵፫፡፡ †ም፡ ፪፡ ፴፮፡፡
፯፡ መላኩም፡ ቆርኔሌዎስን፡ የነገረው፡ በሔደ፡ ጊ
ዜ፡ ሁለቱን፡ ሎሌልቱን፡ ጸራ፡ ዘወትርም፡ ከማይለዩ
ት፡ ከጭፍሮቹ፡ አንዲን፡ እግዚአብሔርን፡ የሚፈራ
ን፡ወታደር።
፰፡ ነገሩንም ፡ ሁሉ ፡ አጫወታቸው ፡ ወደ ፡ ኢዮጴ
ም፡ ሰደዳቸው።
፱፡ በነገውም፡እርሳቸው፡በመንገድ፡ሲሔዱ፡ወደ
ገርም፡በቀረቡ፡ጊዜ፡ ጴጥሮስ፡ወደ፡ ሰገነት፡ ወጣ፡ ይጸ
ልይ፡ ዘንድ፡ በስድስት፡ ሰዓት።
፲፡ ተራበም፡ ሊበላም፡ ወደደ። ሰዎችም፡ መብል፡
ሲያበጁ፡ ራእይ፡ ወደቀበት።
፲፩፡ ሰማዮችም ፡ ተከፍተው ፡ አየ ፡ መጐናጸፊያ
ም፡ ሲወርድ፡ እንደ ፡ ታላቅ፡ ልብስ ፡ ወደ ፡ ምድርም፡
ደርሶ፡*ባራት፡ ወገን፡ታሥሮ። *ም፡ ፲፩፡ ፭፡፡
ሉቃ፡ ፲፫፡ ፳፱፡፡
፲፪፡ የምድርም፡ እንስሳ፡ ሁሉ፡ ነበረበት፡ አራዊት
ም፡ የሚንቀሳቀስም፡ የሰማይም፡ ወፎች።
፲፫፡ ድምጽም፡ወደርሱ፡ መጣ፡እንዲህ፡ ሲል። ተነ
ሣ፡ ጴጥሮስ፡ ሆይ፡ አርደህ፡ ብላ።
፲፬፡ ጴጥሮስም ፡ አለ ። አይሆንም ፡ ከቶ ፡ አቤቱ።
*ርኩስ ፡ የሚያስጸይፍም ፡ በልቼ ፡ ከቶ ፡ አላውቅ
ምና። *ሕዝ፡ ፬፡ ፲፬፡፡ ዘሌዋ፡ ፲፩፡ ፰፡ ፲፫፡ ፳፫፡፡
፲፭፡ ድምጽም፡ ደግሞ፡ ሁለተኛ፡ ወደርሱ፡ መጣ፡
እንደህ፡ሲል።እግዚአብሔር፡*ያነጻውን፡አንተ፡አታ
ርክሰው። *ማቴ፡ ፲፭፡ ፲፩፡፡
፲፮፡ ይህም፡ሆነ፡ሶስትግዜ። እቃውም፡ ከዚያ፡ ወ
ዲያ፡ ወደ፡ ሰማይ፡ ተመለሰ።
፲፯፡ ጴጥሮስም፡ በልቡ፡ ሲማገር፡ያየው፡ ራእይ፡ም
ንድር፡ነው፡ብሎ። እነሷቸው፡ ሰዎች፡ቆርኔሌዎስ፡የላ
ካቸው ፡ የሲሞንን ፡ ቤት፡ ይጠይቁ፡ በደጁም፡ ቁመ
ው፡ነበሩ።
፲፰፡ ጸሩም፡ ይጠይቁ፡ዘንድ፡ ሲሞን ፡ ጴጥሮስ፡ የ
ሚባለው፡ ከዚያ፡ እንግድነት፡ መጥቶ፡ እንደ፡ ሆነ፡ ብ
ለው።

፲፱፤ ጴጥሮስም፡ ሲያስብ፡ባየው፡ራእይ፡ መንፈስ፡ ቅዱስ፡ አለው። እነሆ፡ ሦስት፡ ሰዎች፡ ይሹሃል።

፳፤ ነገር፡ግን፡ ተነሣና፡ ውረድ፡ ከርሳቸው፡ጋራ፡ ሒድ፡በሁለት፡ልብም፡አትሁን። እኔ፡ ልኪያቸዋለሁና።

፳፩፤ ጴጥሮስም፡ ከቆርኔሌዎስ፡ ወደ፡ ተላኩት፡ ሰዎች፡በወረደ፡ ጊዜ፡አለ። እነሆ፡ እኔ፡ ነኝ፡ የምትሹኝ። ምን፡ ምክንያት፡ ነው፡ የመጣችሁበት።

፳፪፤ እርሳቸውም፡አሉ። ቆርኔሌዎስ፡ የመቶ፡አለቃ፡ ጻድቅ፡ ሰው፡ እግዚአብሔርንም፡ የሚፈራ፡ የተመሰከረለትም፡ በአይሁድ፡ ወገን፡ ሁሉ። ቅዱስ፡ መልአክ፡ታየው፡ወደ፡ቤቱም፡ያመጣህ፡ ዘንድ፡አለው፡ ካንተም፡ ነገር፡ ይሰማ፡ ዘንድ።

፳፫፤ ጸራቸውም፡እንግድነትም፡ተቀበላቸው። በነገውም፡ጴጥሮስ፡ከርሳቸው፡ጋራ፡ ወጣ፡ ሰዎችም፡ በኢዮጴ፡ ካሉ፡ ወንድሞች፡ ከርሱ፡ ጋራ፡ ሔዱ።

፳፬፤ በነገውም፡ ወደ፡ ቄሣርያ፡ ገቡ ። ቆርኔሌዎስም፡ ዘመዶችን፡ የቀረቡትንም፡ ወዳጆቹን፡ ጸርቶ፡ ይጠብቃቸው፡ ነበር።

፳፭፤ ጴጥሮስም፡ በገባ፡ ጊዜ፡ ቆርኔሌዎስ፡ ተቀበለው፡ በግሩም፡ ወድቀ፡ ሰገደለትም።

፳፮፤ ጴጥሮስ፡ ግን፡ አስነሣው፡ እንዲህ፡ ሲል ። ተነሣ፡ እኔ፡ ደግሞ፡ ሰው፡ ነኝና። ምዕ፡ ፲፬፤ ፲፭፡፡ ራእ፡ ፲፱፤ ፲፡፡

፳፯፤ ከርሱ፡ጋራ፡ኢየተናገረም፡ገባ፡ እጅግ፡ሰዎችም፡አገኘ፡ ከርሱ፡ ዘንድ፡ተከማችተው።

፳፰፤ አላቸውም ። እላንተ፡ ታውቃላችሁ ፡ ለአይሁድ፡ሰው፡እንዲደገባ፡ደገናኘና፡ደገባ፡ዘንድ፡ወደ፡ሌላ፡ ወገን። ነገር፡ግን፡ እግዚአብሔር፡ አሳየኝ፡ ከሰው፡ ማንንም፡ እንዳልል፡ ርኩስ፡ ወይ፡ የሚያስጸይፍ፡ ነው።

፳፱፤ ስለዚህም፡ሳልጠራጠር፡ መጣሁ፡ብጠሩኝ። አሁንም፡እጠይቃችኋለሁ፡ለምን፡ ምክንያት፡ አመጣችሁኝ።

፴፤ ቆርኔሌዎስም፡ አለ። ካራት፡ቀን፡ ጀምሬ፡እስከዚች፡ሰዓት፡ድረስ፡ጾመኛ፡ነበርሁ። ስጸልይም፡ በቤቴ፡በዘጠኝ፡ ሰዓት፡እነሆ፡ አንድ፡ ሰው፡ በፊቴ፡ ቆመ፡ ነጭ፡ ልብስ፡ለብሶ።

፴፩፤ አለም። ቆርኔሌዎስ፡ ሆይ፡ ጸሎትህ፡ ተሰማችልህ፡ምጽዋትህም፡ታሰበችልህ፡ በእግዚአብሔር፡ ፊት።

፴፪፤ አሁንም፡ወደ፡ኢዮጴ፡ላክ፡ሲሞንንም፡ጴጥሮስ፡የሚባለውን፡አስመጣ። እርሱ፡እንግድነት፡ተቀምጥዋል፡በቆርበት፡ፋቂው፡ በሲሞን፡ቤት፡ በባሕር፡ አጠገብ። እርሱም ፡ መጥቶ፡ ነገር፡ ይነግርሃል።

፴፫፤ የዚያን፡ጊዜም፡ላክሁብህ። አንተም፡መልካም፡ስራ፡ሰራህ፡በመምጣትህ። አሁንም፡እነሆ፡እኛ፡ ሁላችን፡ ከዚህ፡ አለነ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት፡ እንሰማ፡ዘንድ፡አንተ፡ የታዘዝህበትን፡ ሁሉ፡ ከእግዚአብሔር፡ ዘንድ።

፴፬፤ ጴጥሮስም፡አፉን፡ ከፈተ፡ አለም። በውነት፡ አስተዋልሁ፡ እግዚአብሔር፡ ለሰው፡ ፊት፡ እንደያደላ። ፩፤ ሰሙኤ፡ ፲፮፤ ፯፡፡ ሮሜ፡ ፪፤ ፲፩፡፡

፴፭፤ ነገር፡ግን፡ በሕዝብ፡ ሁሉ፡ የሚፈራው፡ ቅን፡ ነገርም፡ የሚያደርግ፡ እርሱ፡ በርሱ፡ ዘንድ፡ የተቀበለ፡ ነው። ዮሐ፡ ፲፤ ፲፮፡፡

፴፮፤ ወደ፡ እሥራኤል፡ ልጆች ፡ የላከውን፡ ነገር፡ የምስራች፡ ሲነግራቸው ፡ በደህንነት ፡ በየሱስ፡ ክርስቶስ። እርሱ፡ *የሁሉ፡ ጌታ፡ ነው። *ማቴ ፳፰፤ ፲፰፡፡

፴፯፤ ይህን፡ ነገር፡እላንተ፡ታውቃላችሁ፡ በይሁዳ፡ ሁሉ፡የሆነውን፡ከገሊላ፡ጀምሮ፡ ዮሐንስ፡ ካስተማረበት፡ጥምቀት፡ በኋላ። ማቴ፡ ፬፤ ፲፪፡፡

፴፰፤ ስለ፡ የሱስ፡ ስለ፡ናዝሬቱ፡እግዚአብሔር፡ በመንፈስ፡ቅዱስ፡በኃይልም፡ቀብቶታልና። የመጣ፡መልካምም፡ ያደረገ፡ ሰይጣን፡ ያሸነፋቸውንም ፡ ሁሉ፡ የፈወሰ። እግዚአብሔር፡ከርሱ፡ጋራ፡ ነበርና። ኢሳ፡ ፷፩፤ ፩፡፡

፴፱፤ እኛም፡ምስክሮች፡ ነነ፡ ባደረገው፡ነገር፡ ሁሉ፡ በይሁዳ፡አገር፡በየሩሳሌምም። ይህን፡የገደሉት፡ በንጨት፡ ላይ፡ ሰቅለው።

፵፤ ይህነን፡እግዚአብሔር፡ አስነሣው፡ በሦስተኛ፡ ቀን፡ ሰጠውም፡ ይገለጥ፡ ዘንድ።

፵፩፤ ለሕዝብ፡ሁሉ፡አይደለም፡ለምስክሮች፡እንጂ፡ እግዚአብሔር፡ አስቀድሞ፡ ለመረጣቸው። እኛም፡ነነ፡ከርሱ፡ጋራ፡ የበላነ፡ የጠጣነም፡ ከሙታን፡ ከተነሣ፡ በኋላ። ዮሐ፡ ፲፬፤ ፳፪፡፡ ፲፭፤ ፳፯፡፡

፵፪፤ ለሕዝብም ፡ እናስተምር ፡ እንመሰክርም፡ ዘንድ፡አዘዘነ፡ ይህ፡እንደ፡ሆነ፡ እግዚአብሔር፡ የመረጠው፡ በሕያዋንና፡ በሙታን፡ *ይፈርድ፡ ዘንድ። *ምዕ፡ ፲፯፤ ፴፩፡፡

፵፫፤ ለርሱም ፡ ይመሰክራሉ ፡ *ነቢያት፡ ሁሉ፡ በርሱ፡የሚያምን፡ሁሉ፡የኃጢአቱን፡ሰርየት፡እንዲወስድ፡በስሙ። *ኢሳ፡ ፶፫፤ ፭፤ ፮፡፡ ኤር፡ ፴፩፤ ፴፬፡፡ ሕዝ፡ ፴፬፤ ፲፮፤ ዳን፡ ፱፤ ፳፬፡፡ ሆሴ፡ ፲፫፡ ፲፬፡፡ ሚክ፡ ፯፤ ፲፰፡፡

፵፬፤ ጴጥሮስም ፡ ይህነን ፡ ነገር፡ ሲናገር ፡ መንፈስ፡ ቅዱስ፡ ነገሩን፡ በሰሙት፡ ሁሉ፡ ላይ፡ ወረደ።

፵፭፤ ከግዝረት፡ ወገንም፡ የሚሆኑ፡ ከጴጥሮስ፡ ጋራ፡የመጡ፡ምእመናን፡ ሁሉ፡ ደነገጡ፡ የመንፈስ፡ ቅዱስ፡ጸጋ፡ በአሕዛብ፡ ላይ፡ ደግሞ፡ ስለ፡ ፈሰሰ።

፵፮፤ በሌላ፡*ቋንቋ፡ ሲናገሩ፡ ሰምተዋቸዋልና፡እግዚአብሔርንም ፡ ሲያከብሩ። *ምዕ፡ ፪፤ ፬፡፡ ማር፡ ፲፮፤ ፲፯፡፡

፵፯፤ የዚያን፡ ጊዜም፡ መለሰ፡ጴጥሮስ፡ አለም። በውኑ፡ማንም፡ ውኃ፡ይከለክላልን፡ እሌህ፡ እንዳይጠመቁ። መንፈስ፡ቅዱስን፡ የወሰዱ፡ እኛ፡ ደግሞ፡ እንደ፡ወሰድነ።

፵፰፤ በጌታ ፡ ስምም ፡ ይጠመቁ ፡ ዘንድ ፡ አዘዛቸው። የዚያን፡ጊዜ፡ *ለመኑት፡ ከርሳቸው፡ ዘንድ፡ አያሌ፡ቀን፡ ይቀመጥ፡ ዘንድ። *ዮሐ፡ ፬፤ ፵፡፡

ምዕራፍ፡ ፲፩፡

፩፡ ሐዋርያትም፡በይሁዳ፡የነበሩ፡ወንድሞችም፡ ሰሙ፡ አሕዛብ፡ ደግሞ፡ የእግዚአብሔርን፡ ነገር፡ እን ደ፡ ተቀበሉ።

፪፡ ጴጥሮስም፡ወደ፡ የሩሳሌም፡ በወጣ፡ጊዜ፡ *የግ ዝረት፡ሰዎች፡ተጣሉት፡እንደህ፡ሲሉ። *ምዕ ፲፡ ፵፭፡፡

፫፡ ወደልተገዘሩ፡ ሰዎች፡ገባህ፡ከርሳቸውም፡ጋራ፡ በላህ። ገላት፡ ፪፡ ፲፪፡፡

፬፡ ጴጥሮስም፡ ወሬውን፡ ሁሉ፡ ተከታትሎ፡ ያጫ ውታቸው፡ ጀመረ፡ እንደህም፡ አለ። ምዕ፡ ፲፡ ፲፡፡

፭፡ እኔ፡ በኢዮጴ፡ አገር፡ ነበርሁ ፡ ስጸልይ፡ በራእይ ም፡አየሁ፡ታላቅ፡ልብስ፡ከሰማይ፡ እንደ፡ ወረደ፡ እን ደ፡ ታላቅ፡ መጐናጸፊያ፡ ባራት፡ወገን፡ ታሥሮ፡ ወደኔ፡ መጣ።

፮፡ አስተውዬም፡ በተመለከትሁ፡ ጊዜ፡ የምድር፡ እንስሳ፡አየሁ፡ አራዊትም፡ ተንቀሳቃሽም፡ የሰማይ ም፡ ወፎች።

፯፡ የሚለኝንም ፡ ድምጽ፡ ሰማሁ። ተነሣ፡ ጴጥሮ ስ፡ ሆይ፡ አረድና፡ ብላ።

፰፡ አልሁም። አይሆንም፡ከቶ፡አቤቱ። አንዳች፡ር ኩስ፡የሚያስጸይፍም፡ወደ፡አፌ፡ገብቶ፡አላውቅምና።

፱፡ ድምጽም፡ከሰማይ፡ደግሞ፡ሁለተኛ፡መለሰል ኝ፡አለኝም። እግዚአብሔር፡ ያነጻውን፡ አንተ፡ አታር ክሰው።

፲፡ ይህም፡ሶስት፡ጊዜ፡ሆነ። ከዚያ፡ በኋላም፡ ሁሉ፡ ወደ፡ሰማይ፡ተሳበ።

፲፩፡ እነሆም፡በዚያች፡ሰዓት፡ሶስት፡ሰዎች፡ቆሙ፡ እኔ፡ ባለሁበት ፡ ቤት ። ከቂሣርያ ፡ ወደኔ ፡ ተልከው።

፲፪፡ መንፈስ፡ቅዱስም፡አለኝ፡ ከርሳቸው፡ጋራ፡ አ ሔድ፡ዘንድ፡በምንም፡ ሳልጠራጠር። ከኔም፡ጋራ፡መ ጡ፡እሌህ፡ስድስቱ፡ ወንድማማች። ወደዚያ፡ ሰው፡ ቤትም፡ ገባነ።

፲፫፡ ነገረነም፡ መልአኩን፡እንዳየ፡ በቤቱ፡ ቁሞ፡ሲ ለውም። ሰዎች፡ወደ፡ኢዮጴ፡ላክ፡ ሲሞንንም፡ ጴጥ ሮስ፡የሚባለውን፡ አስመጣ።

፲፬፡ እርሱ፡ ይነግርሃል፡አንተ፡ የምትድንበትን፡ ነገ ር፡ የቤትህም፡ ሰዎች፡ ሁሉ። ምዕ፡ ፲፡ ፯፡፡

፲፭፡ ለመናገርም፡ በጀመርሁ፡ ጊዜ፡መንፈስ፡ ቅዱ ስ፡ ወረደባቸው፡ በኛ፡ አስቀድሞ፡ እንደ፡ ወረደ። ምዕ፡ ፪፡ ፬፡፡

፲፮፡ የጌታንም፡ ነገር፡ አሰብሁ፡ እንደት፡ እንደለ። ዮሐንስ፡በውኃ፡ አጠመቀ፡እላንት፡ ግን፡ በመንፈስ፡ ቅዱስ፡ትጠመቃላችሁ። ምዕ፡ ፩፡ ፭፡፡ ማቴ፡ ፫፡ ፲፩፡፡

፲፯፡ እግዚአብሔርም፡ የጸጋን፡ አንድነት፡ከሰጣቸ ው፡ለኛ፡እንደ፡ ሰጠ፡ በጌታ፡ በየሱስ፡ ክርስቶስ፡ ባመ ንነ፡ ጊዜ። እኔ፡ማነኝ፡ እግዚአብሔርን፡ ለመከልከል፡ እችል፡ ዘንድ።

፲፰፡ ይህንንም ፡ በሰሙ ፡ ጊዜ፡ ዝማሉ ፡ እግዚአብ ሔርንም፡ አመሰገኑ፡ እንደህ፡ሲሉ። እንግዲህም፡እ ግዚአብሔር፡ ለአሕዛብ፡ ንስሐ፡ ሰጣቸው፡ ይድኑ፡ዘ ንድ።

፲፱፡ የተበተኑት፡ግን፡ በእስጢፋኖስ፡ ላይ፡ በተደረ ገው፡መከራ፡ወደ፡ፊንቄ፡ መጡ፡ ወደ፡ቆጵሮስም፡ወ ደ፡አንጾኪያም፡ ማንንም፡ነገሩን፡ አያስተምሩም፡ነበ ሩ፡ ለአይሁድ፡ ብቻ፡ እንጂ። ምዕ፡ ፰፡ ፩—፬፡፡

፳፡ ሌሎችም፡ ከርሳቸው፡ ሰዎች፡ ከቆጵሮስ፡ ወገ ን፡ነበሩ፡ከቂሬኔም። እርሳቸውም፡ ወደ፡አንጾኪያ፡በ ገቡ፡ጊዜ፡ አረማውያንን፡ አስተማሩ፡ የጌታን፡ የየሱ ስን፡ የምስራች፡ ሲነግሯቸው።

፳፩፡ የእግዚአብሔር፡እጅም፡ከርሳቸው፡ጋራ፡ነበ ር። ሰዎችም፡ቍጥራቸው፡ እጅግ፡ የሚሆን፡ ወደ፡ጌ ታ፡ተመለሱ። ምዕ፡ ፪፡ ፵፯፡፡

፳፪፡ ወሬያቸውም፡ በየሩሳሌም፡ባለው፡ ቤት፡ክ ርስቲያን፡ጆሮ፡ ተሰማ፡ በርናባስንም፡ ሰደዱት፡ ወደ፡ አንጾኪያ፡ ይሔድ፡ ዘንድ።

፳፫፡ በመጣም፡ጊዜ፡ የእግዚአብሔርንም፡ ጸጋ፡ባ የ፡ጊዜ፡ደስ፡አለው፡ ሁሉንም፡አጸናቸው፡ በጌታ፡ይኖ ሩ፡ ዘንድ፡ በጸና፡ በልባቸው፡ ፈቃድ።

ምዕ፡ ፲፫፡ ፵፫፡—፶፪፡፡

፳፬፡ጻድቅ፡ሰው፡ነበረና፡መንፈስ፡ቅዱስም፡*የመ ላበት፡ ሃይማኖትም ። እጅግ ፡ †ሰዎችም ፡ ለጌታ፡ ተ ጨመሩ። *ምዕ፡ ፯፡ ፭፡፡ †ምዕ፡ ፭፡ ፲፬፡፡

፳፭፡ በርናባስም፡ወደ፡ ጠርሲስ፡ ወጣ፡ *ሳውልን፡ ሊሻ። ባገኘውም፡ጊዜ፡ወደ፡አንጾኪያ፡ ይዞት፡ መጣ። *ምዕ፡ ፱፡ ፴፡፡

፳፮፡ አንድ፡ አመትም፡ በቤት፡ ክርስቲያን፡ ተሰበ ሰቡ፡ እጅግ፡ ሰዎችም፡ አስተማሩ ። *በአንጾኪያም፡ አስቀድሞ ፡ ደቀ፡ መዛሙርት ፡ ክርስቲያን ፡ ተባሉ። *ገላት፡ ፪፡ ፲፩፡፡

፳፯፡ በዚችም፡ ወራት፡ *ነቢያት፡ ከየሩሳሌም፡ ወ ደ፡ አንጾኪያ፡ ወረዱ። *ምዕ፡ ፲፫፡ ፩፡፡ ፲፭፡ ፴፪፡፡

፳፰፡ ከርሳቸውም፡አንዱ፡ተነሣ፡ስሙን፡አጋቦስ፡ የሚሉት፡በመንፈስ፡ ቅዱስም፡ተናገረ፡ታላቅ፡ ራብ፡ እንዲሆን፡በዓለም፡ ሁሉ። እርሱም፡ የሆነ፡ በአቅሎ ዲዮስ፡ ቄሣር፡ ዘመን። ምዕ፡ ፳፩፡ ፲፡፡

፳፱፡ ደቀ፡መዛሙርትም፡ *ፈቀዱ፡ከርሳቸው፡ኢ ያንዳንዱ፡ እንደ፡ ከብቱ፡ መጠን፡ ማገልገል፡ ይሰዱ፡ ዘንድ፡ በይሁዳ፡ላሉት፡ ወንድሞች። *ገላት፡ ፪፡ ፲፡፡

፴፡ ይህነንም፡አደረጉ፡ወደ፡ሽማግሎችም፡ ሰደዱ ት፡ *በበርናባስና፡ በሳውል፡ እጅ። *ምዕ፡ ፲፪፡ ፳፭፡፡

ምዕራፍ፡ ፲፪፡

፩፡ በዚያም፡ ዘመን፡ *ሄሮድስ፡ ንጉሥ፡እጁን፡ ባያ ሌ፡ሰዎች፡ ላይ፡ከቤተ፡ክርስቲያን፡ ጫነ፡ መከራ፡ሊያ ሰያቸው። *ምዕ፡ ፬፡ ፫፡፡

፪፡ ያዕቆብንም ፡ የዮሐንስን፡ ወንድም ፡ በሰይፍ፡ ገደለው።

፫፤ ያም፡አይሁድን፡ደስ፡እንዳሰኛቸው፡ባየ፡ ጊዜ፡ ጨመረበት፡ ጴጥሮስን፡ ሊይዝ፡ ደገመ። የፋሲካም፡ በዓል፡ ወራት፡ነበረ።

፬፤ በያዘውም፡ጊዜ፡ *በግዞት፡አስቀመጠው፡ ላራት፡ጭፍሮችም፡ አሳልፎ፡ ሰጠው፡ ይጠብቁት፡ ዘንድ፡ ከፋሲካ፡ በኋላ፡ ወደ፡ ሕዝብ ፡ ያወጣው ፡ ዘንድ ፡ ፈቀደ። *ም፡ ፲፯፡ ፳፬፡፡

፭፤ ጴጥሮስም፡ በግዞት፡ ይጠበቅ፡ ነበረ፡ ደሮ ፡ ግን፡ ጸሎት፡ ሁለጊዜ፡ በቤተ፡ ክርስቲያን፡ ወደ፡ እግዚአብሔር፡ ይሆን፡ ነበረ፡ ስለርሱ።

፮፤ ሄሮድስም፡ ወደርሳቸው፡ ያወጣው፡ ዘንድ፡ በወደደ፡ጊዜ፡ በዚያ፡ሌሊት፡ጴጥሮስ፡ተኝቶ፡ ነበር፡ በሁለት፡ወታደር፡መካከል፡ በሁለት፡ ሰንሰለት፡ ታሥሮ። ጠባቆችም ፡ በደጁ፡ ፊት፡ የግዞቱን፡ ቤት፡ ይጠብቁ፡ ነበር።

፯፤ እነሆም፡ የእግዚአብሔር፡ መልአክ፡ ወደርሱ፡ ቆመ፡ብርሃንም፡በቤቱ፡በራ። የጴጥሮስንም፡ ጎን፡ መታው፡ አስነሣውም፡ እንደህ፡ ሲል። ፈጥነህ ፡ ተነሣ። ሰንሰለቶቹም፡ ከጁ፡ ወደቁ። ም፡ ፭፡ ፲፱፡፡

፰፤ መልአኩም፡አለው። ታጠቅ፡ጫማህንም፡ልበስ። እንደሁም፡አደረገ። አለውም። ልብስን፡ ልበስና፡ ተከተለኝ።

፱፤ ጴጥሮስም ፡ ተከትሎት፡ ወጣ፡ በመልአኩም፡ የሚደረገው፡ ነገር፡ እውነት፡ እንደ፡ ሆነ፡ አላወቀም፡ ራእይ፡ የሚያይ፡ ይመስለው፡ ነበረ፡ እንጂ።

፲፤ የመጀመርያውንም ፡ ሁለተኛውንም ፡ ዘብ፡ ባለፉ፡ ጊዜ፡ ወደገር፡ ወደሚወስደው፡ ወደ ፡ ብረቱ፡ ደጅ፡ ደረሱ፡ በገዛጁ ፡ የተከፈተላቸው ። በወጡም፡አንዲንም፡ መንገድ፡በሔዱ፡ ጊዜ፡ የዚያን፡ ጊዜ፡ መልአኩ፡ ከርሱ፡ ራቀ።

፲፩፤ ጴጥሮስም፡ወደ፡ልቡ፡ ተመለሰ፡ አለም። አሁን፡ በውነት፡ አወቅሁ፡ እግዚአብሔር፡ መልአኩን፡እንደ፡ ላከ፡ ከሄሮድስም፡ እጅ፡የአይሁድ፡ወገንም፡ ካሰቡት፡ ሁሉ፡ እንደደነኝ።

፲፪፤ እውነት፡እንደ፡ ሆነም፡ ባወቀ፡ ጊዜ፡ ማርቆስ፡ ወደሚባለው፡ወደ፡*ዮሐንስ፡እናት፡ወደ፡ማርያም፡ ቤት፡መጣ፡እጅግ፡ሰዎች፡ ተከማችተውበት፡ ከነበሩት፡ ስፍራ፡ ሲጸልዩ። *ም፡ ፲፭፡ ፴፯፡፡

፲፫፤ ጴጥሮስም፡ የቤቱን፡ደጅ፡ በመታ፡ጊዜ፡ አንዲት፡ብላቴና፡ መጣች፡ ስምዋን፡ ሮደ፡ የሚልዋት፡ ትሰማ፡ዘንድ።

፲፬፤ የጴጥሮስንም፡ድምፅ፡ባወቀች፡ጊዜ፡ከደስታዋ፡ የተነሣ፡ አልከፈተችም፡ ተቀዳደመች፡ እንጂ፡ የምስራችም፡ነገረች፡ ጴጥሮስ፡ በደጅ፡ ቁሞ፡ እንዳለ።

፲፭፤ እርሳቸው፡ግን፡ አልዋት። ታብደለሽ። እርስዋም፡ነገርዋን፡በውነት፡አጸናች፡እርሱ፡ እንደ፡ሆነ። እርሳቸውም፡ አሉ። *መልአኩ፡ ይሆናል። *ሉቃ፡ ፳፬፡ ፴፯፡፡

፲፮፤ ጴጥሮስ፡ ግን ፡ ደጁን፡ ሲመታ ፡ ዘገየ። በከፈቱም፡ ባዩትም፡ ጊዜ፡ አደነቁ።

፲፯፤ እርሱ፡ግን፡በጁ፡ጠቀሳቸው፡ዝም፡እንዲሉ። አጫወታቸውም፡ እንዴት፡ እግዚአብሔር፡ ከግዞት፡ እንደወጣው፡አለም። ይህነን፡ ለያዕቆብ፡ ንገሩ፡ ለወንድሞችም። ወጥቶም፡ ወደ፡ ሌላ፡ስፍራ፡ ሔደ።

፲፰፤ ማልደም ፡ በሆነ ፡ ጊዜ፡ ፍጅት፡ ሆነ፡ በጭፍራው፡ መካከል፡ ጥቂት፡ አይደለውም፡ እንደህ፡ሲሉ። እንጃ፡ ጴጥሮስን፡ ምናገኘው። ም፡ ፭፡ ፳፩፡ ፳፪፡፡

፲፱፤ ሄሮድስም ፡ ባስፈለገው፡ ጊዜ፡ ባያገኘውም፡ ጠባቆችን፡ መረመረ፡ ሊገልዋቸውም፡ አዘዘ። ከይሁዳ ፡ አገርም ፡ ወደ፡ ቂሣርያ ፡ ወረደ፡ ከዚያም ፡ ተቀመጠ።

፳፤ ሄሮድስም፡በጢሮስና፡በሲዶና፡ ሰዎች፡ተቈጥቶ፡ነበረ። እርሳቸው፡ ግን፡ባንድ፡ወደርሱ፡ መጡ፡ብላስጦስንም፡ በንጉሡ ፡ ግዛት፡ የተሾመውን፡ እሺ፡ ባሰኙት፡ጊዜ፡ዕርቅ፡ፈለጉ። *ያገራቸው፡እህል፡ከንጉሡ፡ ግዛት፡ነበርና። *፩፡ ነገሥ፡ ፭፡ ፱፡ ፲፩፡፡ ሕዝ፡ ፳፯፡ ፲፯፡፡

፳፩፤ በተቈረጠም፡ቀን፡ሄሮድስ፡ የንጉሥ፡ልብስ፡ ለበሰ ፡ በዙፋንም፡ ተቀመጠ፡ የግልጽም፡ ነገር፡ ተናገራቸው።

፳፪፤ ሕዝቡም፡ጮሁ። የአምላክ፡ቃል፡ነው፡የሰውም፡ቃል፡ አይደለም። ሕዝ፡ ፳፰፡ ፪፡፡

፳፫፤ የዚያን፡ ጊዜም ፡ የእግዚአብሔር፡ መልአክ፡ ቀሠፈው፡ለእግዚአብሔር፡ *ምስጋና፡ ስላልሰጠ። ትልም፡ ፈላበትና፡ ሞተ። *ዳን፡ ፭፡ ፳፡፡

፳፬፤ የእግዚአብሔር፡ ነገር፡ ግን፡ ያድግ፡ ይበዛም፡ ነበረ። ም፡ ፮፡ ፯፡፡ ኢሳ፡ ፶፭፡ ፲፩፡፡

፳፭፤ በርናባስና፡ሳውል፡ግን፡ ከየሩሳሌም፡ ተመለሱ ፡ መልእክታቸውን ፡ *በፈጸሙ ፡ ጊዜ ። ከርሳቸውም፡ጋራ፡ ዮሐንስን፡ ወሰዱ፡ †ማርቆስ፡ የተባለውን። *ም፡ ፲፩፡ ፳፱፡፡ †ቆ፡ ፲፪፡፡ ም፡ ፲፭፡ ፴፯፡፡

## ምዕራፍ፡ ፲፫፤

፩፤ በአንጾኪያም ፡ ባለች፡ ቤተ፡ ክርስቲያን፡ *ነቢያትና፡መምህራን፡ነበሩ፡ ከርሳቸውም፡ በርናባስ፡ ስምዖንም፡ ኒጌር፡ የሚባለው። ሉክዮስም፡ የቂሬናው። ማናይንም፡ከሄሮድስ፡ካራተኛው፡ አለቃ፡ጋራ፡ ያደገው። ሳውልም። *ም፡ ፲፩፡ ፳፯፡፡ ፳፩፡ ፲፡፡

፪፤ እርሳቸውም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ሲያገለግሉ፡ ሲጾሙም፡መንፈስ፡ቅዱስ፡አለ። *በርናባስንና፡ ሳውልን፡ ለዩልኝ፡ ለጸራኋቸው፡ ስራ። *ም፡ ፱፡ ፲፭፡፡

፫፤ የዚያን ፡ ጊዜም፡ *ጾሙ፡ ጸለዩም ። እጃቸውንም፡ †በጫኑባቸው፡ ጊዜ፡ ሰደዱዋቸው። *ም፡ ፲፬፡ ፳፫፡፡ †ም፡ ፮፡ ፮፡፡

፬፤ እሌህም፡ ከመንፈስ፡ቅዱስ፡በተላኩ፡ ጊዜ፡ወደ፡ሴሌውቅያ፡ መጡ፡ ከዚያም፡ወደ፡ ቆጵሮስ፡ በመርከብ፡ ሰረሩ።

፭፤ ወደ፡ሰላሚስም፡በደረሱ፡ጊዜ፡በእግዚአብሔ

ር፡ ነገር፡ አስተማሩ፡ በአይሁድ፡ መስጊዶች። *ዮሐንስም፡ ከርሳቸው፡ ጋራ፡ ነበረ፡ ሲያገለግላቸው።
*ም፡ ፲፪፡ ፲፪፡ ፳፭።

፮፡ ደሴቱንም፡ ሁሉ፡ በዞሩ፡ ጊዜ፡ ወደ፡ ጳፉስ፡ መጡ። ከዚያም፡ አስማተኛ፡ ሰው፡ አስተኛም፡ ነቢይ፡ አገኙ፡ ከአይሁድ፡ ወገን፡ ስሙን፡ ባርየሱስ፡ የሚሉት።

፯፡ ከሰርጌዎስ፡ ጳውሎስ፡ ከሹሙ፡ ካስተዋይ፡ ሰው፡ ጋራ፡ የነበረ። ይህ፡ በርናባስንና፡ ሳውልን፡ አስመጣ፡ የእግዚአብሔርንም፡ ነገር፡ ሊሰማ፡ ለመነ።

፰፡ ኤሊማስም፡አስማተኛው፡ ስሙ፡እንደሁ፡ይተረጐማልና፡ ተቋቋማቸው፡ ሹሙን፡ ከሃይማኖቱ፡ ሊመልስ፡ ሲሻ። ፪፡ ጢሞ፡ ፫፡ ፰።

፱፡ ሳውል፡ግን፡ደግሞ፡ ጳውሎስ፡ የተባለው፡ መንፈስ፡ ቅዱስን፡ መላ፡ ዓይኑንም፡ ተክሎ፡ ተመለከተው።

፲፡ አለም።አንተ፡ ሽንገላ፡ የመላበት፡ ተንኰልም፡ ሁሉ፡ የሰይጣን፡ ልጅ፡ የጽድቅም፡ ሁሉ፡ ጸላት። አትተውምን፡የእግዚአብሔርን፡ መንገድ፡ የቀናችውን፡ ጠማማ፡ ማድረግ።

፲፩፡ አሁንም፡እነሆ፡ የእግዚአብሔር፡እጅ፡ባንተ፡ላይ፡ነው። ዕውርም፡ ሁን፡ ፀሐይም፡አትይ፡ እስከ፡ጊዜው። የዚያን፡ጊዜም፡ ጽጋግ፡ ወደቀችበት፡ ጨለማም። ይዞርም፡ ጀመረ፡ የሚመሩትንም፡ ለመነ።

፲፪፡ የዚያን፡ጊዜም፡ ሹሙ፡ የተደረገውን፡ ተአምራት፡ ባየ፡ ጊዜ፡ አመነ፡ ተገርሞ፡ ከእግዚአብሔር፡ ትምህርት፡ የተነሣ።

፲፫፡ ጳውሎስ፡ግን፡ ከርሱም፡ጋራ፡ የነበሩት፡ ከጳፉስ፡ በሔዱ፡ ጊዜ፡ ወደ፡ጵርጊያ፡መጡ፡ በጵምፌልያ፡ያለችው። ዮሐንስ፡ ግን፡ ተለያቸው፡ *ወደ፡ የሩሳሌምም፡ ተመለሰ። *ም፡ ፲፭፡ ፴፰።

፲፬፡ እርሳቸውም፡ ከጵርጊያ፡ አለፉ፡ ወደ፡ አንጾኪያም፡የጲሲድያ፡ወደምትሆን፡አገር፡መጡ።ወደ፡መስጊድም፡ በገቡ፡ ጊዜ፡ ቅዳሚ፡ ቀን፡ ተቀመጡ።

፲፭፡ ኦሪትም፡ ነቢያትም፡ ከተነበቡ፡ በኋላ፡ የመስጊድ፡ አለቆች፡ ወደርሳቸው፡ ላኩ፡ እንደዚህ፡ ሲሉ። እላንት፡ ሰዎች፡ ወንድሞች፡ የትምህርት፡ ነገር፡ እንደላችሁ፡ ለሕዝቡ፡ ይነገር፡ ዘንድ፡ የሚገባ፡ ተናገሩ።

፲፮፡ ጳውሎስም፡ተነሣ፡ በጁም፡ ጠቀሳቸው፡ አለም። እላንት፡ሰዎች፡ የእሥራኤል፡ ወገን፡ እግዚአብሔርንም፡ የምትፈሩ፡ ስሙ።

፲፯፡ የዚህ፡ የእሥራኤል፡ወገን፡ አምላክ፡ አባቶቻችንን፡መረጠ፡ *ሕዝቡንም፡ በተሰደደባት፡ በምሥር፡ አገር፡†ከፍ፡ከፍ፡አደረገው፡ከርስዋም፡አወጣቸው፡ በታላቅ፡ ክንድ። *ኢሳ፡ ፩፡ ፪።
†ዘፀአ፡ ፲፪፡ ፴፯፡ ፵፩።

፲፰፡ አርባ፡አመትም፡ ምሉ፡ በምድረ፡ በዳ፡ መገባቸው። ዘፀአ፡ ፲፮፡ ፴፭። ዘኍል፡ ፲፬፡ ፴፬።
ዘዳግ፡ ፩፡ ፴፩።

፲፱፡ *ሰባት፡ አሕዛብም፡ በከነዓን፡ አገር፡ ካጠፋ፡ በኋላ፡ ምድራቸውን፡ †በፀ፡ አካፈላቸው።
*ዘዳግ፡ ፯፡ ፩። †ኢያ፡ ፲፬፡ ፪።

፳፡ ከዚህም፡ በኋላ፡ ፈራጆች፡ ሰጣቸው፡ አራት፡ መቶ፡ካምሳ፡አመት፡የሚያህል፡እስከ፡ ነቢዩ፡እስከ፡ ሳሙኤል፡ዘመን፡ድረስ። መሳ፡ ፪፡ ፲፮። ፫፡ ፱።

፳፩፡ ከዚያም፡በኋላ፡ንጉሥ፡ለመኑ፡እግዚአብሔርም፡ ሳኦልን፡ ሰጣቸው፡ የቂስን፡ ልጅ፡ ከብንያም፡ ወገን፡ የሚሆንን፡ ሰው፡ አርባ፡ አመት።
፩፡ ሳሙ፡ ፲፡ ፳፩።

፳፪፡ እርሱንም፡ ካሻረው፡ በኋላ፡ ንጉሥ፡ አስነሣላቸው፡*ዳዊትን፡ የመሰከረለትን፡ ያለውንም። ዳዊትን፡የእሤይን፡ልጅ፡አገኘሁ፡እንደ፡ልቤ፡ያለ፡ ሰው፡ ፈቃዴን፡ሁሉ፡ የሚያደርግ።
*፩፡ ሳሙ፡ ፲፮፡ ፲፪፡ ፲፫።

፳፫፡ እግዚአብሔርም፡ከዚህ፡ *ዘር፡ እንደ፡ መሐላው፡ ለእሥራኤል፡ የሱስን፡ አስነሣ፡ መድኃኒት፡ አድርጎ። *ኢሳ፡ ፲፩፡ ፩።

፳፬፡ ዮሐንስም፡ አስቀድሞ፡ የምስራች፡ ተናገረ፡ በመምጣቱ፡ፊት፡*በንስሐ፡ጥምቀት፡ለእሥራኤል፡ ወገን፡ ሁሉ። *ማቴ፡ ፫፡ ፩።

፳፭፡ ዮሐንስም፡ ሩጫውን፡ በፈጸመ፡ ጊዜ፡ አለ። ምንድር፡ ነው፡ የመሰላችሁ፡ እኔ፡ እንደ፡ ሆንሁ። ያ፡ እኔ፡አይደለሁም።ነገር፡ግን፡እነሆ፡ ከኔ፡በኋላ፡ይመጣል፡ የማይገባኝ፡ የግሩን፡ ጫማ፡ እፈታ፡ ዘንድ።
ዮሐ፡ ፩፡ ፳። ማር፡ ፩፡ ፮። ሉቃ፡ ፫፡ ፲፮።

፳፮፡ እላንት፡ ወንድማማች፡ ሰዎች። የአብርሃም፡ ዘር፡ልጆች፡ ከላንትም፡ እግዚአብሔርን፡ የምትፈሩ፡ ሁሉ። ለላንት፡ ተላከ፡ የዚህ፡ መድኃኒት፡ ነገር።
ቈ፡ ፵፮።

፳፯፡ በየሩሳሌም፡ የሚኖሩ፡ ሰዎች፡ ግን፡ አለቆቻቸውም፡ ይህነን፡ *ባያውቁ፡ የነቢያትንም፡ ድምጽ፡ ቅዳሚ፡ ቅዳሚ፡ የሚነበበውን፡ ፈጸሙት፡ ባፈረዱበት፡ ጊዜ። *ዮሐ፡ ፲፮፡ ፫።

፳፰፡ ለሞትም፡የምታደርስ፡አንዲት፡ ሰንኳ፡ ምክንያት፡ባያገኙበት፡ ወደ፡ ጲላጦስ፡ *ለመኑ፡ ይገድሉው፡ ዘንድ። *ማቴ፡ ፳፯፡ ፳፪፡ ፳፫።

፳፱፡ ስለርሱ፡ የተጻፈውንም፡ ሁሉ፡ በፈጸሙ፡ ጊዜ፡*ከንጨት፡አወረዱት፡ በመቃብርም፡ ጨመሩት።
*ማቴ፡ ፳፯፡ ፶፱።

፴፡ እግዚአብሔር፡ ግን፡ ከሙታን፡ አስነሣው።
ም፡ ፫፡ ፲፭።

፴፩፡ ብዙ፡ቀንም፡ ተገለጠ፡ከገሊላ፡ ወደ፡ የሩሳሌም፡ ከርሱ፡ ጋራ፡ ለወጡ። እርሳቸውም፡ ምስክሮቹ፡ ናቸው፡ በሕዝብ፡ ዘንድ። ም፡ ፩፡ ፫።

፴፪፡ እኛም፡የምስራች፡ እንነግራችኋለን፡ላባቶቻችን፡ በሆነው፡ ተስፋ። ቈ፡ ፳፫።

፴፫፡ እግዚአብሔር፡ ይህነን፡ ለኛ፡ ለልጆቻቸው፡ ፈጽሞታልና፡ የሱስን፡ ባስነሣ፡ ጊዜ። እንደ፡ ተጻፈ፡ ደ

ግሞ፡ በሁለተኛው፡ መዝሙር፡ እንዲህ፡ ሲል። *አን
ተ፡ ልጄ፡ ነህ፡ እኔ፡ ዛሬ፡ ወለድሁህ። *መዝ፡ ፪፡ ፯።
፴፬፡ እርሱም፡ ከሙታን፡ አስነሥቶታልና፡ ወደ፡
ጥፋትም፡ አይመለስምና፡ ደግሞ፡ እንዲሁ፡ አለ። *የ
ዳዊትን፡ የታመነችውን፡ ጸጋ፡ እሰጣችኋለሁ።
*ኢሳ፡ ፶፭።
፴፭፡ ስለዚህም፡ በሌላው፡ ስፍራ፡ ደግሞ፡ ይላል።
ወዳጅህን፡ አተውም፡ ጥፋት፡ ያይ፡ ዘንድ።
መዝ፡ ፲፮፡ ፲።
፴፮፡ ዳዊትም፡ የእግዚአብሔርን፡ ፈቃድ፡ በዘመ
ኑ፡ካገለገለ፡በኋላ፡ አንቀላፋ፡ ወደ፡ አባቶቹም፡ ሔደ፡ ጥ
ፋትም፡ አየ። ም፡ ፪፡ ፳፱።
፴፯፡ ይህ፡ግን፡እግዚአብሔር፡ያስነሣው፡ ጥፋት፡
አላየም።
፴፰፡ አሁንም፡ በእንት፡ዘንድ፡ የታወቀ፡ ይሁን፡እ
ላንት፡ ሰዎች፡ ወንድማማች፡ በዚህ፡ እንዲነገርላች
ሁ፡ የኃጢአት፡ ስርየት።
፴፱፡ ከኃጢአትም፡ ሁሉ፡ በሙሴ፡ ኦሪት፡ ከርስ
ዋ፡ ትነጹ፡ ዘንድ፡ የማትችሉ። በዚህ፡ የሚያምን፡ ሁ
ሉ፡ይነጻል። ሮሜ፡ ፲፡ ፬።
፵፡ አሁንም፡ተጠንቀቁ፡እንዳይመጣባችሁ፡ *በነ
ቢያት፡ የተባለው። *እንባ፡ ፩፡ ፭።
፵፩፡ እዩ፡እላንት፡ቸልተኞች፡ተደነቁም፡ ጥፉም።
እኔ፡ በዘመናችሁ፡ ስራ፡ እሰራለሁና፡ የማታምኑትን፡
ማንም፡ ቅሉ፡ ቢነግራችሁ።
፵፪፡ እርሳቸውም፡ከአይሁድ፡መስጊድ፡ሲወጡ፡
ለመንዋቸው፡አሕዛብ፡በሚመጣው፡ ቅዳሜ፡ ይህነ
ን፡ነገር፡ ይነግርዋቸው፡ ዘንድ።
፵፫፡ ጉባዔውም፡ በተፈታ፡ ጊዜ፡ ከአይሁድ፡ እጅ
ግ፡ ሰዎች፡ስደተኞችም፡ ለእግዚአብሔር፡ የሚገዙ፡
ጳውሎስንና፡ በርናባስን፡ ተከተሉ። የነገርዋቸው፡ እ
ሺ፡ያሰኝዋቸውም፡ በእግዚአብሔር፡ *ጸጋ፡ ይጸኑ፡ ዘ
ንድ። *ም፡ ፲፩፡ ፳፫።
፵፬፡ በሁለተኛውም፡ቅዳሜ፡ ተሰበሰቡ፡ ያገሩ፡ሰ
ዎች፡ ሁሉ፡የእግዚአብሔርን፡ ነገር፡ ይሰሙ፡ ዘንድ።
፵፭፡ አይሁድም፡ የተሰበሰቡትን፡ ባዩ፡ ጊዜ፡ ቅና
ት፡ መላባቸው። የጳውሎስንም፡ ነገር፡ አፈረሱ፡ ኢየ
ተቃወሙ፡ ኢየተሳደቡም። ቆ፡ ፱፡ ም፡ ፲፬፡ ፪።
፵፮፡ ጳውሎስና፡በርናባስም፡አጽንተው፡ ተናገሩ፡
አሉም። *አስቀድመን፡የእግዚአብሔርን፡ነገር፡ለላን
ት፡እንነግር፡ ዘንድ፡ይገባል። ነገር፡ግን፡ብትገፉት፡ በነፍ
ሳችሁም፡ብትፈርዲ፡ የዘላለም፡ ሕይወት፡ እንደይገ
ባችሁ፡ እነሆ፡ ወደ፡ አሕዛብ፡ እንመለሳለን።
*ም፡ ፫፡ ፳፮። ማቴ፡ ፲፡ ፮።
፵፯፡ እግዚአብሔር፡ እንዲሁ፡አዞናልና፡እንዲህ፡
ሲል። *ለአሕዛብን፡ብርሃን፡ አደረግሁህ፡መድኃኒት፡
ትሆን፡ ዘንድ፡ እስከ፡ ምድር፡ ዳርቻ፡ ድረስ።
*ኢሳ፡ ፵፱፡ ፮።
፵፰፡ አሕዛብም፡ በሰሙ፡ ጊዜ፡ ደሳላቸው፡ የእግ
ዚአብሔርንም፡ ነገር፡ አመሰገኑ። ለዘላለም፡ ሕይወ
ትም፡ *የተዘጋጁ፡ ሁሉ፡ አመኑ። *ሮሜ፡ ፰፡ ፳፱።
፵፱፡ የእግዚአብሔርም፡ ነገር፡ በዚያች፡ አገር፡ ሁ
ሉ፡ ወጣ።
፶፡ አይሁድ፡ ግን፡የሚገዙትን፡ የሚከብሩትንም፡
ሴቶች፡ አወኩ፡ ያገሩንም፡ አለቆች። ስደትም፡ አስነ
ሡ፡ በጳውሎስና፡ በበርናባስ፡ ላይ፡ ካገራቸውም፡ አ
ወጥዋቸው።
፶፩፡ እርሳቸው፡ ግን፡ የግራቸውን፡ ትቢያ፡ አረገፉ
ባቸው፡ ወደ፡ ኢቆንዮምም፡ መጡ። ም፡ ፲፰፡ ፮።
ማቴ፡ ፲፡ ፲፬።
፶፪፡ ደቀ፡ መዛሙርትም፡ ደስታን፡ መንፈስ፡ ቅ
ዱስንም፡ መሉ።

ምዕራፍ፡ ፲፬፡

፩፡ በኢቆኒዮምም፡ ሆነ፡ ወደ፡ አይሁድ፡ መስጊድ፡
ደግሞ፡ ገቡ፡ እንዲሁም፡ ተናገሩ፡ ብዙ፡ ሰዎች፡ እስ
ኪያምኑ፡ ድረስ፡ ከአይሁድ፡ ከአረማውያንም።
፪፡ ያላመኑ፡ አይሁድ፡ ግን፡ የአሕዛብን፡ ልብ፡ አስ
ነሡ፡ አስከፉም፡ በወንድሞች፡ ላይ። ም፡ ፲፫፡ ፵፭።
፫፡ እርሳቸው፡ ግን፡ ከዚያ፡ረጅም፡ዘመን፡ ተቀመ
ጡ፡ በእግዚአብሔር፡ ሲጋደሉ፡ ለጸጋው፡ ነገር፡ የመስ
ከረ፡ ተአምራትም፡ ድንቅም፡ በጃቸው፡ ይሆን፡ ዘን
ድ፡ የሰጠ። ም፡ ፲፱፡ ፲፩። ዕብ፡ ፪፡ ፬።
፬፡ ያገሩም፡ ሰዎች፡ተከፈሉ። እኩሌቶቹም፡ ከአ
ይሁድ፡ ሆኑ፡ እኩሌቶቹም፡ ከሐዋርያት፡ ጋራ።
፭፡ የአሕዛብና፡ የአይሁድም፡ መነሣት፡ በሆነ፡ ጊ
ዜ፡ ካለቆቻቸው፡ ጋራ፡ ያጉሰቍልዋቸው፡ ይወግርዋ
ቸውም፡ ዘንድ። ቆ፡ ፲፱፡ ፪። ፩፡ ጢሞ፡ ፫፡ ፲፩።
፮፡ ያነን፡ ባወቁ፡ ጊዜ፡ ወደ፡ ሊቃኦኒያ፡ አገር፡ ኩብ
ለሉ፡ ወደ፡ ልስጥራ፡ ወደ፡ ደርቤም፡ ባጠገብዋም፡ ወ
ዳለቸው፡ አገር።
፯፡ ከዚያም፡ የምስራች፡ ይነገሩ፡ ነበር።
ም፡ ፲፩፡ ፲፱፡ ፳።
፰፡ በልስጥራም፡ አንድ፡ ሰው፡ ነበር፡ ለግሩ፡ ኃይል፡
የሌለው፡ ተቀምጦ። አንካሳ፡ ከናቱ፡ ማሕፀን፡ጀም
ር፡ ከቶም፡ አይሔድም፡ ነበር። ም፡ ፫፡ ፪።
፱፡ ይህ፡ ሰማ፡ ጳውሎስ፡ሲናገር። እርሱም፡ ዓይኑ
ን፡ ተክሎ፡ በተመለከተው፡ባየም፡ጊዜ፡ *ሊድማኖት
እንዳለው፡ ይድን፡ ዘንድ። ማቴ፡ ፱፡ ፳፰።
፲፡ በታላቅ፡ ቃል፡ አለው። በግርህ፡ቀንተህ፡ ቁም።
ተነሥቶም፡ ሔደ።
፲፩፡ አሕዛብም፡ ጳውሎስ፡ ያደረገውን፡ ባዩ፡ ጊዜ፡
ድምጻቸውን፡ ከፍ፡ ከፍ፡ አደረጉ፡ በሊቃኦኒያ፡ ቋን
ቋ፡ ሲሉ። አማልክት፡ ሰዎች፡ መሰሉ፡ ወደኛም፡ ወ
ረዱ። ም፡ ፳፰፡ ፮።
፲፪፡ በርናባስንም፡ ድያ፡ አሉት፡ ጳውሎስንም፡ ሄ
ርሜን። እርሱ፡ ነውና፡ ነገሩን፡ የሰራ።

፲፫፡ የድያ፡ ካህን፡ ግን፡ ባገራቸው፡ ፊት፡ የነበረ፡ በ
ሮችና፡ አክሊሎች፡ ወደ፡ ደጅ፡ አመጣ፡ ሊሠዋላቸው
ም፡ ወደደ፡ ከሰዎች፡ ጋራ።

፲፬፡ ሐዋርያትም፡ ጳውሎስና፡ በርናባስ፡ ይህነን፡
በሰሙ፡ ጊዜ፡ ልብሳቸውን፡ ቀደዱ፡ ወደ፡ ሕዝቡም፡
ቀልጥፈው፡ ሮጡ።

፲፭፡ ኢየጮሁ፡ ኢያሉም። እላንት፡ሰዎች፡ለምን፡
ይህነን፡ ትሰራላችሁ። እኛም፡ እንደላንት፡ ሰዎች፡
ነን፡ በድካም፡ የተካከልናችሁ። እናስተምራችሁማ
ለን፡ ትመለሱ፡ ዘንድ፡ ከዚህ፡ ከንቱ፡ ወደ፡ ሕያው፡
እግዚአብሔር፡ ሰማይን፡ ምድርንም፡ ባሕርንም፡ ዓ
ለምንም፡ ሁሉ፡ በርሳቸውም፡ ያለውን፡ የፈጠረ።
ም፡ ፲፡ ፳፮፡፡

፲፮፡ ባለፈው፡ ትውልድ፡ አሕዛብን፡ ሁሉ፡ የተወ፡
በመንገዳቸው፡ ይሔዱ፡ ዘንድ። ም፡ ፲፯፡ ፴፡፡

፲፯፡ ምንስ፡እርሱ፡ራሱን፡ያለ፡ ምስክር፡ያልተው፡
ለኛ፡ በጎ፡ ሲያደርግ፡ ከሰማይም፡ ዝናም፡ ሲሰጠን፡
ፍሬ፡ የሚሆንበትንም፡ ጊዜ። ልባችንንም፡ መብልና፡
ደስታ፡ ሲመላው። መዝ፡ ፻፵፯፡ ፰፡፡ ኤር፡ ፭፡ ፳፬፡፡

፲፰፡ ይህነንም፡ ብለው፡ የግድ፡ አሕዛብን፡ አስተ
ውዋቸው፡ እንዳይሠዉላቸው።

፲፱፡ አይሁድ፡ ግን፡ ከአንጾክያ፡ ከኢቆኒዮምም፡
መጡ፡ አሕዛብንም፡ እሺ፡ አሰኝዋቸው፡ ጳውሎስን
ም፡ *ወገሩት፡ ካገር፡ ወደ፡ሜዳም፡ ጐተቱት፡ የሞተ
ም፡ መስላቸው። *፪፡ ቆሮ፡ ፲፩፡ ፳፭፡፡
፪፡ ጢሞ፡ ፫፡ ፲፩፡፡

፳፡ ደቀ፡ መዛሙርት፡ ግን፡ ከበውት፡ ሳሉ፡ ተነሥ
ቶ፡ ወደገር፡ ገባ፡ በነገውም፡ ወደ፡ ደርቤ፡ ወጣ፡ ከበር
ናባስ፡ ጋራ።

፳፩፡ በዚያችም፡ አገር፡ ባስተማሩ፡ ጊዜ፡ እጅግ፡
ሰዎችም፡ደቀ፡ መዛሙርት፡ ባደረጉ፡ ጊዜ፡ ወደ፡ ልስ
ጥራ፡ ተመለሱ፡ ወደ፡ አቆኒዮምም፡ ወደ፡ አንጾክ
ያም።

፳፪፡ የደቀ፡ መዛሙርትንም፡ ልብ፡ ያጸኑ፡ ይለም
ኑዋቸውም፡ ነበረ፡ በሃይማኖት፡ ይጸኑ፡ ዘንድ፡እንደ
ህ፡ ሲሉ። በብዙ፡ መከራ፡ ይገባናል፡ ወደ፡ እግዚአብ
ሔር፡ መንግሥት፡ እንገባ፡ ዘንድ። ም፡ ፲፩፡ ፳፫፡፡
፩፡ ተሰ፡ ፫፡ ፫፡፡

፳፫፡ ሽማግሎችም፡መረጡ፡ ለርሳቸው፡ በኢየማ
ኅበሩ፡ ሁሉ። በጾምም፡ ጸለዩላቸው፡ ለእግዚአብሔ
ርም፡ ላመኑበት፡ አደራ፡ ሰጥዋቸው። ም፡ ፲፫፡ ፫፡፡

፳፬፡ በጲሲድያም፡ በዞሩ፡ ጊዜ፡ከዚያ፡ ወደ፡ ጵም
ፊልያ፡ መጡ።

፳፭፡ በጰርጊያም፡ የእግዚአብሔርን፡ ነገር፡ ከተና
ገሩ፡ በኋላ፡ ወደ፡ አጠልያ፡ ወረዱ።

፳፮፡ ከዚያም፡ ወደ፡ አንጾክያ፡ በባሕር፡ ሰረሩ።
ለእግዚአብሔርን፡ ጸጋ፡ አስቀድሞ፡ አደራ፡ ወደ፡ ተ
ሰጡበት፡ ስፍራ፡ ለፈጸሙት፡ ስራ። ም፡ ፲፫፡ ፩፡ ፪፡፡

፳፯፡ በመጡም፡ ጊዜ፡ የቤተ፡ ክርስቲያንንም፡ ሰ
ዎች፡ ሁሉ፡ በሰበሰቡ፡ ጊዜ፡ እግዚአብሔር፡ ከርሳቸ
ው፡ ጋራ፡ ያደረገውን፡ ነገር፡ ሁሉ፡ነገሩ፡ ለአሕዛብም፡
የሃይማኖትም፡*ደጅ፡እንደ፡ከፈተ። *፩፡ቆሮ፡፲፮፡፱፡፡

፳፰፡ ከዚያም፡ አያሌ፡ ቀን፡ ተቀመጡ፡ ከደቀ፡
መዛሙርት፡ ጋራ።

ምዕራፍ፡ ፲፭፡

፩፡ ሰዎችም፡ ከአይሁደ፡ መጡ፡ ወንድሞችንም፡
አስተማሩ፡ እንደህ፡ ሲሉ። እንደ፡ ሙሴ፡ ሥርዓት፡
ካልተዘራችሁ፡ አትችሉም፡ ትድኑ፡ ዘንድ።
ገላ፡ ፭፡ ፪፡፡

፪፡ ጽልም፡ ክርክርም፡ ለጳውሎስና፡ ለበርናባስ፡
ከርሳቸው፡ ጋራ፡ ጥቂት፡ ያይደለ፡ በሆነ፡ ጊዜ፡ ጳውሎ
ስና፡ በርናባስ፡ ከርሳቸውም፡ ሌሎች፡ ሰዎች፡ ወደ፡
የሩሳሌም፡ ይሔዱ፡ ዘንድ፡ አዘዙ፡ ወደ፡ ሐዋርያት፡
ወደ፡ ሽማግሎችም፡ ስለዚህ፡ ክርክር። ም፡ ፲፩፡ ፴፡፡
ገላ፡ ፪፡ ፩፡፡

፫፡ እርሳቸውም፡ ከጉባዔው፡ ተሸኝተው፡ ወደ፡ ፊ
ንቂ፡ ወደ፡ ሰማርያም፡ ሔዱ፡ የአሕዛብንም፡ መመ
ለስ፡ ይነግርዋቸው፡ነበረ፡ ታላቅ፡ ደስታም፡አደረጉ፡ ለ
ወንድሞች፡ ሁሉ።

፬፡ ወደ፡ የሩሳሌምም፡ በደረሱ፡ጊዜ፡ ተቀበልዋቸ
ው፡ ቤተ፡ ክርስቲያኑ፡ ሁሉ፡ ሐዋርያትም፡ ሽማግሎ
ችም። እግዚአብሔርም፡ ባደረገው፡ሁሉ፡ከርሳቸው፡
ጋራ፡ አጫወትዋቸው። ም፡ ፲፬፡ ፳፯፡፡

፭፡ ሰዎችም፡ ተነሡ፡ ከፈሪሳውያን፡ወገን፡ያመኑ፡
እንደህ፡ ሲሉ። ይገባል፡ ትገዝርዋቸው፡ ዘንድ፡ ታዝ
ዋቸውም፡ ዘንድ፡ የሙሴን፡ ሕግ፡ እንዲጠብቁ።

፮፡ ሐዋርያትም፡ ሽማግሎችም፡ ተሰበሰቡ፡ ይህነ
ን፡ ነገር፡ ያዩ፡ ዘንድ።

፯፡ እጅግም፡ ክርክር፡ በሆነ፡ ጊዜ፡ ጴጥሮስ፡ ተነሣ፡
አላቸውም። እላንት፡ ወንድሞች፡ ሰዎች። እላንት፡
ታውቃላችሁ፡ ባለፈው፡ዘመን፡እግዚአብሔር፡ ከኛ፡
እንደ፡ መረጠ፡ አሕዛብ፡ ካፌ፡ የወንጌል፡ ነገር፡ ይሰ
ሙ፡ ዘንድ፡ ያምኑም፡ ዘንድ። ም፡ ፲፩፡ ፲፪፡፡

፰፡ ልብንም፡ የሚያውቅ፡ አምላክ፡ መሰከረላቸ
ው፡ መንፈስ፡ ቅዱስን፡ በሰጣቸው፡ ጊዜ፡ ለኛ፡ እንደ፡
ሰጠን፡ ደግሞ።

፱፡ በርሳቸውና፡ በኛም፡ መካከል፡ አንዳች፡ አልለ
የም፡ ልባቸውንም፡ በሃይማኖት፡ አነጻው።
ም፡ ፲፡ ፵፬፡፡

፲፡ አሁንም፡ ለምን፡ እግዚአብሔርን፡ ትፈታተና
ላችሁ፡ ቀምበርስ፡ ትጭናላችሁ፡ በደቀ፡ መዛሙርት፡
ጫንቃ፡ ላይ፡ አባቶቻችን፡ እኛም፡ እንሸከመው፡ ዘን
ድ፡ ያልቻልነ። ገላ፡ ፫፡ ፲፡፡ ፭፡ ፩፡፡

፲፩፡ ነገር፡ ግን፡ በጌታ፡ በየሱስ፡ ክርስቶስ፡ ጸጋ፡ እን
ድን፡ ዘንድ፡ እናምናለን፡ እንደለዚያ። ገላ፡ ፪፡ ፲፮፡፡
ኤፌ፡ ፪፡ ፬፡—፲፡፡

፲፪፡ ሰዎችም፡ ሁሉ፡ ዝም፡ አሉ፡ ጳውሎስና፡ በርና

ባስም፡ተአምራቱን፡ ቢያሚውቱ፡ሰሙ፡ድንቁንም፡ እግዚአብሔር፡ በጀቸው፡ በአሕዛብ፡ ያደረገውን።

፲፫፡ እርሳቸውም፡ ዝም፡ ካሉ፡ በኋላ፡ መለሰ፡ ያዕቆብ፡ እንዲህ፡ ቢል። አላንት፡ ሰዎች፡ ወንድሞች፡ ስሙኝ። ም፡ ፳፩፡ ፲፰።

፲፬፡ ስምዖን፡ ተናግርዋልና፡እግዚአብሔር፡ አስቀድሞ፡ እንዴት፡እንደ፡ ጐበኘ፡ ከአሕዛብ፡ ወገን፡ ይወስድ፡ ዘንድ፡ ለስሙ።

፲፭፡ ይህም፡ ለነቢያት፡ ቃል፡ ይስማማል፡ እንደ፡ ተጻፈ።

፲፮፡ ከዚህ፡ በኋላ፡ እመለሳለሁ፡ የዳዊትንም፡ ጎጆ፡ የወደቀውን፡ እሰራለሁ፡ የፈረሰውንም፡ ተመልሼ፡አጸናለሁ፡አቀመዋለሁም። ዓሞ፡ ፱፡ ፲፩፡ ፲፪።

፲፯፡ የቀሩቱ፡ ሰዎች፡ እግዚአብሔርን፡ ይፈልጉ፡ ዘንድ፡ አሕዛብም፡ሁሉ፡ስሜ፡ በርሳቸው፡የተጸራው። ይህነን፡ ሁሉ፡ የሚያደርግ፡ እግዚአብሔር፡ አለ።

፲፰፡ ለእግዚአብሔር፡ ስራው፡ሁሉ፡የታወቀ፡ነው፡ ከጥንት፡ ጀምር።

፲፱፡ ስለዚህም፡ እኔ፡ እፈርዳለሁ፡ ከአሕዛብ፡ ወደ፡እግዚአብሔር፡ የተመለሱትን፡ እንዳታደክሙ።

፳፡ ነገር፡ግን፡እንላክባቸው፡ከጣዖታት፡ ርኩሰቱ፡ ይርቁ፡ ዘንድ፡ ከዝሙትም፡ ከታነቀም፡ *ከደምም።

*ዘፍ፡ ፱፡ ፬። ዘሌዋ፡ ፫፡ ፲፯።

፳፩፡ ለሙሴ፡ ከቀደመው፡ ትውልድ፡ ጀምር፡ ሰዎች፡ ነበሩትና፡ ቅዳሜ፡ ቅዳሜ፡ ባገሩ፡ ሁሉ፡በየመስጊዱ፡ የሚያነቡት። ም፡ ፲፫፡ ፲፭።

፳፪፡ የዚያን፡ ጊዜም፡ ሐዋርያት፡ ሽማግሎችም፡ ከቤተ፡ ክርስቲያኑ፡ ሁሉ፡ ጋራ፡ አዩ፡ በጎ፡ እንደሆን፡ ከርሳቸው፡ ሰዎችን፡ ይመርጡ፡ ዘንድ፡ ወደ፡ አንጾክያም፡ ይሰዱ፡ ዘንድ፡ ከጳውሎስና፡ ከበርናባስ፡ ጋራ። እርሳቸውም፡ ይሁዳ፡ በርሰባስ፡የተባለው፡ሲላስም፡ ከወንድሞች፡ መርች፡ የነበሩ።

፳፫፡ በጀቸውም፡ይህነን፡ነገር፡ ጻፉ። ከሐዋርያት፡ ከሽማግሎችም፡ ከወንድሞችም፡ ወደ፡ወንድሞች፡ ከአሕዛብ፡ ወገን፡ በአንጾክያ፡ በሻምም፡ በቂልቂያም፡ ደስ፡ይበላችሁ።

፳፬፡ ከኛ፡ ሰዎች፡ *ወጥተው፡ እንደወኳችሁ፡ ልባችሁንም፡ በነገራቸው፡ እንደ፡ ገለበጡት፡ ሰምተናልና። እንዲህ፡ ሲሉ። ትገዘሩ፡ ዘንድ፡ ኦሪትንም፡ ትጠብቁ፡ ዘንድ፡ ይገባችኋል። እኛ፡ ያላዘዝናቸውን።

*ም፡ ፳፡ ፴። ገላት፡ ፪፡ ፬።

፳፭፡ አየነ፡ ባንድ፡ በተሰበሰብነ፡ ጊዜ፡ ሰዎች፡ እንመርጥ፡ ዘንድ፡ ወደላንት፡የምንሰዳቸው፡ ከወዳጆቻችን፡ ከበርናባስና፡ ከጳውሎስ፡ ጋራ።

፳፮፡ ነፍሳቸውን፡ የለወጡ፡ ሰዎች፡ ስለ፡ ጌታችን፡ ስለ፡ የሱስ፡ ክርስቶስ፡ ስም።

፳፯፡ ይሁዳንና፡ ሲላስንም፡ ላክነ፡ እርሳቸውም፡ ደግሞ፡ ባፋቸው፡ ይህነን፡ ነገር፡ ይነግርዋችኋል።

፳፰፡ መንፈስ፡ቅዱስ፡አይትዋልና፡ እኛም፡ አይተናልና፡ ትርፍ፡ ሸክም፡እንደንጭንባችሁ፡ከዚሁ፡ከሚገባችሁ፡ ሕግ፡ በቀር።

፳፱፡ ለጣዖት፡ ከተሠዋ፡ መበል፡ ትርቁ፡ ዘንድ፡ ከደምም፡ ከታነቀም፡ ከዝሙትም። ከዚህ፡ ራሳችሁን፡ ከጠበቃችሁ፡መልካም፡ታደርጋላችሁ። ጤና፡ ይስጣችሁ።

፴፡ እርሳቸውም፡ በተሰናበቱ፡ ጊዜ፡ ወደ፡ አንጾክያ፡ መጡ። ሕዝቡንም፡ ሁሉ፡ ሰብሰበው፡መልእክቱን፡ ሰጥዋቸው።

፴፩፡ *ባነበቡትም፡ ጊዜ፡ ደሳላቸው፡ ልባቸውም፡ ጸና። *ም፡ ፲፫፡ ፵፯።

፴፪፡ ይሁዳና፡ ሲላስ፡ ግን፡ *ነቢያት፡ ነበሩና፡ ወንድሞችን፡ በጅግ፡ ነገር፡ ደስ፡ አሰኙዋቸው፡ አጸንዋቸውም። *ም፡ ፲፩፡ ፳፯። ፲፫፡ ፩።

፴፫፡ ከርሳቸውም፡ ዘንድ፡ አያሌ፡ ቀን፡ በተቀመጡ፡ ጊዜ፡ ከወንድሞች፡ ወደ፡ ሐዋርያት፡ በደህና፡ ተሰናብተው፡ ሔዱ።

፴፬፡ ሲላስ፡ ግን፡ ወደደ፡ ከዚያ፡ ይቀመጥ፡ዘንድ።

፴፭፡ ጳውሎስና፡ ባርናባስም፡ በአንጾክያ፡ ተቀመጡ፡ ያስተምሩም፡ የመስራችም፡ ይነግሩ፡ ነበሩ፡ በእግዚአብሔር፡ ነገር፡ ከሌሎች፡ ደግሞ፡ ከብዙ፡ ሰዎች፡ ጋራ።

፴፮፡ ከብዙ፡ ቀንም፡ በኋላ፡ ጳውሎስ፡ በርናባስን፡ አለው፡ ና፡ እንመለስ፡ ወንድሞቻችንን፡ እንጐብኛቸው፡ የእግዚአብሔርን፡ ነገር፡ባስተማርነባት፡አገር፡ ሁሉ፡ እንዴት፡ናቸው። ፩፡ ተሰ፡ ፫፡ ፭።

፴፯፡ ባርናባስን፡ ወደደ፡ ከርሳቸው፡ ጋራ፡ ዮሐንስን፡ይወስድ፡ ዘንድ፡ ማርቆስ፡ የተባለውን።

ም፡ ፲፪፡ ፲፪፡ ፳፭።

፴፰፡ ጳውሎስ፡ ግን፡ አልወደደም፡ይህነን፡ከርሳቸው፡ ጋራ፡ ሊወስደ፡ ከርሳቸውም፡ ከጵምፊልያ፡ የተለየውን፡ ከርሳቸውም፡ ጋራ፡ ወደ፡ ስራ፡ ያልመጣውን። ም፡ ፲፫፡ ፲፫።

፴፱፡ በመካከላቸውም፡ መከፋፋት፡ ሆነ፡ እስኪለያዩ፡ ድረስ። በርናባስም፡ ማርቆስን፡ ወሰደ፡በመርከብም፡ ሰረረ፡ ወደ፡ ቆጵሮስም፡ ሔደ።

፵፡ ጳውሎስ፡ ግን፡ ሲላስን፡ መረጠ፡ ወጣም፡ ለእግዚአብሔር፡ ጸጋ፡ ተማኅፅና፡በወንድሞች፡ ጸሎት።

፵፩፡ በሶርያም፡ በቂልቅያም፡ ዞረ፡ አብያት፡ ክርስቲያናትንም፡ አጸና።

## ምዕራፍ፡ ፲፮፡

፩፡ ወደ፡ ደርቤና፡ ወደ፡ ልሥጥራም፡ ደረሰ። እነሆም፡ ከዚያ፡ አንድ፡ ደቀ፡ መዝሙር፡ ነበረ፡ ስሙም፡ *ጢሞቴዎስ። ያመነችም፡የአይሁዳዊት፡ቤት፡ልጅ፡ ነበር፡ አባቱ፡ ግን፡አረማዊ። *ም፡ ፲፯፡ ፲፬። ፲፰፡ ፳፪።

፪፡ በጎም፡ የተመሰከረለት፡ ነበረ፡ በልስጥራና፡ በኢቆኒዮም፡ ከሚኖሩ፡ ወንድሞች። ም፡ ፮፡ ፫።

፫፡ ይህነን፡ ወደደ፡ ጳውሎስ፡ ከርሱ፡ ጋራ፡ ይወጣ፡

ዘንድ፡ ወስደውም፡ ገዘረውም፡ በዚያ፡ ስፍራ፡ ስላ፡ ነበሩ፡ አይሁድ። ሁሉ፡ አባቱን፡ አውቁት፡ ነበሩና፡ አረማዊ፡ እንደ፡ ሆነ። ፪፡ ጢሞ፡ ፩፡ ፭።

፬፡ አገሩንም፡ ሁሉ፡ ሲዞሩ፡ አሳልፈው፡ ስጥዋቸው፡ ከሐዋርያት፡ ከሽማግሌቹም፡ በየሩሳሌም፡ ከሚኖሩ፡ *የታዘዘውን፡ ትእዛዝ፡ ይጠብቁ፡ ዘንድ። ም፡ ፲፭፡ ፳፫—፳፱።

፭፡ አብያተ፡ ክርስቲያናትም፡ ሁሉ፡ በሃይማኖት፡ ጸንተው፡ ይኖሩ፡ ነበር፡ በቍጥርም፡ ይበዙ፡ ነበር፡ ዕለት፡ ዕለት።

፮፡ ወደ፡ አፍሪጊያም፡ ወደ፡ ገላትያም፡ ካለፉ፡ በኋላ፡ ከመንፈስ፡ቅዱስ፡ ተከለከሉ፡ ነገር፡ እንደይናገሩ፡ በእስያ። ም፡ ፲፰፡ ፳፫።

፯፡ ወደ፡ ሚስያም፡ መጡ፡ በቢቲንያም፡ይሔዱ፡ ዘንድ፡ ወደዱ፡ መንፈስ፡ ግን፡ አልተዋቸውም።

፰፡ ከሚስያም፡ ባለፉ፡ ጊዜ፡ወደ፡ጥርአስ፡መጡ።

፱፡ ለጳውሎስም፡ በሌት፡ ራእይ፡ ታየው። አንድ፡ የመቄዶንያ፡ ሰው፡ ቁሞ፡ ይለምነው፡ነበረ፡እንደሁ፡ ሲል። ወደ፡ መቄዶንያ፡ አለፍና፡ እርዳኝ።

፲፡ ራእይም፡ ባየ፡ ጊዜ፡ የዚያን፡ ጊዜውን፡ ወደ፡ መቄዶንያ፡ እንሔድ፡ ዘንድ፡ ፈቀድነ፡ፈርድናልና፡ እግዚአብሔር፡ እንደ፡ ጸራነ፡ ልናስተምራቸው።

፲፩፡ ከጥርአስም፡በወጣነ፡ጊዜ፡መንገዳችንን፡ወደ፡ ሳሞትራኬ፡ አቀናነ። በነገውም፡ ወደ፡ ኔያጶሊስ፡ ሔድነ።

፲፪፡ ከዚያም፡ ወደ፡ ፊልጵስዩስ፡ እርስዋም፡ የመቄዶንያ፡ ግዛት፡ መጀመርያ፡ የምትሆን፡ የኮሎንያ፡ ም። በዚቺም፡ አገር፡ አያሌ፡ ቀን፡ ተቀመጥነ።

፲፫፡ ቅደሚ፡ ቀንም፡ ካገር፡ ወደ፡ ሚደ፡ ወጣነ፡ ወደ፡ ወንዙ፡ ጸሎት፡ ይደረግበት፡ ዘንድ፡ ወደ፡ ለመደው፡ ስፍራ። በተቀመጥነም፡ ጊዜ፡ ለተሰበሰቡት፡ ሴቶች፡ ተናገርነ።

፲፬፡ አንዲት፡ሴትም፡ ስምዋን፡ ሊድያ፡ የሚልዋት፡ ቀይ፡ ሐር፡ የምትሸጥ፡ ከቲያቲራ፡ አገር፡ ለእግዚአብሔር፡ የምትገዛ፡ ትሰማ፡ነበረች። እግዚአብሔርም፡ ልብዋን፡ ከፈተላት፡ ከጳውሎስ፡ ወደ፡ተገለው፡ ነገር፡ ታደምጽ፡ ዘንድ። ዮሐ፡ ፮፡ ፵፬።

፲፭፡ እርስዋም፡ በተጠመቀች፡ ጊዜ፡ የቤትዋም፡ ሰዎች፡ ለመኑችነ፡ እንደሁ፡ ስትል። ይታወቃችሁስ፡ እንደ፡ ሆን፡ እኔ፡በጌታ፡ እንደመንሁ፡ ወደ፡ ቤቴ፡ገቡና፡ ተቀመጡ። የግድም፡ አለችነ።

፲፮፡ እንደህም፡ ሆነ፡እኛ፡ ወደ፡ጸሎት፡ ስንሔድ፡ አንዲት፡ ቀንጆ፡ ተቀበለችነ፡ የምዋርተኝነትም፡ መንፈስ፡ነበረባት። በጠንቋይነትዋም፡ ለጌቶችዋ፡ እጅግ፡ ጥቅም፡ ትጠቅም፡ ነበረች። ም፡ ፲፪፡ ፳፬።

፲፯፡ ይህች፡ ጳውሎስን፡ ተከተለች፡እኛንም። እንደሁ፡ ስትልም፡ ጮኸች። እሌህ፡ ሰዎች፡ የልዑል፡ አምላክ፡ ባሮች፡ ናቸው። እርሳቸውም፡ የመድኃኒት፡ መንገድ፡ ያስተምሩዋችኋል። ማር፡ ፩፡ ፳፬።

፲፰፡ ይህነንም፡ እጅግ፡ ቀን፡ አደረገች። ይህም፡ ጳውሎስን፡ አሳዘነው፡ ተመለሰም፡ ለዚያ፡ ጋኔንም፡ አለ። አዝዛለሁ፡ በየሱስ፡ ክርስቶስ፡ ስም፡ ከርስዋ፡ ትወጣ፡ዘንድ።በዚያውም፡ጊዜ፡ወጣ። ማቴ፡ ፲፯፡ ፲፰።

፲፱፡ ጌቶችዋም፡ ባዩ፡ ጊዜ፡ የመጠቀማቸው፡ ተስፋ፡ እንደ፡ ተቈረጠ፡ ጳውሎስንና፡ ሲላስን፡ ያዝዋቸው፡ በገቢያም፡ ወደ፡ለቆች፡ ጐተትዋቸው።

፳፡ ወደ፡ አገርም፡ ሹማምት፡ባመጥዋቸው፡ጊዜ፡ አሉ። እሌህ፡ ሰዎች፡ አገራችንን፡ እጅግ፡ አወኩ፡ እርሳቸውም፡ አይሁድ፡ ናቸው። ም፡ ፲፯፡ ፮።

፳፩፡ እንቀበለውም፡እናደርገውም፡ዘንድ፡የማይገባነን፡ሕግ፡ያስተምራሉ። እኛ፡ የሮም፡ ሰዎች፡ነንና።

፳፪፡ ሕዝቡም፡ ተነሣባቸው፡ሹማምትም፡ልብሳቸውን፡ ቀደዱ፡ በሽመልም፡ *ይመትዋቸው፡ ዘንድ፡ አዘዙ። *፪፡ ቆሮ፡ ፲፩፡ ፳፭። ፊል፡ ፩፡ ፴። ፩፡ ተሰ፡ ፪፡ ፪።

፳፫፡ በብዙ፡ መምታትም፡በገረፉዋቸው፡ጊዜ፡ ወደ፡ ግዞት፡ ቤት፡ ጣልዋቸው፡ ግዞት፡ ጠባቂውንም፡ አዘዙት፡ ተጠንቅቆ፡ ይጠብቃቸው፡ ዘንድ።

፳፬፡ እርሱም፡ ይህነን፡ ትእዛዝ፡ በተቀበለ፡ ጊዜ፡ ወደ፡ ውስጡ፡ግዞት፡ አዘጋቸው፡ እግራቸውንም፡ በመጠርቀቂያ፡ ጠረቀቃቸው።

፳፭፡ በመንፈቀ፡ሌሊትም፡ጳውሎስና፡ ሲላስ፡ *ይጸልዩ፡ እግዚአብሔርንም፡ ያመሰግኑ፡ ነበሩ። እሥረኞችም፡ይሰምዋቸው፡ ነበሩ። *ም፡ ፬፡ ፴፩። ፭፡ ፵፩።

፳፮፡ ድንገትም፡ ታላቅ፡መናወጥ፡ ሆነ፡የግዞቱ፡ መሠረት፡እስኪናወጥ፡ ድረስ። የዚያን፡ጊዜም፡ ደጆች፡ ሁሉ፡ ተከፈቱ። እሥራቱም፡ ለታሠሩት፡ ሁሉ፡ ተፈታላቸው።

፳፯፡ ግዞት፡ ጠባቂውም፡ ከእንቅልፉ፡ በነቃ፡ጊዜ፡ የግዞቱንም፡ ደጁ፡ ሁሉ፡ ተከፍቶ፡ ባየ፡ ጊዜ፡ሰይፉን፡ መዘዘ፡ ራሱን፡ ይገድል፡ ዘንድ፡ የታሠሩቱ፡ የኰበለሉ፡ መስሎት።

፳፰፡ ጳውሎስ፡ ግን፡ በታላቅ፡ ቃል፡ ጮኸበት፡ እንደሁ፡ ሲል። በራስህ፡ ክፉ፡ ነገር፡ አታድርግ። እኛ፡ ሁላችን፡ ከዚህ፡ ነንና።

፳፱፡ መብራትም፡ፈለገ፡ ተነሣም፡ኢየተንቀጠቀጠም፡ ገባ፡ ለጳውሎስና፡ ለሲላስም፡ ሰግደ፡ ወደቀ።

፴፡ ወደ፡ ሚደም፡ አወጣቸው፡ አለም። ጌቶቼ፡ ሆይ፡ ምን፡ ይገባኛል፡ *አደርገው፡ ዘንድ፡ እንድድን። ም፡ ፪፡ ፴፯። *ሉቃ፡ ፫፡ ፲።

፴፩፡ እርሳቸውም፡አሉት። በጌታ፡በየሱስ፡ ክርስቶስ፡ *እመን፡ አንተም፡ ትድናለህ፡ ቤትህም፡ ሁሉ። *ዮሐ፡ ፫፡ ፲፮።

፴፪፡ የጌታንም፡ ነገር፡ አሜወቱት፡ በቤቱ፡ ላሉትም፡ ሰዎች፡ ሁሉ።

፴፫፡ በዚያን፡ ጊዜም፡ በሌት፡ ወስዷቸው፡ ቍስላቸውንም፡አጠባቸው። የዚያን፡ ጊዜውንም፡ተጠመቀ፡ እርሱ፡ የቤቱም፡ ሰዎች፡ ሁሉ።

፴፬፤ ወደ፡ ቤቱም፡ አወጣቸው፡ ማዕድም፡ አቀረ
በላቸው፡ ደኅለውም፡ እርሱ፡የቤቱም፡ ሰዎች፡ሁሉ፡
በእግዚአብሔር፡ ስላመኑ።
፴፭፤ ማልደም፡ በሆነ፡ጊዜ፡ሹማምት፡አሣሮችን፡
ሰደዱ፡ እንደሁ፡ ሲሉ፡ እሊያን፡ ሰዎች፡ ፍታ።
፴፮፤ ግዞት፡ ጠባቂውም፡ ለጳውሎስ፡ የምስራች፡
ነገረው፡ በዚህ፡ ነገር። ሹማምት፡ ላኩ፡ ትወጡ፡ ዘን
ድ። አሁንም፡ ውጡ፡ በደህናም፡ ሒዱ።
፴፯፤ ጳውሎስ፡ ግን፡ አላቸው። በግልጽ፡ መቱን፡ ያ
ለ፡ ፍርድ፡ አኛ፡ *የሮም፡ ሰዎች፡ ስንሆን፡ በግዞትም፡
ጨመሩን። አሁንም፡ በሥውር፡ ያወጡናልን። አይሆ
ንም። እርሳቸው፡ መጥተው፡ ያውጡን፡እንጂ።
ም፡ ፳፬፡ ፳፭።
፴፰፤ አሣሮችም፡ ይህነን፡ነገር፡ለሹማምት፡ነገሩ።
የሮም፡ ሰዎች፡ እንደ፡ ሆኑም፡ በሰሙ፡ ጊዜ፡ ፈሩ።
፴፱፤ ወደርሳቸውም፡ መጡ፡ተናገርዋቸውም፡ አ
ወጥዋቸውም፡ ከከተማም፡ ይወጡ፡ ዘንድ፡ *ለመ
ንዋቸው። *ማቴ፡ ፳፡ ፴፬።
፵፤ ከግዞትም፡ ከወጡ፡ በኋላ፡ ወደ፡ሊድያ፡ ገቡ።
ወንድሞችንም፡ ባዩ፡ ጊዜ፡ አጽንዋቸው፡ ወጡም።

ምዕራፍ፡ ፲፯፤

፩፤ ወደ፡ አምፊጶሊስም፡ ወደ፡አጶሎንያም፡ ካለ
ፉ፡ በኋላ፡ ወደ፡ ተሰሎንቄ፡ መጡ፡ የአይሁድ፡ መስ
ጊድ፡ ወደለባት። ፩፡ ተሰ፡ ፪፡ ፪።
፪፤ ጳውሎስም፡ እንደ፡ ለመደው፡ ወደርሳቸው፡
ገባ፡ ሶስት፡ ሰንበትም፡ የመጽሐፉን፡ ይነግራቸው፡
ነበር።
፫፤ ኢየከፈተ፡ ኢየገለጸም፡ ለክርስቶስ፡እንደተገ
ባው፡ ሕማማት፡ ይቀበል፡ ዘንድ፡ ከሙታንም፡ ይነ
ሣ፡ ዘንድ። እንደ፡ህም፡ ሲል። ይህ፡ ክርስቶስ፡የሱስ፡
ነው፡ እኔ፡ እርሱን፡ የማስተምራችሁ።
ሉቃ፡ ፳፬፡ ፳፯፡ ፵፭።
፬፤ ከርሳቸውም፡ ሰዎች፡ አመኑ፡ ከጳውሎስና፡ ከ
ሲላስም፡ ኃራ፡ ሆኑ። ከአረማውያንም፡ እግዚአብ
ሔርን፡ ከሚፈሩ፡ ሰዎች፡ እጅግ፡ ብዙ። ከሴቶችም፡
ከታላላቆች፡ ጥቂት፡ ያይደሉ።
፭፤ የማያምኑ፡ አይሁድ፡ ግን፡ ክፉ፡ ሰዎች፡ ከገቢ
ያ፡ ይሰበስቡባቸው፡ ነበሩ፡ አገሩንም፡ አወኩ፡ በያሶ
ንም፡ ቤት፡ ቀሙ፡ ሲሸዋቸው፡ ወደ፡ ሕዝብ፡ ይወስ
ድዋቸው፡ ዘንድ።
፮፤ ባለገኟቸውም፡ ጊዜ፡ ያሶንን፡ ከወንድሞች
ም፡ አንዳንዱን፡ ወደገሩ፡ አለቆች፡ ጐተቱ፡ እንደሁ፡
ሲሉም፡ ጮሁ። እለዚህ፡ ዓለሙን፡ ያወኩ፡ ደግሞ፡
ከዚህ፡ መጡ። ም፡ ፲፮፡ ፳። ፩፡ ነገሥ፡ ፲፰፡ ፲፯።
፯፤ ያሶንም፡ ተቀበላቸው። እሌህም፡ ሁሉ፡የቄሣ
ርን፡ ትእዛዝ፡ የሚጣላ፡ ያደርጋሉ፡ እንደሁ፡ ሲሉ።
ሌላ፡ ንጉሥ፡ አለ፡ የሱስ፡ የሚሉት። ሉቃ፡ ፳፫፡ ፪።
፰፤ ሕዝብንም፡ ያገሩንም፡ አለቆች፡ አስታወኩ፡
ይህነን፡ ነገር፡ በሰሙ፡ ጊዜ።
፱፤ ከያሶንም፡ ከቀሩትም፡ዋስ፡ተቀበሉ፡ ለቀቅዋ
ቸውም።
፲፤ ወንድሞችም፡ የዚያን፡ ጊዜ፡ ጳውሎስንና፡ሲላ
ስን፡ ወደ፡ ቤርያ፡ አገር፡ በሌት፡ ሰደድዋቸው። ወደር
ስዋም፡ በመጡ፡ ጊዜ፡ወደ፡ አይሁድ፡ መስጊድ፡ገቡ።
፲፩፤ እርሳቸውም፡ የከበሩ፡ ነበሩ፡ በተሰሎንቄ፡ ከ
ሚኖሩት፡ ይልቅ። ነገሩን፡ በፍጹም፡ ልባቸው፡ ተቀ
ብለዋልና። ሁለጊዜም፡ መጻሕፍትን፡ *ይመረምሩ፡
ነበሩ፡ ይህ፡ነገር፡እንደሁ፡እንደሆነ። *ኢሳ፡ ፴፬፡ ፲፮።
ሉቃ፡ ፲፮፡ ፳፱። ዮሐ፡ ፭፡ ፴፱።
፲፪፤ ከርሳቸውም፡ብዙ፡ ሰዎች፡ አመኑ። ከዮናው
ያንም፡ እጅግ፡ ከተመረጡም፡ ሴቶች፡ ወንዶችም፡
ጥቂት፡ ያይደሉ።
፲፫፤ አይሁድም፡ በተሰሎንቄ፡ ያሉት፡ ባወቁ፡ጊዜ፡
ጳውሎስ፡ የእግዚአብሔርን፡ነገር፡ በቤርያ፡ ያስተም
ር፡ እንደ፡ ነበረ፡ ወደዚያ፡ ደግሞ፡ መጡ፡ሰዎችንም፡
አናወጡ። ፩፡ ተሰ፡ ፪፡ ፲፬።
፲፬፤ በዚያን፡ ጊዜም፡ወንድሞች፡ ጳውሎስን፡ ሰደ
ዱ፡ ወደ፡ ባሕር፡ ይሔድ፡ዘንድ። ሲላስና፡ *ጢሞቴዎ
ስ፡ ግን፡ ከዚያው፡ ተቀመጡ። *ም፡ ፲፮፡ ፩።
፲፭፤ ጳውሎስንም፡ የወሰዱት፡ወደ፡ አቴና፡ይዘው
ት፡ ሔዱ። ከርሱም፡ መልክት፡ በወሰዱ፡ ጊዜ፡ ወደ፡
ሲላስና፡ ወደ፡ ጢሞቴዎስ፡ ፈጥነው፡ ወደርሱ፡ ይሔ
ዱ፡ ዘንድ፡ ወጡ።
፲፮፤ ጳውሎስ፡ ግን፡ በአቴና፡ ሲጠብቃቸው፡ ሰው
ነቱ፡ ታወከበት፡ በራሱ፡ አገሪቱ፡ ብዙ፡ ጣዖት፡ ስታመ
ልክ፡ እንደ፡ ነበረች፡ አይትዋልና።
፲፯፤ በጉባዔም፡ አይሁድን፡ ያስተምር፡ ነበረ፡ እግ
ዚአብሔርንም፡ የሚፈሩትን። በገቢያም፡ ሁለግዜ፡
የሚያገኟቸውን።
፲፰፤ ከኤጲቆሮስም፡ ከእስጦኢኮችም፡ ፈሎሶፎ
ች፡ ወገን፡ ይጋደሉት፡ ነበሩ። ምን፡ ይሻል፡ ይህ፡ *ነገር፡
ዘሪ፡ ይል፡ ዘንድ። ሌሎችም፡ አሉ። ባዲሶች፡ አማል
ክት፡ስም፡ያስተምረናል። በየሱስ፡በትንሣኤውም፡
ያስተምራቸው፡ ነበርና። *፩፡ ቆር፡ ፬፡ ፲፪።
፲፱፤ ያዙትም፡ ወደ፡ አርዮስ፡ ፋጎስም፡ ወሰዱት፡
እንደሁ፡ ሲሉ። ይህነን፡ አዲስ፡ ትምህርት፡ የምትና
ገርበትን፡ እናውቅ፡ ዘንድ፡ ይቻለናልን።
፳፤ ባዲስ፡ ነገር፡ ጆሮዋችነን፡ ታደክመሃልና። እኛ
ም፡ እንወደለን፡ እናውቅ፡ ዘንድ፡ ይህ፡ ነገር፡ ምንድ
ር፡ ነው።
፳፩፤ አቴናዎች፡በዚያም፡የነበሩ፡እንግዶች፡ጊዜያ
ቸውን፡ በሌላ፡ ነገር፡አያሳልፉም፡ነበሩና፡አዲስ፡ነገር፡
ከመናገርና፡ ከመስማት፡ በቀር።
፳፪፤ ጳውሎስም፡ በአርዮስ፡ ፋጎስ፡ መካከል፡ ቀ
መ፡ አለም። እላንተ፡ የአቴና፡ ሰዎች፡ አያችኋለሁ፡
በስራችሁ፡ ሁሉ፡ጣዖታትን፡ ማምለክ፡እንድታበዙ።

፳፫፤ እኔ፡ ሳልፍ፡ የምታመልኩትን፡ አይቻለሁና፡ መሠዊያም፡ አገኘሁ፡በርሱ፡ የተጻፈ፡ የሚል። ለማ ይታወቅ፡ አምላክ። ይህም፡ የምታመልኩት፡የማታ ውቁትም፡ ይህነን፡ እኔ፡እነግራችኋለሁ።

፳፬፤ ዓለሙን፡ የፈጠረ፡አምላክ፡ በርሱዋ፡ያለው ንም፡ ሁሉ። እርሱ፡ የሰማይና፡ የምድር፡ ጌታ፡ነውና፡ አይኖርም፡ እጅ፡ በሰራው፡ መቅደስ። ም፡ ፯፡ ፵፰፡፡

፳፭፤ የሰው፡እጅም፡ አያገለግለውም፡ *ማነንም፡ አይሻም። እርሱ፡ለሁሉ፡ ሕይወትና፡ትንፋሽ፡ ይሰጣልና፡ ያላቸውንም፡ ነገር፡ ሁሉ። *መዝ፡ ፶፡ ፰፡፡

፳፮፤ እርሱም፡ ካንድ፡ ደም፡ አሕዛብን፡ ሁሉ፡ ፈጠረ፡ በምድር፡ ፊት፡ ሁሉ፡ ላይ፡ ይኖሩ፡ ዘንድ። ዘመኑንም፡ ለርሳቸው፡ ሠራ፡ ከጥንት፡ ጀምሮ፡ ስፍራቸውንም፡ *ይኖሩበት፡ዘንድ። *ዘዳግ፡ ፴፪፡ ፰፡፡

፳፯፤ እግዚአብሔርን፡ እንዲሹ፡ እንዲፈልጉም፡ ምናልባት፡ ያገኙት፡ እንደ፡ሆነ። ነገር፡ ግን፡ ከኛ፡ ከሁላችን፡ የራቀ፡ አይደለም።

፳፰፤ እኛ፡ በርሱ፡ እንኖራለንና፡ እንንቀሳቀሳለንም፡ እንገኛለንም። ከላንት፡አዋቆች፡ የቅኔ፡ አድራጎች፡ ደግሞ፡ እንደተናገሩ። እኛ፡ ዘመዶቹ፡ነንና።

፳፱፤ የእግዚአብሔር፡ ዘመዶች፡ከሆነ፡አይገባም፡ እንል፡ ዘንድ፡ ወርቅም፡ ሆነ፡ ብርና፡ ድንጊያ፡ ሆነ፡ በሰው፡ ብልሃት፡ ባሳቡም፡ የተቀረጸ፡ የተጸረበም፡ ስራ፡ ሆነ፡ ይህ፡ አምላክን፡ ይመስላል። *ዘፍ፡ ፩፡ ፳፯፡፡ ኢሳ፡ ፵፡ ፲፰፡፡

፴፤ ያነንም፡ የድንቍርናውን፡ *ወራት፡ እግዚአብሔር፡ አሳለፈው። አሁን፡ ግን፡ሰውን፡ ሁሉ፡በየቦታቸው፡ †አዘዘ፡ ንስሐ፡ ይገቡ፡ ዘንድ። *ም፡ ፲፬፡ ፲፮፡፡ †ሉቃ፡ ፳፬፡ ፵፯፡፡

፴፩፤ በዓለሙ፡የሚፈርድበትን፡ ቀን፡ አቁሞዋልና፡ በቅን፡ ፍርድ፡ በዚያ፡ ሰው፡ እጅ፡ በመረጠው። ስለዚህም፡ የታመነ፡ ምስክር፡ለሁሉ፡ሰጠው፡እርሱን፡ በማስነሣቱ፡ ከሙታን። ሮሜ፡ ፲፡ ፲፬፡፡

፴፪፤ በሙታንም፡ መነሣት፡በሰሙ፡ጊዜ፡እኩሌታቸው፡ *አፌዙ፡ እኩሌታቸውም፡ አሉ። ይህነንም፡ ደግሞ፡ እንሰማሃለን። *፩፡ ቆሮ፡ ፩፡ ፳፫፡፡

፴፫፤ እንደሁም፡ወጣ፡ጳውሎስ፡በመካከላቸው።

፴፬፤ ከሰዎች፡ ግን፡ተከፍለው፡ከርሱ፡ጋራ፡አንድ፡ ሆኑ፡ አመኑም። ከርሳቸውም፡ አንዱ፡ ዲዮናስዮስ፡ ነበር፡ የአርዮስ፡ ፋጎስ፡ ፈራጅ። አንዲት፡ ሴትም፡ ስምዋን፡ደማሪስ፡የሚሉዋት። ሌሎችም፡ከርሳቸው፡ ጋራ።

## ምዕራፍ፡ ፲፰፡

፩፤ ከዚህም፡ በኋላ፡ጳውሎስ፡ ከአቴና፡ወጣ፡ወደ፡ ቆሮንቶስም፡ መጣ።

፪፤ ከዚያም፡ አንድ፡ አይሁዳዊ፡ አገኘ፡ ስሙም፡ አኪላስ፡ አገሩም፡ ጳንጦስ፡የሚሆን። እርሱም፡ከጥቂት፡ወራት፡ በፊት፡ ከኢጣልያ፡ መጣ፡ ከጵርስኪላ፡ ከምሽቱ፡ ጋራ። አቅሎዲዮስ፡ አዞ፡ ነበርና፡ አይሁድ፡ ከሮሜ፡ ይወጡ፡ ዘንድ። ሮሜ፡ ፲፮፡ ፫፡፡

፫፤ ከርሳቸውም፡ ጋራ፡ ተቀመጠ፡ *ይሰራም፡ነበር፡ ከስራቸው፡ ወገን፡ ነበረና። ስራቸውም፡ ድንኳን፡ መስፋት፡ ነበረ። *፩፡ ቆሮ፡ ፬፡ ፲፪፡፡

፬፤ ቅዳሜ፡ ቅዳሜም፡ በመስጊድ፡ ይናገር፡ ነበር፡ አይሁድንም፡ አረማውያንንም፡ እሺ፡ ያሰኝ፡ ነበረ።

፭፤ *ሲላስና፡ ጢሞቴዎስም፡ ከመቄዶንያ፡ በመጡ፡ ጊዜ፡ ጳውሎስ፡ በመንፈስ፡ በረታ፡ ለአይሁድ፡ መሰከረ፡ የሱስ፡ ክርስቶስ፡ እንደ፡ ሆነ። *ም፡ ፲፯፡ ፲፬፡ ፲፭፡፡

፮፤ እርሳቸው፡ግን፡በተቋቋሙ፡በተሳደቡም፡ጊዜ፡ ልብሱን፡ *አረገፈ፡አላቸውም።ደማችሁ፡በራሳችሁ፡ ይሁን። እኔ፡ ንጹህ፡ ነኝ። ከንግዲህ፡ ወዲህ፡ወደ፡ አሕዛብ፡ እሔዳለሁ። *ም፡ ፲፫፡ ፶፩፡፡ ፳፡ ፳፮፡፡

፯፤ ከዚያም፡ ወጥቶ፡ ወደንድ፡ ሰው፡ ቤት፡ ገባ፡ ስሙ፡ ዮስጦስ፡ለእግዚአብሔር፡የሚገዛ። ቤቱም፡ ወደ፡ መስጊድ፡ የቀረበ፡ ነበር።

፰፤ ቀሪስጶስም፡ የመስጊዱ፡ አለቃ፡ በጌታ፡ አመነ፡ ከቤቱ፡ሰዎች፡ሁሉ፡ጋራ።ብዙም፡ሰዎች፡ከቆሮንቶስ፡ ወገን፡ በሰሙ፡ ጊዜ፡ አመኑ፡ ተጠመቁም።

፱፤ ጌታም፡ በሌት፡ በራእይ፡ ጳውሎስን፡ አለው። አትፍራ፡ ነገር፡ ግን፡ ተናገር፡ ዝምም፡ አትበል። ፩፡ ቆሮ፡ ፪፡ ፫፡፡

፲፤ እኔ፡ ካንተ፡ ጋራ፡ ነኝና። ማንም፡ አይነካህም፡ ክፉ፡ ሊያደርግብህ። በዚህ፡ አገር፡ †እጅግ፡ ወገን፡ አለኝና። *ኤር፡ ፩፡ ፰፡፡ †ሆሴ፡ ፪፡ ፳፫፡፡ ዮሐ፡ ፲፡ ፲፮፡፡

፲፩፤ በቆሮንቶስም፡ አመት፡ ከስድስት፡ ወር፡ ተቀመጠ፡ የእግዚአብሔርን፡ ነገር፡ ሲያስተምር፡ በመካከላቸው።

፲፪፤ ጋሊዮንም፡ በአካይያ፡ ላይ፡ በተሾመ፡ ጊዜ፡ አይሁድ፡ ተግብረው፡ በጳውሎስ፡ ተነሡበት፡ ወደ፡ መቀመጫውም፡ አመጡት።

፲፫፤ እንደህ፡ ሲሉ። ይህ፡ ሰዎችን፡ ያግባባል፡ እግዚአብሔርን፡ ያመልኩ፡ ዘንድ፡ በሕግ፡ ላይ።

፲፬፤ ጳውሎስም፡ አፉን፡ ይገልጽ፡ ዘንድ፡ በወደደ፡ ጊዜ፡ጋሊዮን፡ አይሁድን፡ አላቸው። በደል፡ ቢሆን፡ ወይም፡ ሌላ፡ ክፉ፡ ነገር፡ አላንት፡ አይሁድ፡ መልካም፡ ነበረ፡ እሰማችሁ፡ ዘንድ። ም፡ ፳፭፡ ፲፩—፲፰፡፡

፲፭፤ ነገር፡ግን፡መጣበት፡ከሆነ፡ስለ፡ ነገር፡ ስለ፡ ስምም፡ ስለ፡ሕጋችሁም፡ አላንት፡ *እወቁ።እኔ፡ አልወድምና፡ በዚህ፡ ነገር፡ ፈራጅ፡ እሆን፡ ዘንድ። *ማቴ፡ ፳፯፡ ፳፬፡፡ ዮሐ፡ ፲፰፡ ፴፩፡፡

፲፮፤ ከዚያ፡ ወዲያም፡ ከወንበሩ፡ ፊት፡ አስወጣቸው።

፲፯፤ ሕዝቡም፡ ሁሉ፡ *ሶስቴኔስን፡ያዙት፡የመስጊዱን፡ አለቃ፡ በወንበሩ፡ ፊትም፡ መቱት። ጋልዮንም፡ በዚህ፡ነገር፡ሁሉ፡አንዳች፡አላለም። *፩ ቆሮ፡ ፩፡ ፩፡፡

፲፰፤ ጳውሎስ፡ግን፡ደግሞ፡እጅግ፡ቀን፡ተቀመጠ።

ከዚያም፡ በኋላ፡ ወንድሞችን፡ ተሰናበተና፡ወደ፡ ሶር
ያ፡ሔደ። ከርሱም፡ጋራ፡ጵርስኪላስ፡ አኪላስም፡ *ራ
ሱን፡ በተላጨ፡ ጊዜ፡ በክንክሬያ። ስለት፡ ነበረበትና።
*ም፡ ፳፩፤ ፳፬፤፤ ዘኍል፡ ፮፤ ፱፤ ፲፰፤፤

፲፱፤ ወደ፡ኤፌሶንም፡ ደረሰ፡ እሊያንም፡ ከዚያ
ው፡ተዋቸው። እርሱ፡ ግን፡ወደ፡ መስጊድ፡ ገባ፡ ለአይ
ሁድም፡ ተናገረ።

፳፤ እርሳቸውም፡ በለመኑት፡ ጊዜ፡እጅግ፡ ቀን፡ከ
ርሳቸው፡ ዘንድ፡ እንዲቀመጥ፡ ልመናቸውን፡ አልሰ
ማም።

፳፩፤ ተሰናበታቸው፡ እንጂ፡ እንዲህ፡ ሲል። ከቶ፡
ይገባኛል፡የሚመጣውን፡በዓል፡ *በየሩሳሌም፡አደር
ግ፡ዘንድ። ነገር፡ግን፡ ወደላንት፡ እመለሳለሁ፡ በእግዚ
አብሔር፡ ፈቃድ። ከኤፌሶንም፡ ወጣ።
*፩፤ ቆሮ፡ ፬፤ ፲፱፤፤ ዕብ፡ ፮፤ ፫፤፤ ያዕ፡ ፬፤ ፲፭፤፤

፳፪፤ ወደ፡ ቂሣርያ፡ በመጣ፡ጊዜ፡ ከዚያ፡ ወጣ፡ ለ
ቤተ፡ክርስቲያንም፡ ሰላም፡ ሰጠ፡ ወደ፡ አንጾኪያም፡
ወረደ።

፳፫፤ ከዚያም፡አያሌ፡ ቀን፡ከተቀመጠ፡ በኋላ፡ወ
ጣ፡በገላትያና፡ በፍሪጊያም፡ አገር፡ ሁሉ፡ አለፈ፡ደቀ፡
መዛሙርትንም፡ ሁሉ፡አጸና።

፳፬፤ አንድም፡አይሁዳዊ፡ነበረ፡ ስሙን፡ አጵሎስ፡
የሚሉት፡አገሩም፡እስክንድርያ። ተናጋሪ፡ ሰው። መ
ጽሐፍ፡ለመተርጐምም፡ብርቱ፡ነበረ። ፩፤ቆሮ፡፫፤፮፤፤

፳፭፤ ይህ፡በእግዚአብሔር፡መንገድ፡የተማረ፡ነበ
ር፡በመንፈስም፡የሚቃጠል፡ነበረ። በጌታም፡ነገር፡ ይ
ናገር፡ ያስተምርም፡ነበረ። የዮሐንስንም፡ ጥምቀት፡
ብቻ፡ ያውቅ፡ ነበረ።

፳፮፤ ይህም፡ በመስጊድ፡ነገሩን፡ ይገልጥ፡ ጀመረ።
አኪላስና፡ጵርስኪላም፡ በሰሙት፡ ጊዜ፡ ወሰዱት፡ የ
እግዚአብሔርንም፡ መንገድ፡ አስታወቁት፡ እጅግ፡
ፈጽም፡ ማስታወቅ።

፳፯፤ እርሱም፡ ወደ፡አካይያ፡ ማለፍ፡ በወደደ፡ ጊ
ዜ፡ወንድሞች፡ወደ፡ደቀ፡ መዛሙርት፡ስለርሱ፡ ጻፉ፡
ለመንዋቸውም፡ ይቀበሉት፡ ዘንድ። ወደርሳቸው
ም፡በመጣ፡ ጊዜ፡ እጅግ፡ ጠቀመ፡ በጸጋ፡ ላመኑት፡ ሰ
ዎች።

፳፰፤ አይሁድን፡ በሁሉ፡ ፊት፡ ይገሥጽ፡ ነበርና፡ ጽ
ኑ፡ተግሣጽ፡ከመጽሐፍ፡ኢየገለጠ፡ የሱስ፡ክርስቶስ፡
እንደ፡ሆነ።
ም፡ ፱፤ ፳፪፤፤ ፲፯፤ ፫፤፤

## ምዕራፍ፡ ፲፱፤

፩፤ አጵሎስም፡ በቆሮንቶስ፡ ሳለ፡ ጳውሎስ፡ የዚያ
ን፡አገር፡ላይ፡ላዩን፡ ይዞር፡ ነበር፡ወደ፡*ኤፌሶንም፡መ
ጣ፡ደቀ፡መዛሙርትም፡አገኘ። *ም፡ ፲፰፤ ፲፱፤ ፳፩፤፤

፪፤ አላቸውም። *መንፈስ፡ ቅዱስን፡ ተቀበላችሁ
ን፡ባመናችሁ፡ጊዜ። እርሳቸው፡ግን፡ አሉት። መቀበል
ስ፡ ይቅርና፡ †መንፈስ፡ቅዱስ፡ እንዳለ፡ ሰንኳ፡ አልሰ
ማንም።
*ም፡ ፲፤ ፵፬፤፤ †ዮሐ፡ ፯፤ ፴፱፤፤

፫፤ አላቸውም። በምን፡ ተጠመቃችሁ። እርሳቸው
ም፡ አሉ። በዮሐንስ፡ ጥምቀት።

፬፤ ጳውሎስም፡አለ። *ዮሐንስስ፡ በንስሐ፡ጥምቀ
ት፡አጠመቀ፡ለሕዝብ፡እንዲህ፡ ሲል፡ ያምኑ፡ ዘንድ፡
ከርሱ፡ በኋላ፡ በሚመጣው። ያውም፡ በክርስቶስ፡ የ
ሱስ።
*ማቴ፡ ፫፤ ፲፩፤፤

፭፤ ይህንም፡ በሰሙ፡ ጊዜ፡ ተጠመቁ፡ በጌታ፡ በየ
ሱስ።

፮፤ ጳውሎስም፡ እጁን፡ በጫነባቸው፡ ጊዜ፡ መንፈ
ስ፡ቅዱስ፡ ወረደላቸው። ባዲስ፡ቋንቋም፡ ተናገሩ፡ ት
ንቢትም፡ ተናገሩ።
ም፡ ፰፤ ፲፯፤፤ ፲፤ ፵፬፤ ፵፮፤፤

፯፤ ሰዎችም፡አሥራ፡ሁለት፡ያህል፡ ነበሩ።

፰፤ ወደ፡ መስጊድም፡ በገባ፡ ጊዜ፡ በግልጥ፡ ይናገር፡
ነበር፡ ሶስት፡ ወርም፡ የሚያህል፡ ተቀመጠ፡ ሲያስተ
ምር፡ሲረዳቸውም፡ ስለ፡እግዚአብሔር፡ ስለ፡ መንግ
ሥቱ፡ ነገር።

፱፤ ሰዎችም፡ ከርሳቸው፡ *እምቢ፡ ቢሉ፡ ባያምኑ
ም፡ መንገዱንም፡ †ቢሰድቡ፡ በጉባኤው፡ ፊት። ከር
ሳቸው፡ራቀ፡ደቀ፡ መዛሙርትንም፡ ከርሳቸው፡ ለየ፡
ሁለግዜም፡ ይነግር፡ ነበረ፡ ባንድ፡ ሰው፡ ቤት፡ ስሙን፡
ጢራኑስ፡ የሚሉት፡ እርሱም፡ መምህር፡ የሚሆን።
*፪፤ ጢሞ፡ ፩፤ ፲፭፤፤ †ም፡ ፱፤ ፪፤፤

፲፤ ይህም፡ ሆነ፡ ሁለት፡ አመት፡ በእስያ፡ የተቀመ
ጡት፡ሁሉ፡የጌታን፡ የየሱስን፡ ነገር፡ እስኪሰሙ፡ ድረ
ስ። እርሳቸውም፡ አይሁድ፡ አረማውያንም።

፲፩፤ እግዚአብሔርም፡ ልዩ፡ ልዩ፡ ታላቅ፡ ተአምራ
ት፡ ያደርግ፡ ነበረ፡ በጳውሎስ፡ እጅ።
ም፡ ፲፬፤ ፫፤፤

፲፪፤ ከሰውነቱ፡ መጠምጠሚያውን፡ ሌላ፡ ልብሰ
ም፡ እስኪወስዱ፡ ድረስ፡ በድውያንም፡ ላይ፡ እስኪ
ጭኑት፡ ድረስ። ከርሳቸውም፡ ደዌያቸው፡ ይወጣ፡
ነበረ። ደግሞም፡ አጋንንት፡ ክፉ፡ ክፉ፡ የሆኑ፡ ከርሳቸ
ው፡ ይወጡ፡ ነበሩ።
ም፡ ፭፤ ፲፭፤፤

፲፫፤ ከአይሁድም፡ ሰዎች፡ መጡ፡ አስማት፡ ኢያ
ደረጉ፡ የሚዞሩ። የጌታንም፡ የየሱስን፡ ስም፡ ይጸሩ፡
ጀመሩ፡ክፉ፡ ክፉ፡ አጋንንት፡ ባሉባቸው፡ ላይ። እንዲ
ህ፡ሲሉ። እናምላችኋለን፡ በየሱስ፡ ጳውሎስ፡ በሚያ
ስተምርበት።
ሉቃ፡ ፱፤ ፵፱፤፤

፲፬፤ እንዲህም፡ ያደረጉት፡ ሰዎች፡ የአስቄዋ፡ የአ
ይሁዳዊ፡ የካህናቱ፡አለቃ፡ ልጆች፡ነበሩ፡ ሎጥራቸው
ም፡ ሰባት፡ ነበር።

፲፭፤ ክፉውም፡ጋኔን፡መለሰ፡እንዲህም፡አለ። የሱ
ስንስ፡ አውቀዋለሁ፡ ጳውሎስንም፡ ተረድቸዋለሁ፡
ነገር፡ ግን፡ እላንት፡ እለማን፡ናችሁ።

፲፮፤ ያ፡ሰውም፡ክፉ፡ጋኔን፡ያለበቱ፡ርጠባቸው፡ገዛ
ቸውም፡አሸነፋቸውም። ከዚያ፡ቤት፡ ራቁታቸውን፡
ተቍስለው፡ እስኪሸሹ፡ ድረስ።

፲፯፤ ይህም፡በኤፌሶን፡በሚኖሩ፡በአይሁድና፡በአ
ረማውያን፡ ሁሉ፡ ዘንድ፡ ታወቀ፡ በሁሉም፡ ላይ፡ ፍር

ሣት፡ ወደቀባቸው፡ የጌታም፡ የየሱስ፡ ስም፡ ታላቅ፡ ሆነ። ምዕ፡ ፭፡ ፭፡ ፲፩።

፲፰፡ ካመኑትም፡ እጅግ፡ ሰዎች፡ ይመጡ፡ ነበር፡ ኀጢአታቸውን፡ ኢያስታውቁ፡ ያደረጉትንም፡ ኢየተናገሩ።

፲፱፡ እጅግም፡ ሰዎች፡ አስማት፡ ያደረጉ፡ መጽሐፋቸውን፡ አከማቹ፡ በሰው፡ ሁሉ፡ ፊትም፡ አቃጠሉት። ዋጋውንም፡ ቈጠሩ፡ አገኙትም፡ አምሳ፡ ሺህ፡ ብር።

፳፡ እንደሁ፡ የእግዚአብሔር፡ ነገር፡ በኃይል፡ ያድግ፡ ይጸናም፡ ነበር። ምዕ፡ ፮፡ ፯።

፳፩፡ ይህም፡ ነገር፡ በተፈጸመ፡ ጊዜ፡ ጳውሎስ፡ በመንፈስ፡ አሰበ፡ ወደ፡ መቄዶንያና፡ ወደ፡ አካይያ፡ ካለፈ፡ በኋላ፡ ወደ፡ የሩሳሌም፡ ይሔድ፡ ዘንድ፡ እንደሁ፡ ሲል። ወደዚያም፡ ከደረስሁ፡ በኋላ፡ ደግሞ፡ *ሮሚን፡ አይ፡ ዘንድ፡ ይገባኛል። *ምዕ፡ ፳፫፡ ፲፩።

፳፪፡ ከሚያገለግሉትም፡ ሁለት፡ ሰዎች፡ ወደ፡ መቄዶንያ፡ ላከ። እርሳቸውም፡ *ጢሞቴዎስና፡ †ኤራስጦስ። እርሱ፡ ግን፡ በእስያ፡ አያሌ፡ ቀን፡ ተቀመጠ። *ምዕ፡ ፲፯፡ ፲፬። †ሮሚ፡ ፲፮፡ ፳፫።

፳፫፡ በዚያም፡ ወራት፡ ሁከት፡ ሆነ፡ ጥቂት፡ ያይደለ፡ ስለዚህ፡ መንገድ። ቈ፡ ፱። ፪፡ ቆሮ፡ ፩፡ ፰።

፳፬፡ አንድ፡ ሰው፡ ነበርና፡ ስሙን፡ ድሚጥሮስ፡ የሚሉት፡ ብር፡ ሰሪ። የብርም፡ ታናሽ፡ መቅደስ፡ ለአርጤምስ፡ ይሰራ፡ ነበረ፡ አንጥረኞችንም፡ *እጅግ፡ ይረባ፡ ነበር። *ምዕ፡ ፲፮፡ ፲፮።

፳፭፡ እርሱም፡ ይህነን፡ ስራ፡ የሚሰሩን፡ ሁሉ፡ ሰበሰበ፡ አላቸውም። እላንት፡ ሰዎች፡ ታውቃላችሁ፡ ጥቅማችን፡ ከዚህ፡ ስራ፡ እንደ፡ ሆነ።

፳፮፡ አይታችኋልም፡ ሰምታችኋልም፡ በኤፌሶን፡ ብቻ፡ አይደለም፡ በእስያ፡ ሁሉ፡ እንጂ። ይህ፡ ጳውሎስ፡ እጅግ፡ ሰዎች፡ እንደ፡ ረዳ፡ እንደ፡ መለሰም፡ እንደህ፡ ሲል። እሌህ፡ በጅ፡ የተሰሩ፡ አማልክት፡ አይደሉም።

፳፯፡ ይህም፡ ብቻ፡ የሚያስጨንቀን፡ አይደለም፡ ስራችን፡ የተናቀ፡ እንደ፡ ሆነ። የታላቂቱ፡ የአርጤምስ፡ መቅደስ፡ ምናምን፡ ይሆናል፡ እንጂ። ታላቅነትዋም፡ ደግሞ፡ ይቀራል፡ እስያ፡ ሁሉ፡ ዓለሙም፡ የሚያመልካት።

፳፰፡ ይህንም፡ በሰሙ፡ ጊዜ፡ ቍጣ፡ መለባቸው፡ ጮሁም፡ እንደህ፡ ሲሉ። ታላቅ፡ ናት፡ የኤፌሶን፡ አርጤምስ።

፳፱፡ አገሩም፡ ሁሉ፡ ተሸበረ፡ ሁሉም፡ ወደ፡ ጨወታ፡ ስፍራ፡ ፈጥነው፡ መጡ። ጋይዮስንና፡ አርስጠርኮስንም፡ የመቄዶንያን፡ ሰዎች፡ የጳውሎስን፡ ባልንጀሮች፡ ነጥቀው፡ ከርሳቸው፡ ጋራ፡ ወሰደ። ፪፡ ቆሮ፡ ፩፡ ፰።

፴፡ ጳውሎስ፡ ግን፡ ወደ፡ ሕዝቡ፡ ይገባ፡ ዘንድ፡ በወደደ፡ ጊዜ፡ ደቀ፡ መዛሙርት፡ አልተውትም።

፴፩፡ ሌሎችም፡ ከእስያ፡ አለቆች፡ ወደጆቹ፡ ላኩበት፡ ሲለምኑ፡ ወደ፡ ጨወታ፡ ስፍረ፡ መሔድ፡ እንደይደፈር።

፴፪፡ ሌሎችም፡ በሌላ፡ ነገር፡ ይጮሁ፡ ነበሩ፡ ጉባዔውም፡ ደንግጠው፡ ነበሩ፡ የሚበልጡትም፡ አላወቁም፡ ስለ፡ ምን፡ ተሰበሰቡ።

፴፫፡ ከሕዝቡም፡ እስክንድሮስን፡ አወጡት፡ አይሁድ፡ በፊት፡ ሲያቀሙት። እስክንድሮስ፡ ግን፡ በጁ፡ ጠቀሰ፡ ለሕዝብ፡ ይናገር፡ ዘንድ፡ ወደ።

፴፬፡ ባወቁም፡ ጊዜ፡ አይሁዳዊ፡ እንደ፡ ሆነ፡ ከሰዎች፡ ጩኸት፡ ሆነ፡ ሁለት፡ ሰዓት፡ ይሆን፡ ኢየጮሁ፡ እንደህ፡ ሲሉ። ታላቅ፡ ናት፡ አርጤምስ፡ የኤፌሶኒቱ።

፴፭፡ የአገር፡ ጸሐፊ፡ ግን፡ ሰዎችን፡ ዝም፡ አሰኛቸው፡ እንደህ፡ ሲል። እላንት፡ የኤፌሶን፡ ሰዎች፡ ማነው፡ የማያውቅ፡ ሰው፡ የኤፌሶን፡ ሰዎች፡ አገር፡ ታላቂቱን፡ አርጤምስን፡ እንድታመልክ፡ ጣዖትዋንም፡ ከሰማይ፡ የወረደውን።

፴፮፡ ይህም፡ የማይከረከረበት፡ ነገር፡ ነውና፡ ስለዚህ፡ ዝም፡ ትሉ፡ ዘንድ፡ ይገባችኋል፡ ምንም፡ በችኰላ፡ ሳታድርጉ።

፴፯፡ እሌህን፡ ሰዎች፡ አምጥታችኋልና፡ የመቅደሳችሁን፡ እቃ፡ ያልሰረቁ፡ አምላካችሁንም፡ ያልሰደቡ።

፴፰፡ ድሚጥሮስና፡ ከርሱ፡ ጋራ፡ ያሉ፡ ሰራተኞች፡ ግን፡ በማንም፡ ላይ፡ ነገር፡ እንደላቸው፡ እነሆ፡ ፍርድ፡ አለ፡ አለቆችም፡ አሉ። እርሱ፡ በርሳቸው፡ ይከራከሩ።

፴፱፡ ሌላ፡ ነገር፡ ግን፡ ትሹ፡ እንደ፡ ሆን፡ በጉባዔው፡ ይፈታል፡ እንደ፡ ሕግ፡ በሚሰበሰቡት።

፵፡ ፍርሃት፡ ነውና፡ እኛ፡ ዛሬ፡ በሆነ፡ ነገር፡ ስለ፡ ዓመፃ፡ እንከሰስ፡ ዘንድ፡ ምክንያትም፡ አልተገኘም፡ እንመልሰበት፡ የምንችል፡ ስለዚህ፡ መራወጥ። ይህነንም፡ ብሎ፡ ሕዝቡን፡ ሰደደ።

ምዕራፍ፡ ፳፡

፩፡ ሁከቱም፡ ጸጥ፡ ካለ፡ በኋላ፡ ጳውሎስ፡ ደቀ፡ መዛሙርትን፡ ጸራ፡ ከተሳለማቸውም፡ *በኋላ፡ ወደ፡ መቄዶንያ፡ ይሔድ፡ ዘንድ፡ ወጣ። *፩፡ ጢሞ፡ ፩፡ ፫።

፪፡ ያነንም፡ ስፍራ፡ በዞረ፡ ጊዜ፡ በብዙ፡ ነገርም፡ ባጸናቸው፡ ጊዜ፡ ወደ፡ ፅርዕ፡ መጣ።

፫፡ ከዚያም፡ ሶስት፡ ወር፡ ከተቀመጠ፡ በኋላ፡ ክፉ፡ ምክርም፡ ከአይሁድ፡ በርሱ፡ ላይ፡ በሆነ፡ ጊዜ፡ ወደ፡ ሶርያ፡ ለመሔድ፡ አሰቦ፡ ሳለ፡ ወደ፡ መቄዶንያ፡ ይመለስ፡ ዘንድ፡ ፈቃዱን፡ አቀመ።

፬፡ ከርሱም፡ ጋራ፡ ወጣ፡ ሶሲጳጥሮስ፡ የጲሮስ፡ ልጅ፡ *ከቤርያ። ከተሰሎንቄ፡ ወገንም፡ †አርስጠርኮስ፡ ሳኩንደስም፡ ጋይዮስም፡ ጢሞቴዎስም፡ ከደርቤ፡ ወገን፡ የሚሆን። ከእስያ፡ ወገን፡ ግን፡ ጢኪቆስ፡ ጥሮፊሞስም። *ምዕ፡ ፲፯፡ ፲። †ምዕ፡ ፲፱፡ ፳፱።

፭፡ እሌህ፡ አልፈው፡ በጥሮአስ፡ ቈዩን። ምዕ፡ ፲፮፡ ፰።

፮፡ እኛ፡ ግን፡ ከፈልጽበዩስ፡ በባሕር፡ ሔድን፡ ከፊሊ

ካ፡ወራት፡በኋላ፡ወደ፡ጥሮአስም፡መጣነ፡ከርሳቸው፡ ዘንድ፡ ሰባት፡ ቀን፡ ወደ፡ ተቀመጥነበት።

፯፡ ከሰንበታቱም፡ *በመጀመርያው፡ ቀን፡ ደቀ፡ መዛሙርት፡ ተከማችተው፡ ሳሉ፡ †እንጀራ፡ ይቈርሱ፡ ዘንድ፡ ጳውሎስ፡ ይሰብካቸው፡ ነበር። በነገው፡ የሚወጣ፡ነበርና። ነገሩንም፡አረዘመ፡እስከ፡መንፈቀ፡ ሌሊት። *፩፡ ቆር፡ ፲፮፡ ፪። †ም፡ ፪፡ ፵፪። ፵፮።

፰፡ በነበርንበትም፡ ቤት፡ ንጉሥ፡እጅግ፡ መብራት፡ ነበረ።

፱፡ አንድ፡ ብላቴናም፡ ነበረ፡ ስሙን፡ አውጢኮስ፡ የሚሉት፡ በመስኮት፡ ተቀምጦ። ታላቅ፡ እንቅልፍም፡ ወሰደው፡ ጳውሎስ፡ እጅግ፡ ነገር፡ ሲያስረዝም። እንቅልፍም፡ በበረታበት፡ ጊዜ፡ ከሦስተኛው፡ ደርብ፡ ወደ፡ታች፡ወደቀ፡ ሙቶም፡ በርሱ፡ አነሡት።

፲፡ ጳውሎስም፡ወረደ፡ በላዩም፡ *ወደቀበት፡ አቀፈውም፡ አለም። አደንግጹ፡ ነፍሱ፡ አለችና። *፩፡ ነገሥ፡ ፲፯፡ ፳፩።

፲፩፡ ደግሞም፡ወጣ፡እንጀራም፡ ቈረሰና፡ በላ፡ እጅግም፡ነገራቸው፡ እስኪጠባ። እንደህም፡ ወጣ።

፲፪፡ ብላቴናውንም፡ደህና፡ ሁኖ፡ወሰዱት፡ ጥቂት፡ ያይደለ፡ ደስታም፡ ደሳላቸው።

፲፫፡ እኛ፡ ግን፡ ወደ፡ መርከብ፡ መጣነ፡ ወደ፡ አሶስም፡ ሰረርነ። ከዚያም፡ ጳውሎስን፡ እንወስደው፡ ዘንድ፡አሰብነ። እንደሁ፡ነግሮነ፡ነበርና፡በግሩ፡ይሔድ፡ ዘንድ፡ አስቦ።

፲፬፡ በአሶስም፡ ባገኘነው፡ ጊዜ፡ ወሰድነው፡ ወደ፡ ሚጢሊኒም፡ ይዘነው፡ መጣነ።

፲፭፡ ከዚያም፡ በባሕር፡ ሰረርነ፡ በሚመጣውም፡ ቀን፡በኪዩስ፡ፊት፡መልሕቅ፡ጣልነ። በነገውም፡ ወደ፡ ሳሞስ፡መጣነ፡ በትሮጊሊዮም፡ተቀመጥነ፡ ከዚያም፡ በኋላ፡ወደ፡ ሚሌጦስ፡ ደረስነ።

፲፮፡ ጳውሎስ፡ከኤፌሶን፡ ርቀ፡ያልፍ፡ ዘንድ፡ ወድዋልና፡እጅግ፡ዘመን፡እንዳይቀመጥ፡በእስያ። ይፈጥን፡ነበርና፡ ቢቻለው፡ የጰንጠቆስጤን፡ ቀን፡ በየሩሳሌም፡ ይውል፡ ዘንድ። ም፡ ፲፰፡ ፳፩። ፳፩፡ ፬፡ ፲፪።

፲፯፡ ከሚሌጦስም፡ወደ፡ኤፌሶን፡ ላከ፡ የቤተ፡ ክርስቲያኒቱንም፡ ሽማግሎችን።

፲፰፡ ወደርሱም፡በመጡ፡ጊዜ፡አላቸው። እላንተ፡ ታውቃላችሁ፡ወደ፡እስያ፡ ከገባሁበት፡ከመጀመርያ፡ ቀን፡ ጀምሬ፡ እንደት፡ ነበርሁ፡ ከላንተ፡ ጋራ፡ ዘመን፡ ሁሉ። ም፡ ፲፰፡ ፲፱። ፲፱፡ ፲።

፲፱፡ እግዚአብሔርን፡አገለግል፡ ነበርሁና፡ በትሕትና፡ሁሉ፡በብዙ፡እንባም፡በደረሰብኝም፡ፈተና፡በአይሁድ፡ መሸጉጥ። ቍ፡ ፫።

፳፡ ከሚጠቅማላችሁም፡ ነገር፡ አንዳች፡ አላስቀረሁም፡ እነግራችሁ፡ አስተምራችሁም፡ ነበርሁ፡ አንጂ፡ በጉባዔም፡ በቤትም።

፳፩፡ ስመሰክር፡ ለአይሁድ፡ ለአረማውያንም፡ወደ፡እግዚአብሔር፡ በመመለስ፡ በጌታችንም፡ በየሱስ፡ ክርስቶስ፡ በማመን።

፳፪፡ አሁንም፡እኔ፡በመንፈስ፡ቅዱስ፡ ታሥሬ፡ እኑሆ፡ወደ፡የሩሳሌም፡ እሔዳለሁ፡ በርሰዋ፡ ምን፡ የሚሆንብኝን፡ ሳላውቅ። ም፡ ፲፰፡ ፳፩። ፲፱፡ ፳፩።

፳፫፡ መንፈስ፡ቅዱስ፡ግን፡ባገሩ፡ሁሉ፡ ይመሰክርልኛል፡እንደህ፡ ሲል። እሥራትና፡ መከራ፡ ይቈይሃል። ም፡ ፱፡ ፲፮። ፳፩፡ ፬፡ ፲፩።

፳፬፡ ደሮ፡ግን፡ ይህን፡ ምክንያት፡ አድርጌ፡ አልቈጥረውም። ነፍሴም፡ ደግሞ፡ በኔ፡ ዘንድ፡ እንድትከበር፡አላስብም፡ሩጫዬን፡እስክፈጽም፡ድረስ፡በደስታ፡ መልእክቴንም፡ከጌታ፡ከየሱስ፡ የተቀበልኋትን፡በእግዚአብሔር፡ ጸጋ፡ ወንጌልን፡ እመሰክር፡ ዘንድ። ም፡ ፳፩፡ ፲፫።

፳፭፡ አሁንም፡እነሆ፡ እኔ፡አውቃለሁ፡ ሁላችሁ፡ደግሞ፡ፊቴን፡እንደታዩ። እላንተ፡የዞርኋችሁ፡ የእግዚአብሔርን፡ መንግሥት፡ ሳስተምራችሁ።

፳፮፡ ስለዚህም፡ እኔ፡ እመሰክርላችኋለሁ፡ በዚህ፡ ቀን፡ ንጹህ፡ እንደ፡ ሆንሁ፡ ከሁላችሁ፡ ደም። ም፡ ፲፰፡ ፮።

፳፯፡ የእግዚአብሔርን፡ ምክር፡ ሁሉ፡ እላንተን፡ ከማስተማር፡ አልተውሁምና።

፳፰፡ አሁንም፡ለራሳችሁ፡ተጠንቀቁ፡ለመንጋውም፡ሁሉ፡ መንፈስ፡ ቅዱስ፡ በርሱ፡ላይ፡ ጠባቆች፡ አድርጎ፡የሾማችሁ፡የእግዚአብሔርን፡ ቤተ፡ ክርስቲያን፡ ትጠብቁ፡ ዘንድ፡ እርሱ፡ በደሙ፡ የዋጃትን። ፩፡ ጢሞ፡ ፬፡ ፲፮። ፩፡ ጴጥ፡ ፭፡ ፪።

፳፱፡ ይህን፡እኔ፡አውቃለሁና፡ ከሔድሁ፡ በኋላ፡የሚያጠቁ፡ *ጅቦች፡ እንዲገቡባችሁ፡ ለመንጎች፡ የማያዝኑ። *ማቴ፡ ፯፡ ፲፭።

፴፡ ከበውሥጣችሁም፡የሚነሡ፡ሰዎች፡ አሉ፡ጠማማ፡ ነገር፡የሚናገሩ፡ደቀ፡መዛሙርትን፡ ወደ፡ ኋላቸው፡ይስቡ፡ ዘንድ።

፴፩፡ ስለዚህም፡ ንቁ፡ አስባችሁ፡ እንደልተውሁ፡ ሦስት፡አመት፡ሌትና፡ቀን፡እላንተን፡በንብ፡ ከማስተማር፡ ካላንት፡ ኢያንደንደችሁ።

፴፪፡ አሁንም፡ ውንድሞቼ፡ ለእግዚአብሔር፡ አደራ፡ሰጥቻችኋለሁ፡ለጸጋውም፡ነገር፡ ይሰራችሁ፡ ዘንድ፡የሚችል፡ርስትም፡ይሰጣችሁ፡ ዘንድ፡ ከቅዱሳን፡ ሁሉ፡ጋራ።

፴፫፡ ወርቅ፡ግን፡ብርም፡ሆነ፡ልብስም፡ ሆነ፡ ከማንም፡ አልሻሁም። ማቴ፡ ፲፡ ፰። ፩፡ ቆር፡ ፱፡ ፲፪። ፩፡ ሳሙኤ፡ ፲፪፡ ፫።

፴፬፡ እላንትም፡ ታውቃላችሁ፡ እሌህ፡ እጆቼ፡ ለምሻው፡ነገር፡ከኔ፡ ጋራ፡ ላሉትም፡ እንደገለገሉ። ም፡ ፲፰፡ ፫። ፩፡ ቆር፡ ፬፡ ፲፪። ፩፡ ተሰ፡ ፪፡ ፱።

፴፭፡ ሁሉንም፡ገለጥሁላችሁ። እንደሁ፡እንዲገባችሁ፡ ትሰሩ፡ ዘንድ፡ ለደካሞችም፡ ረዲት፡ ትሰጡ፡ ዘንድ፡ የጌታን፡ የየሱስን፡ ቃል፡ አስባችሁ። እርሱ፡ብል

ዋልና። ከሚወስድ፡ ይልቅ፡ለሚሰጥ፡ ምስጋና፡ ይገባዋል።

፴፮፤ ይህነንም፡ ባለ፡ ጊዜ፡ በጕልበቱ፡ ተንበረከከ፡ ከሁሉ፡ ጋራ፡ *ጸለየም። *ም፡ ፳፩፡ ፭፡፡

፴፯፤ ከሁሉም፡እጅግ፡ ልቅሶ፡ ሆነ፡ በጳውሎስም፡ አንገት፡ላይ፡ወድቀው፡ይስሙት፡ ነበረ።

፴፰፤ ይልቁን፡ አዝነው፡ ባለው፡ ነገር፡ እንግዲህ፡ ደግሞ፡ ፊቴን፡ አታዩም። እስከ፡ መርከብም፡ ድረስ፡ ሸኙት።

## ምዕራፍ፡ ፳፩፤

፩፤ ከርሳቸውም፡ከተለየነ፡በኋላ፡ እኛ፡ ሰረርነ፡ መንገዳችነንም፡አቅንተን፡ወደ፡ቆስ፡መጣነ፡ በነገውም፡ ወደ፡ ሮደስ፡ ከዚያም፡ ወደ፡ ጳጥራ።

፪፤ ወደ፡ ፊንቄም፡ የሚያልፍ፡ መርከብ፡ አገኘነ፡ በርሱም፡ ተቀመጥነና፡ ሔድነ።

፫፤ ቆጵሮስም፡ ባየነ፡ ጊዜ፡ በግራችን፡ ተውናት፡ ወደ፡ ሶርያም፡ ሔድነ፡ ወደ፡ ጢሮስም፡ መጣነ። ከዚያ፡ መርከብ፡ ሸክሙን፡ የሚገለብጥ፡ ነበረና።

፬፤ ደቀ፡መዛሙርትንም፡ባገኘነ፡ጊዜ፡ ከርሳቸው፡ ዘንድ፡ተቀመጥነ፡ሰባት፡ቀን። እርሳቸውም፡በመንፈስ፡ጳውሎስን፡አሉት፡ወደ፡የሩሳሌም፡እንዳይወጣ። ቍ፡ ፲፩፡ ፲፪፡፡ ም፡ ፳፡ ፳፫፡፡

፭፤ ጊዜያችነንም፡ ፈጽመን፡ በተቀመጥነ፡ ጊዜ፡ ወጣነ፡ሔድነም። እርሳቸውም፡ሁሉ፡ ሸኙነ፡ ከሴቶቻቸው፡ ከልጆቻቸውም፡ ጋራ፡ እስካገሩ፡ ሚደ፡ ድረስ። ተንበረከክነም፡ በባሕር፡ ዳር፡ ጸለይነም። ም፡ ፳፡ ፴፮፡፡

፮፤ እርሱ፡በርሳችንም፡ተሰነባበትነ፡ወደ፡ መርከብም፡ ሰረርነ። እሊያም፡ ወደ፡ ቤታቸው፡ ተመለሱ።

፯፤ እኛ፡ግን፡ከጢሮስ፡ተነሥተን፡የባሕሩን፡ መንገድ፡በፈጸምነ፡ጊዜ፡ ወደ፡ጵቶሌማይስ፡ ወጣነ። ወንድሞችንም፡ እንዴት፡ ናችሁ፡ አልነ፡ ከርሳቸውም፡ ዘንድ፡ አንድ፡ ቀን፡ ተቀመጥነ።

፰፤ በነገውም፡ ወጥተን፡ ወደ፡ቂሣርያ፡ መጣነ፡ ወደ፡ ወንጌላዊውም፡ ወደ፡ ፊልጶስ፡ ቤት፡ ገባነ። እርሱም፡ ከሰባቱ፡ አንድ፡ የሚሆን። ወደርሱም፡ ተቀመጥነ። ም፡ ፰፡ ፵፡፡

፱፤ ለዚህም፡ አራት፡ ሴቶች፡ ልጆች፡ ደናግል፡ ነበሩት፡ ትንቢት፡ የሚናገሩ። ም፡ ፪፡ ፲፯፡፡

፲፤ ከዚያም፡ እጅግ፡ ቀን፡ በተቀመጥነ፡ጊዜ፡ ከአይሁድ፡ አገር፡ ነቢይ፡ ሰው፡ወረደ፡ስሙን፡ *አጋቦስ፡የሚሉት። *ም፡ ፲፩፡ ፳፰፡፡

፲፩፤ ወደኛም፡ መጣ፡የጳውሎስንም፡ መቀነት፡ ወስዶ፡ እጁንና፡እግሩንም፡አሠረበት፡አለም። ይህነን፡ ነገር፡ ይላል፡ መንፈስ፡ ቅዱስ። የዚህን፡ መቀነት፡ ባለቤት፡ ሰው፡ እንዲሁ፡ አይሁድ፡ ያሥሩታል፡ በየሩሳሌም፡ ለአሕዛብም፡ እጅ፡ አሳልፏ፡ ይሰጡታል። ም፡ ፳፡ ፳፫፡፡

፲፪፤ ይህነንም፡ ነገር፡ በሰማነ፡ ጊዜ፡ እኛ፡ ያገሩም፡ ሰዎች፡ ለመነው፡ ወደ፡ የሩሳሌም፡ እንዳይወጣ። ም፡ ፲፯፡ ፳፪፡፡

፲፫፤ ጳውሎስም፡ መለሰ፡ አለም። ምን፡ ታደርጋላችሁ፡ ለምንስ፡ ታለቅሳላችሁ፡ ልቤንም፡ ትሰብሩታላችሁ። እኔ፡የጨከንሁ፡ነኝና፡ ለሥራት፡ብቻ፡ አይደለም፡ ለሞትም፡ እንጂ፡ በየሩሳሌም፡ ስለ፡ ጌታ፡ ስለ፡ የሱስ፡ ስም። ም፡ ፳፡ ፳፬፡፡

፲፬፤ ባይታዘዘነም፡ ዝምማልነ፡ እንዲህ፡ ስንል። የጌታ፡ ፈቃድ፡ ትሁን።

፲፭፤ ከዚያችም፡ ቀን፡ በኋላ፡ የተዘጋጀነ፡ ወደ፡ የሩሳሌምም፡ ወጣነ።

፲፮፤ ከኛም፡ ጋራ፡ ደግሞ፡ ሰዎች፡ ከደቀ፡ መዛሙርት፡ ወገን፡ ከቂሣርያ፡ መጡ፡ አንድም፡ ሰው፡ ከነርሳቸው፡ ጋራ፡ አመጡ፡ምናሶንን፡ የቆጵርያኖሱን፡ የሸመገለ፡ ደቀ፡ መዝሙር፡ ከርሱ፡ ዘንድ፡ ያደርነ።

፲፯፤ ወደ፡ የሩሳሌምም፡ በደረስነ፡ ጊዜ፡ ወንድሞች፡ በደስታ፡ ተቀበሉነ።

፲፰፤ በነገውም፡ ጳውሎስ፡ከኛ፡ጋራ፡ ወደ፡ ያዕቆብ፡ ገባ፡ ሽማግሎችም፡ ሁሉ፡ ከዚያ፡ ነበሩ። ም፡ ፲፭፡ ፲፫፡፡ ገላት፡ ፩፡ ፲፱፡፡

፲፱፤ በተገናኘቸውም፡ ጊዜ፡ አጫወታቸው፡ ኢያንዳንዲቱ፡ እግዚአብሔር፡ ካደረገት፡ ስራ፡ በአሕዛብ፡ መካከል፡ በማገልገሉ።

፳፤ እርሳቸውም፡ ይህነን፡ በሰሙ፡ ጊዜ፡እግዚአብሔርን፡አመሰገኑ፡አሉትም።ታያለህ፡ወንድም፡ሆይ፡ ስንት፡ አእላፋት፡ናቸው፡ ከአይሁድ፡ያመኑ፡ እርሳቸውም፡ ሁሉ፡ ለኦሪት፡ የሚቀኑ፡ ናቸው። ም፡ ፲፭፡ ፩፡፡

፳፩፤ ስላንተም፡ ሰምተዋል፡በአሕዛብ፡ መካከል፡ ያሉትን፡ አይሁድን፡ ሁሉ፡እንድታስተምር፡ከሙሴ፡ ሥርዓት፡ ይርቁ፡ ዘንድ፡ እንዲህ፡ ኢያልህ። ልጆቻቸውን፡እንዳይገዝሩ፡በሕግም፡እንዳይሔዱ። ም፡ ፲፯፡ ፫፡፡ ሮሜ፡ ፲፡ ፬፡፡

፳፪፤ እንግዲህስ፡ምን፡ይሁን። የግድ፡ሕዝብ፡ሳይሰበሰቡ፡አይቀሩም። አንተ፡ እንደ፡ መጣህ፡ ይሰማሉና።

፳፫፤ አሁንም፡ይህነን፡የምንልህን፡አድርግ።ከኛ፡ዘንድ፡አራት፡ሰዎች፡አሉ፡በራሳቸው፡ስለት፡ያለባቸው።

፳፬፤ እሌህንም፡ ውሰድና፡ ከርሳቸው፡ ጋራ፡ ንጻ፡ ገንዘብን፡ ስትሰጣቸው፡ራሳቸውን፡እንዲላጩ። እንዲህም፡ የሆነ፡ እንደ፡ ሆን፡ ሁሉ፡ ያውቃሉ፡ ስላንተ፡ የመጣላቸው፡ ወሬ፡ ሁሉ፡ አበት፡ እንደ፡ ሆነ፡ አንተ፡ እንደ፡ ተስማማህ፡ እንጂ፡ ሐግንም፡ ጠባቂ፡ እንደ፡ ሆንህ። ም፡ ፲፰፡ ፲፰፡፡

፳፭፤ ስላመኑት፡ አሕዛብ፡ ግን፡ እኛ፡ ላክነላቸው፡ አዘዝናቸውም፡ እንዲህ፡ ያለ፡ ነገር፡ እንዳይጠብቁ፡ ስውነታቸውን፡ ከመጠበቅ፡ በቀር፡ለጣዖት፡ ከታረደው፡ ከደምም፡ ከታነቀውም፡ ከዝሙትም። ም፡ ፲፭፡ ፳፡ ፳፱፡፡

፳፯፡ የዚያን፡ጊዜም፡ጳውሎስ፡ ሰዎችን፡ ወሰደ፡ በነገውም፡ ነጽ፡ ከርሳቸው፡ ጋራ፡ ወደ፡ መቅደስም፡ ገባ፡ኢያወራ፡የመንጻቱን፡ ቀን፡ ፍጻሜ፡ ስለ፡ ሁሉ፡ ኢያንደንደቸው፡ *መሥዋዕት፡ እስኪሠው፡ ድረስ። *ዘኁ፡ ፮፡ ፲፫።

፳፰፡ ሰባቱ፡ቀንም፡ ይፈጸም፡ ዘንድ፡በቀረበ፡ጊዜ፡ ከእስያ፡ የመጡ፡ አይሁድ፡ በመቅደስ፡ አዩት፡ሰዎችንም፡ ሁሉ፡ አወኩ፡ እጃቸውንም፡ ጣሉበት።

፳፱፡ ኢየጮሁ፡ እንደህም፡ኢያሉ። እላንተ፡ሰዎች፡ የእሥራኤል፡ ወገን፡ እርዱ። ይህ፡ ነው፡ ሁሉን፡ ያሚያስተምር፡ ሰው፡በየስፍራው፡ሕዝባችንን፡የሚጣላ፡ ትምህርት፡ኦሪትንም፡ይህንም፡ስፍራ። የናውያንንም፡ ደግሞ፡ ወደ፡ መቅደስ፡ አገባ፡ ይህንም፡የተቀደሰ፡ስፍራ፡አረከሰው። ም፡፮፡፲፫። ሕዝ፡ ፵፬፡፯።

፴፡ አስቀድመው፡ *ጥሮፊሞስን፡የኤፌሶኑን፡ ባገር፡ ከርሱ፡ ጋራ፡ አይተው፡ ነበረና፡ ጳውሎስም፡ ወደ፡ መቅደስ፡ ያገባው፡ መሰላቸው። *ም፡ ፳፡ ፬። ፪፡ ጢሞ፡ ፬፡ ፳።

፴፩፡ ምሉው፡ አገር፡ ሁሉም፡ ታወከ፡ የሕዝብም፡ ሁሉ፡ መራወጥ፡ሆነ። ጳውሎስንም፡ ያዙት፡ ከመቅደስ፡ ወደ፡ ሜዳም፡ አወጡት፡ የዚያን፡ ጊዜውም፡ ደጆ፡ ሁሉ፡ ተዘጋ።

፴፪፡ እርሳቸውም፡ ሊገሉት፡ ሲሹ፡ ወደ፡የሻለቃው፡ በጭፍራ፡ ላይ፡ የተሾመ፡ወሬ፡ደረሰ፡የሩሳሌም፡ ፈጽማ፡ እንደ፡ ታወከች።

፴፫፡ እርሱም፡ በዚያው፡ጊዜ፡ ጭፍራ፡የመቶ፡አለቆችም፡ ወሰደ፡ ሲሮጥም፡ ደረሰባቸው። እርሳቸው፡ ግን፡ የሻለቃውን፡ ጭፍሮችንም፡ ባዩ፡ ጊዜ፡ ጳውሎስን፡ ከመምታት፡ ተውት።

፴፬፡ የዚያን፡ጊዜም፡ የሻለቃው፡ ወደርሱ፡ ቀረበ፡ ያዘውም፡ በሁላት፡ ሰንሰለትም፡ ይታሠር፡ ዘንድ፡ አዘዘ፡ ጠየቀም፡ ማን፡ እንደ፡ ሆነ፡ ምንስ፡ አደረገ።

ም፡ ፳፡ ፳፫።

፴፭፡ ከሕዝቡም፡ አንዱ፡ ይህን፡ሌላውም፡ ያነን፡ ነገር፡ ጮኸ። እርግጡን፡ ማወቅ፡ ባይቻለው፡ ስለ፡ ጩኸቱ፡ ብዛት፡ ወደ፡ደራሹ፡ ይወስዱት፡ ዘንድ፡ አዘዘ።

፴፮፡ ወደ፡ መውጫውም፡በደረሰ፡ጊዜ፡ጭፍሮች፡ እንደ፡ ተሸከሙት፡ ሆነ፡ ስለ፡ ሕዝቡ፡ ጭንቀት።

፴፯፡ የሕዝብ፡ ብዛት፡ ይከተሉት፡ ነበርና፡ ኢየጮሁ፡ እንደህም፡ ኢያሉ። አስነሣው።

፴፰፡ ወደደራሹም፡ ሲወስዱት፡ ጳውሎስ፡ የሻለቃውን፡ አለው። ትፈቅድልኛለህን፡ አንድ፡ ነገር፡ ብነግርህ። እርሱም፡ አለ። የፅርዕ፡ ቋንቋ፡ ታውቃለህን።

፴፱፡ አንተ፡ የምሥር፡ ሰው፡ አይደለህምን፡ ከዚህ፡ ዘመን፡ አስቀድመህ፡ ሁከት፡ ያደርገህ፡ ወደ፡ ምድረ፡ በዳስ፡ አራት፡ ሺህ፡ በተንኰል፡ ገዳዮችን፡ ያወጣህ።

፵፡ ጳውሎስም፡ አለ። እኔስ፡ አይሁዳዊ፡ ሰው፡ ነኝ፡ አገሬም፡ *ጠርሴስ፡ ነው፡ የከበረ፡ ከተማ፡ የሚሆን፡በኪልቅያ፡ ምድር። እለምንሃለሁ፡ እንድትታወኝ፡ ለሕዝቡ፡ እነግር፡ ዘንድ። *ም፡ ፱፡ ፲፩።

፵፩፡ በተወለትም፡ጊዜ፡ጳውሎስ፡በመድረኩ፡ላይ፡ ቆመ፡ ሕዝቡንም፡ በጁ፡ ጠቀሰ። እጅግም፡ ጸጥታ፡ በሆነ፡ ጊዜ፡በዕብራይስጥ፡ቋንቋ፡ ነገራቸው፡እንደህ፡ ሲል። ም፡ ፲፪፡ ፲፯። ፲፫፡ ፲፮። ፲፱፡ ፴፫።

ምዕራፍ፡ ፳፪።

፩፡ እላንተ፡ሰዎች፡ወንድሞች፡አባቶችም፡ ነገሬን፡ ስሙ፡ ዛሬ፡ ለላንተ፡ ስለ፡ ሰውነቴ፡ የምነግራችሁን።

ም፡ ፯፡ ፪። ፲፫፡ ፳፮።

፪፡ በሰሙም፡ጊዜ፡ በዕብራይስጥ፡ ቋንቋ፡ እንደ፡ ነገራቸው፡ ጸጥታ፡ አበዙ። እርሱም፡ አለ።

ም፡ ፳፩፡ ፵።

፫፡ እኔ፡ አይሁዳዊ፡ ሰው፡ ነኝ፡ በጠርሴስ፡ አገር፡ በ ቂልቅያ፡ ምድር፡ የተወለድሁ፡ በዚቺም፡ አገር፡ ያደ ግሁ፡ ከገማልዬል፡ እግር፡በታች። ባባቶችን፡ሕግ፡ በጣም፡ ተምሬ፡ ለእግዚአብሔር፡ ቅናተኛ፡ ሆንሁ፡ እንደላንተ፡ እንደ፡ ሁላችሁ፡ ዛሬ። ም፡ ፭፡ ፴፬።

ም፡ ፱፡ ፩—፳፪። ፳፮፡ ፱—፲፭።

፬፡ በዚህ፡መንገድም፡የሚሔዱን፡ሰዎች፡ እስከ፡ ሞት፡ ድረስ፡ አስጨነቅሁ፡ አሠርሁም፡ ወደ፡ ግዞትም፡ አመጣሁ፡ ወንዶችንም፡ ሴቶችንም።

ም፡ ፰፡ ፫።

፭፡ እንደ፡ መሰከርልኝ፡ ደግሞ፡ የካህናቱ፡ አለቃ፡ ሽማግሎችም፡ ሁሉ። ከርሳቸው፡ ወደ፡ ወንድሞች፡ መልእክት፡ ተቀበልሁ፡ ወደ፡ ደማስቆም፡ ሔድሁ፡ ከዚያ፡ ያሉትን፡ አሥሬ፡ ወደ፡ የሩሳሌም፡ ላመጣ፡ ይሣቀዩ፡ ዘንድ።

፮፡ ስሔድም፡ ወደ፡ ደማስቆም፡ *ስቀርብ፡ በቀትር፡ ጊዜ፡ ድንገት፡ ታላቅ፡ ብርሃን፡ በዙርያዩ፡ በራ።

*ም፡ ፱፡ ፫—፲፮። ፩፡ ቆሮ፡ ፲፭፡ ፰።

፯፡ በምድርም፡ ላይ፡ ወደቅሁ፡ እንደህ፡ የሚለኝንም፡ ድምጽ፡ ሰማሁ። ሳውል፡ ሳውል፡ ለምን፡ ታሳደኛለህ። ም፡ ፳፮፡ ፲፬፡ ፲፭።

፰፡ እኔም፡ መለስሁ፡ አልሁም፡ አንተ፡ማነህ፡አቤቱ። አለኝም። እኔ፡ ነኝ፡ የቡስ፡ የናዝሬቱ፡ አንተ፡ የምታሳደኝ።

፱፡ *ከኔ፡ ጋራ፡ የነበሩት፡ ግን፡ ብርሃኑን፡ አዩ፡ እጅግም፡ ፈሩ። የሚናገረኝን፡ ድምጽ፡ ግን፡ አልሰሙም።

*ም፡ ፱፡ ፯።

፲፡ አልሁም። ምን፡ልስራ፡ አቤቱ። ጌታም፡ አለኝ። *ተነሥተህ፡ወደ፡ደማስቆ፡ ሒድ። ከዚያም፡ ላንተ፡ ይገላል፡ የተሠራልህን፡ ሁሉ፡ ታደርገው፡ ዘንድ።

*ም፡ ፱፡ ፮።

፲፩፡ ማየትም፡ አጥቼ፡ ከዚያ፡ ብርሃን፡ ብልጭታ፡ የተነሣ፡ ከኔ፡ ጋራ፡ የነበሩ፡ ሰዎች፡ ሲመሩኝ፡ ወደ፡ ደማስቆ፡ መጣሁ።

፲፪፡ አንድ፡ ሰውም፡ ስሙን፡ ሐናንያ፡ የሚሉት፡

እግዚአብሔርን፡ የሚፈራ፡ እንደ፡ ሕጉ፡ ከአይሁድ
ም፡ ከዚያ፡ የሚኖሩ፡ መልካም፡ የተመሰከረለት።
፲፫፡ እርሱ፡ወደኔ፡መጣ፡በፊቴም፡ቆሞ፡አለኝም።
ወንድሜ፡ ሆይ፡ ሳውል፡ እይ። እኔም፡ በዚያች፡ ጊዜ፡
ወደርሱ፡ አየሁ።
፲፬፡ እርሱም፡ አለ። ያባቶቻችን፡ አምላክ፡ አስቀ
ድሞ፡ *መረጠህ፡ ፈቃዱን፡ ታውቅ፡ ዘንድ፡ ጻድቁን
ም፡ ታይ፡ ዘንድ፡ ካፉም፡ ድምጽ፡ ትሰማ፡ ዘንድ።
*ም፡ ፱፡ ፲፭።
፲፭፡ በሰውም፡ ሁሉ፡ ፊት፡ ምስክር፡ ትሆንለታለ
ህ፡ ባየኸው፡ በሰማኸውም፡ ሥራ፡ ሁሉ።
፲፮፡ አሁንስ፡ ምን፡ ትዘገያለህ። ተነሣና፡ ተጠመ
ቅ፡ኃጢአትህንም፡ ታጸብ፡ የጌታን፡ ስም፡ ስትጸራ።
፲፯፡ ሆነም፡ ወደ፡ የሩሳሌም፡ *በተመለስሁ፡ ጊዜ፡
በመቅደስም፡ በጸለይሁ፡ ጊዜ፡ በራእይ፡ ተነጥቄ።
*ም፡ ፱፡ ፳፮።
፲፰፡ እርሱን፡ አየሁ፡ የሚለኝን። ከየሩሳሌም፡ ቶ
ሎ፡ ውጣ፡ ለኔ፡ የምትመሰክረውን፡ አይቀበሉህ
ምና።
፲፱፡ እኔም፡ አልሁ። አቤቱ፡ እርሳቸው፡ ያውቃሉ፡
በመስጊድ፡ ሁሉ፡ እኔ፡ እመታ፡ አሥርም፡ እንደ፡ ነበ
ርሁ፡ ባንተ፡ የሚያምኑን። ቍ፡ ፬።
፳፡ የሰማዕትህም፡ የእስጢፋኖስ፡ ደም፡በፈሰሰ፡
ጊዜ፡እኔ፡ ከርሳቸው፡ ጋራ፡ ቁሜ፡ ደስታዬን፡ በሞቱ፡
አየሁ፡ የገደሉትንም፡ ልብስ፡ *እጠብቅ፡ ነበርሁ።
*ም፡ ፯፡ ፶፯። ፰፡ ፩።
፳፩፡ አለኝም። ሒድ፡ እኔ፡ እልክሃለሁና፡ ሩቅ፡ አ
ገር፡ ወደ፡ አሕዛብ። ም፡ ፱፡ ፲፭። ፲፫፡ ፪።
፳፪፡ እርሱንም፡ ሰሙት፡ እስከዚህ፡ ቃል፡ ድረስ።
ድምጻቸውንም፡ አነሡ፡ ተግብረው፡ እንዲህ፡ ሲሉ።
እንዲህ፡ ያለውን፡ ከምድር፡ አስነሣው። አይገባው
ምና፡ ይኖር፡ ዘንድ። ም፡ ፳፩፡ ፴፮።
፳፫፡ እርሳቸውም፡ ሲጮሁ፡ ልብሳቸውንም፡ ሲጥ
ሉ፡ ትቢያም፡ ወደ፡ ነፋስ፡ ሲበትኑ።
፳፬፡ የሻለቃው፡ አዘዘ፡ ወደደራሽ፡ ይወስዱት፡ ዘ
ንድ፡ በመግረፍያም፡ እንዲመረምሩት፡ ያውቅ፡ዘን
ድ፡ በምን፡ ምክንያት፡ እንዲህ፡ ይጮሁበታል።
፳፭፡ ለመግረፍም፡ የፍጥኝ፡ ባሠሩት፡ ጊዜ፡ ጳው
ሎስ፡ ለመቶው፡ አለቃ፡ለማስገረፍ፡ቁሞ፡ ለነበረው፡
አለ። *ይገባችኋልን፡ የሮምን፡ ሰው፡ ትገርፉ፡ ዘንድ፡
ያልተፈረደበትን። *ም፡ ፲፮፡ ፴፯። ፳፫፡ ፳፯።
፳፮፡ የመቶው፡ አለቃም፡ በሰማ፡ ጊዜ፡ መጣ፡ ለሻ
ለቃውም፡ ነገረው፡ እንዲህ፡ ሲል። ምን፡ ትሻለህ፡ ታ
ደርግ፡ ዘንድ። ይህ፡ ሰው፡ ሮማዊ፡ ነውና።
፳፯፡ የሻለቃውም፡ ወደርሱ፡ ቀረበ፡ አለውም። ን
ገረኝ፡ አንተ፡ ሮማዊ፡ እንደ፡ ሆንህ። እርሱም፡ አለ።
አዎን።
፳፰፡ የሻለቃውም፡ መለሰ፡ አለም። እኔ፡ በብዙ፡
ከብት፡ ይህነን፡ የሮምን፡ የባላባትነት፡ ሥልጣን፡ ገዛ
ሁት። ጳውሎስም፡ አለ። እኔ፡ ግን፡ በርስዋ፡ ተወለ
ድሁ።
፳፱፡ የዚያን፡ ጊዜም፡ ከርሱ፡ ራቁ፡ ይመቱት፡ የነበ
ሩት። የሻለቃውም፡ ደግሞ፡ ፈራ፡ በሰማ፡ ጊዜ፡ ሮማ
ዊ፡ እንደ፡ ሆነ፡ ስላሠረውም።
፴፡ በነገውም፡ የሰራውን፡ ነገር፡ አስረግጦ፡ ሊያው
ቅ፡ በወደደ፡ ጊዜ፡ ስለ፡ ምንስ፡ ከአይሁድ፡ እንደ፡ ተ
ከሰሰ፡ እርሱን፡ ከሥራቱ፡ ፈታው፡ የካህናቱ፡ያለቆች
ም፡ ከጉባዔው፡ ሁሉ፡ ጋራ፡ ይመጡ፡ ዘንድ፡ አዘዘ።
ጳውሎስንም፡ አሰወርዶ፡ በፊታቸው፡ አቆመው።

## ምዕራፍ፡ ፳፫፡

፩፡ ጳውሎስም፡ ጉባዔውን፡ አጽንቶ፡ ኢያየ፡ አለ።
እላንት፡ ወንድማማች፡ ሰዎች፡ እኔ፡ *በመልካም፡
ሕሊና፡ ሁሉ፡ በእግዚአብሔር፡ ፊት፡ ኖርሁ፡ እስከ፡
ዛሬ፡ ድረስ። *ም፡ ፳፬፡ ፲፮።
፪፡ ሐናንያ፡ የካህናቱ፡ አለቃ፡ግን፡በፊቱ፡ቁመው፡
የነበሩትን፡ አዘዘ፡ አፉን፡ ይመቱት፡ ዘንድ።
፫፡ የዚያን፡ ጊዜም፡ ጳውሎስ፡ አለው። እግዚአ
ብሔር፡ ይመጣሃል፡ አንተ፡ የተለሰንህ፡ ግድግዳ። አ
ንተ፡ ተቀምጠህን፡ በሥርዓት፡ ትፈርድብኛለህ፡ያለ፡
ሥርዓትስ፡ ታዛለህ፡ እመታ፡ ዘንድ።
፬፡ የቆሙት፡ ግን፡ አሉ። የእግዚአብሔርን፡ ካህና
ት፡ አለቃንን፡ ትሰድባለህ።
፭፡ ጳውሎስም፡ አለ። አላወቅሁም፡ ወንድሞቼ፡
ሆይ፡ የካህናት፡ አለቃ፡ እንደ፡ ሆነ። *ተጽፎዋልና፡ የ
ሕዝብህን፡ አለቃ፡ አትስድብ፡ ተብሎ።
*ዘፀአ፡ ፳፪፡ ፳፰። ፪፡ ጴጥ፡ ፪፡ ፲።
፮፡ ጳውሎስም፡ ባወቀ፡ ጊዜ፡ እኩሌታቸው፡ ሰዱ
ቃውያን፡ እኩሌታቸውም፡ ፈሪሳውያን፡ እንደ፡ ሆኑ፡
በሸንጎው፡ መካከል፡ ጮኸ፡ እንዲህ፡ ሲል። እላንት፡
ወንድማማች፡ ሰዎች። እኔ፡ *ፈሪሳዊ፡ ልጅ፡ ነኝ። ስለ፡
ተስፋው፡ ስለ፡ ሙታንም፡ ትንሣኤ፡ በኔ፡ ይፈረድብ
ኛል። *ም፡ ፳፮፡ ፭።
፯፡ ይህነንም፡ ባለ፡ ጊዜ፡ መለየት፡ ሆነ፡ በፈሪሳው
ያንና፡ በሰዱቃውያን፡ መካከል፡ ጉባዔውም፡ ተከ
ፈለ።
፰፡ *ሰዱቃውያን፡ ይላሉና፡ ትንሣኤ፡ የለም፡ መ
ልአክም፡ መንፈስም። ፈሪሳውያን፡ ግን፡ በዚህ፡ ሁ
ሉ፡ ያምናሉ። *ማቴ፡ ፳፪፡ ፳፫።
፱፡ ታላቅም፡ ጩኸት፡ ሆነ። የፈሪሳውያንም፡ ወገ
ን፡ ጸፎች፡ ተነሡ፡ ስለርሱም፡ ተጣሉ፡ እንዲህ፡ ሲሉ።
በዚህ፡ ሰው፡ *ክፉ፡ ነገር፡ አናገኝም። መንፈስ፡ ነግሮ
ት፡ እንደሆን፡ እንጂ፡ ወይም፡ መልአክ፡ †እግዚአብ
ሔርን፡ አንጣላ። *ም፡ ፳፭፡ ፳፭። †ተም፡ ፭፡ ፴፱።
፲፡ እጅግም፡ መለየት፡ በሆነ፡ ጊዜ፡ የሻለቃው፡ ፈ
ራ፡ ጳውሎስን፡ በመካከላቸው፡ እንዳይነጥቁት። ጭ
ፍራውንም፡ አዘዘ፡ ከመካከላቸው፡ ጠልፈው፡ ይወ
ስዱት፡ ዘንድ፡ ወደደራሹም፡ ያገቡት፡ ዘንድ።

፲፩፤ በምትመጣውም፡ ሌሊት፡ጌታ፡ በፊቱ፡ቆሞ፡ አለም። *በርታ፡ ጳውሎስ፡ ሆይ፡አትፍራም። በየሩሳሌም፡ እንደ፡ መሰከርህልኝ፡ እንደሁ፡ ደግሞ፡ ደገባሃልና፡ †በሮሜ፡ ትመሰክርልኝ፡ ዘንድ። *ም፡ ፲፰፡ ፱።። †ም፡ ፲፱፡ ፳፩።።

፲፪፤ በጸባም፡ ጊዜ፡ ከአይሁድ፡ አያሌ፡ ሰዎች፡ ምክር፡ አደረጉ፡ ተማማሉም፡ እንዳይበሉ፡ እንዳይጠጡም፡ ጳውሎስን፡ እስኪገድሉ፡ ድረስ።

፲፫፤ ይህነንም፡ ምክር፡ ያደረጉ፡ ካርባ፡ ይበልጡ፡ ነበር።

፲፬፤ እርሳቸውም፡ ወደ፡ ካህናቱ፡አለቆችና፡ ወደ፡ ሽማግሎች፡ መጡ፡ አሉዋቸውም። እኛ፡ ተማምለናል፡ እንዳች፡ እንዳንቀምስ፡ ጳውሎስን፡ ሳንገድል።

፲፭፤ አሁንም፡ እላንተ፡ ከጉባዔው፡ ጋራ፡ ለሻለቃው፡ ንገሩት፡ ወደላንተ፡ ነገ፡ ያወጣው፡ ዘንድ፡ እንድትወዱ፡ ነገሩን፡በውነት፡ መመርመር። እኛም፡ወደላንት፡ ሳይደርስ፡ እንገድለዋለን።

፲፮፤ የጳውሎስም፡የእኅቱ፡ ልጅ፡ መሸጉጣቸውን፡ በሰማ፡ ጊዜ፡ መጣ፡ ወደደራሽም፡ገባ፡ለጳውሎስም፡ ነገረው።

፲፯፤ ጳውሎስም፡ ከመቶ፡ አለቆች፡ አንዱን፡ ጠራ፡ አለውም። ይህነን፡ ብላቴና፡ ወደ፡የሻለቃው፡ ውሰደው፡ የሚነግረው፡ ነገር፡ አለውና።

፲፰፤ እርሱም፡ ወሰደው፡ ወደ፡ የሻለቃውም፡ አገባው፡ አለም። የታሠረው፡ ጳውሎስ፡ ጸራኝ፡ ለመነኝም፡ ይህነን፡ ብላቴና፡ ወዳንተ፡ አገባው፡ ዘንድ፡ የሚነግርህ፡ ነገር፡ አለውና።

፲፱፤ የሻለቃውም፡ በጁ፡ ያዘው፡ ለብቻውም፡ ወሰደው፡ ጠየቀውም፡ አለውም፡ ምንድር፡ ነው፡ የምትነግረኝ።

፳፤ ብላቴናው፡ ግን፡ አለው። አይሁድ፡ ፈጽመው፡ ተማከሩ፡ይለምኑህ፡ዘንድ፡ጳውሎስን፡ለማውረድ፡ ነገ፡ ወደ፡ ፍርድ፡ ሸንጎ፡ እንዲወዱ፡ ነገሩን፡ በጣም፡ መመርመር።

፳፩፤ አንተ፡ ግን፡ እሺ፡ አትበላቸው። ከርሳቸው፡ ወገን፡ ካርባ፡ ሰዎች፡ የሚበልጡ፡ ሸምቀውበታልና። የተማማሉ፡ እንዳይበሉ፡ እንዳይጠጡም፡ ሳይገሉት። አሁንም፡ እርሳቸው፡ ተዘጋጅተዋል፡ ካንተም፡ ምላሹን፡ ይጠብቃሉ።

፳፪፤ የሻለቃው፡ ግን፡ ብላቴናውን፡ ሰደደው፡ አዘዘውም፡ለማንም፡እንዳይናገር፡ ይህነን፡ ወሬ፡ እንደገለጠለት።

፳፫፤ ከመቶ፡ አለቆችም፡ ሁለት፡ሰዎች፡ ጸራ፡ አለም። ሁለት፡ መቶ፡ ጭፍራ፡ አዘጋጁ፡ ወደ፡ ቂሣርያ፡ ይሔዱ፡ዘንድ። ሰባም፡ ፈረሰኞች፡ ሁለት፡ መቶም፡ ጋሻ፡ጃግሮች፡ በሌት፡ በሦስተኛው፡ ሰዓት።

፳፬፤ አባቍልትም፡ ይውሰዱ፡ ከርሳቸው፡ ጋራ፡ ጳውሎስን፡ ለማስቀመጥ፡ ወደ፡ ፊልክስ፡ ወደ፡ ሹሙ፡ ያደርሱት፡ ዘንድ።

፳፭፤ መልእክትም፡ ጻፈ፡ እንዲህ፡ ሲል።

፳፮፤ ከቀላውዴዎስ፡ ሊስያስ፡ ወደ፡ ጽኑ፡ ወደ፡ ፊልክስ። ደስ፡ ይበልህ።

፳፯፤ ይህን፡ ሰው፡ አይሁድ፡ ያዙት፡ ሊገሉትም፡ አስበው፡ ነበረ። እኔም፡ ከጭፍራ፡ ጋራ፡ *ደርሼ፡ አዳንሁት፡ ሮማዊ፡ እንደ፡ ሆነ፡ †ካወቅሁ፡ በኋላ። *ም፡ ፳፩፡ ፴፫።። †ም፡ ፳፪፡ ፳፭።።

፳፰፤ የሚያሳጡትንም፡ ምክንያት፡ አውቅ፡ ዘንድ፡ በወደድሁ፡ ጊዜ፡ ወደ፡ ሸንጎቸው፡ አመጣሁት። ም፡ ፳፪፡ ፴።።

፳፱፤ ስለ፡ ሕጋቸውም፡ ነገር፡ እንደሳጡት፡ አገኘሁት፡ ደሩ፡ ግን፡ ኃጢአት፡ አላገኘሁበትም፡ ወደ፡ ሞት፡ ወደ፡እሥራትም፡የሚያደርሰው። ም፡ ፲፰፡ ፲፬።።

፴፤ ባወቅሁም፡ ጊዜ፡ አይሁድ፡ ክፉ፡ ምክር፡ በዚህ፡ ሰው፡ እንደ፡ መከሩበት፡ በዚያን፡ ጊዜ፡ ወዳንተ፡ ሰደድሁት፡ጸላቶቹንም፡አዘዝሁ፡በፊትህ፡ይከሱት፡ ዘንድ። ጤና፡ ይስጥህ። *ም፡ ፳፬፡ ፰።።

፴፩፤ ጭፍሮችም፡እንደዛዛቸው፡ ጳውሎስን፡በሌት፡ወሰዱት፡ወደ፡ አንቲጳጥሪስም፡ይዘውት፡መጡ።

፴፪፤ በነገውም፡ ፈረሰኞችን፡ አሰናበቱ፡ ከርሱ፡ ጋራ፡ ይሔዱ፡ ወደ፡ ሰፈርም፡ ተመለሱ።

፴፫፤ እሌህም፡ ወደ፡ ቂሣርያ፡ መጡ፡ መልእክቱንም፡ ለሹሙ፡ሰጡ፡ጳውሎስንም፡በፊቱ፡አቀሙት፡

፴፬፤ ባነበባትም፡ ጊዜ፡ ጠየቀው፡ እንዲህ፡ ሲል፡ አንተ፡ ከወዴት፡ አገር፡ነህ። ከቂልቅያም፡እንደ፡ሆነ፡ በሰማ፡ ጊዜ፡ አለው። ም፡ ፳፩፡ ፫።።

፴፭፤ እሰማሃለሁ፡ ከሳሾችህ፡ ደግሞ፡ በመጡ፡ ጊዜ፡ አዘዘም፡ በሄሮድስ፡ አደራሽ፡ ይጠብቁት፡ዘንድ።

## ምዕራፍ፡ ፳፬፤

፩፤ ካምስት፡ ቀንም፡ በኋላ፡ ሐናንያ፡የካህናቱ፡ አለቃ፡ ወረደ፡ ከሽማግሎች፡ ከጉባዔ፡ ነጋሪውም፡ ጋራ፡ ስሙን፡ ጠርጡሎስ፡ የሚሉት። ወደ፡ ሹሙም፡ መጡ፡ ጳውሎስን፡ ሊያሳጡት።

፪፤ በተጸራም፡ ጊዜ፡ ጠርጡሎስ፡ ያሳጣው፡ ጀመረ፡ እንዲህ፡ ሲል።

፫፤ ለኛ፡ ብዙ፡ ሰላም፡ እጅግም፡ መልካም፡ ነገር፡ ለዚህ፡ ሕዝብ፡ በአሳብህ፡ እንደሆነለት፡ እኛ፡ በጊዜው፡ ሁሉ፡ በስፍራውም፡ ሁሉ፡ እንቀበላለን፡ እናመሰግንሃለን፡ ጽኑ፡ ፊልክስ፡ ሆይ።

፬፤ እንዳይበዛብህም፡ እለምንሃለሁ፡ ባጭር፡ ነገር፡ ትሰማን፡ ዘንድ፡ በቸርነትህ።

፭፤ ይህነን፡ ሰው፡ አግኝተናልና፡ መቅሠፍተኛና፡ ሁከት፡ የሚያነሣ፡ በዓለም፡ ባሉ፡ አይሁድ፡ ሁሉ፡ መካከል፡ የመናፍቃን፡ የናዝሬቶች፡ አለቃ፡ ሁና። ም፡ ፲፯፡ ፯።።

፮፤ መቅደሱንም፡ ደግሞ፡ ያረክስ፡ ዘንድ፡ ወደደ። ያዝነውም፡ በሕጋችንም፡ እንዲገባ፡ እንፈርድበት፡ ዘንድ፡ ወደድን። ም፡ ፳፩፡ ፳፰።።

፯፣ ሊስያስ፡ ግን፡ የሻለቃው፡ መጣና፡የግድ፡ ከጃችን፡ ወሰደው።

፰፣ ከሳሾቹንም፡ አዘዘ፡ ወደ፡ንተ፡ ይመጡ፡ዘንድ። ራስህ፡ታገኘዋለህ፡አንተ፡ስትመረምረው፡የዚህን፡ነገር፡ ሁሉ፡እርሱን፡የከሰስነበቱን። ምዕ፡ ፳፫፣ ፴፡፡

፱፣ አይሁድም፡ ደግሞ፡ ተከትለው፡ አሉ፡ ይህ፡ ነገር፡ እንደሁ፡ ነው።

፲፣ ሹሙ፡ በጠቀሰውም፡ ጊዜ፡ይናገር፡ዘንድ፡ ጳውሎስ፡ መለሰ፡ እንደህ፡ሲል። እኔ፡አውቃለሁ፡ከብዙ፡ ዘመን፡ጀምረህ፡ ፈራጅ፡ እንደ፡ ሆንህ፡ ለዚህ፡ ሕዝብ። ስለዚህም፡ ነገሬን፡ እናገራለሁ፡ ልቤን፡ ደስ፡ ኢያለው።

፲፩፣ አንተ፡ ታውቅ፡ ዘንድ፡ ይቻልሃልና፡ካሥራ፡ ሁለት፡ ቀን፡ እንደይበልጥ፡ *ወደ፡ የሩሳሌም፡ ከወጣሁ፡ እሰግድ፡ ዘንድ። *ምዕ፡ ፳፩፣ ፯፡፡

፲፪፣ በመቅደስም፡ አንድ፡ ሰው፡ ሳስተምር፡ አላገኙኝም፡ በሕዝብም፡ ሁከት፡ ስሰራ፡ በመስጊድም፡ ባገርም።

፲፫፣ ዛሬም፡በሚያሳጡኝ፡ነገር፡ ይጸኑበት፡ ዘንድ፡ አይችሉም።

፲፬፣ ነገር፡ ግን፡ እኔ፡ የዚህን፡ እውነቱን፡ እነግርሃለሁ፡*ክሕደት፡ ያሉትን፡ነገር፡ እንደርሱ፡ እኔ፡ ያባቶቼን፡ አምላክ፡አመልካለሁ፡ ለአሪት፡ በነቢያትም፡ የተጻፈትን፡ሁሉ፡ አምኜ። *ቍ፡ ፭፡፡

፲፭፣ ለኔም፡ በእግዚአብሔር፡ ተስፋ፡ አለኝ፡ እርሳቸው፡ ደግሞ፡ ራሳቸው፡የሚጠብቁት፡ ጊዜ፡ እንደለው፡ የሙታን፡ *ትንሣኤ፡ ይሆን፡ ዘንድ፡ ለጻድቃን፡ ለኃጢአተኞችም። *ዳን፡ ፲፪፣ ፪፡፡ ዮሐ፡ ፭፣ ፳፰፣ ፳፱፡፡

፲፮፣ ስለዚህም፡እጋደላለሁ፡ሁልጊዜ፡ የማታስናከል፡ ሕሊና፡ ትሆንልኝ፡ዘንድ፡በእግዚአብሔር፡ በሰውም፡ ፊት። ምዕ፡ ፳፫፣ ፩፡፡

፲፯፣ ከብዙ፡ ዘመንም፡ በኋላ፡ መጣሁ፡ ምጽዋትና፡ ቍርባን፡ ለወገኖቼ፡ አደርግ፡ ዘንድ። ምዕ፡ ፲፩፣ ፳፱፡፡ ገላት፡ ፪፣ ፲፡፡

፲፰፣ በዚያም፡ ጊዜ፡ አይሁድ፡ ከእስያ፡መጥተው፡ በመቅደስ፡አገኙኝ፡ ከሕዝብ፡ጋራ፡ ስከራከር፡ወይስ፡ በፍጅት፡ አይደለም፡ ስነጻ፡ እንጂ። ምዕ፡ ፳፩፣ ፳፯፡፡

፲፱፣ አሁንም፡ ለእለዚያ፡ ከዚህ፡ በፊትህ፡ ይመጡ፡ይከሱኝ፡ ዘንድ፡ይገባቸው፡ ነበር። በኔ፡ ላይ፡ነገር፡ እንደላቸው።

፳፣ ወይም፡ እለዚህ፡ራሳቸው፡ ይነግሩ፡ምን፡ክፉ፡ ነገር፡ አገኙብኝ፡ እኔ፡ በሸንጎ፡ ፊት፡ በቆምሁ፡ ጊዜ።

፳፩፣ ከዚህ፡ ካንድ፡ ነገር፡ በቀር፡ በመካከላቸው፡ ቁሚ፡ የምጮህበት። እኔ፡ ስለ፡ ሙታን፡ ትንሣኤ፡ ዛሬ፡ በፊታችሁ፡ ይፈረድብኛል። ምዕ፡ ፳፫፣ ፮፡፡

፳፪፣ ፊልክስም፡ ይህነን፡ በሰማ፡ ጊዜ፡ ለሌላ፡ ቀን፡ አስቀያቸው፡ ስለዚህ፡ መንገድ፡ እውነተኛ፡ እውቀት፡ አውቋልና፡ እንደህ፡ ሲልም፡ ነገራቸው። *ሊስያስ፡ የሻለቃው፡ በመጣ፡ ጊዜ፡ ነገራችሁን፡ እመረምራለሁ። *ምዕ፡ ፳፫፣ ፳፮፡፡

፳፫፣ የመቶውንም፡ አለቃ፡ አዘዘው፡ ጳውሎስን፡ ይጠብቅ፡ ዘንድ፡ ዕረፍትም፡ ይሰጠው፡ ዘንድ። ወዳጆቹንም፡ እንደይከለክልበት፡ ለርሱ፡ ከማገልገል፡ ወይም፡ ወደርሱ፡ ከመምጣት። ምዕ፡ ፳፯፣ ፫፡፡

፳፬፣ ከጥቂትም፡ቀን፡ በኋላ፡ ፊልክስ፡ መጣ፡ ከድሩሲላ፡ ከምሽቱ፡ ጋራ። እርስዋም፡ አይሁዳዊት፡ ነበረች። ጳውሎስንም፡ አስመጣ፡ ከርሱም፡ ሰማ፡ ስለ፡ ክርስቶስ፡ ሃይማኖት።

፳፭፣ በነገረውም፡ ጊዜ፡ ስለ፡ ጽድቅ፡ ስለ፡ፍትወትም፡ መተው፡ስለሚመጣም፡ኩነኔ፡ ፊልክስ፡ ደነገጠ፡ መለሰለትም። አሁንም፡ ሒድ፡ በተመቸኝ፡ ጊዜ፡ አስጸራሃለሁ።

፳፮፣ ከዚህም፡ ጋራ፡ ተስፋ፡ አደረገ፡ ከጳውሎስ፡ ብር፡ ይወስድ፡ ዘንድ፡ እንዲፈታው። ስለዚህም፡ ብዙ፡ ጊዜ፡ ያስመጣው፡ ይጫወተውም፡ ነበረ።

፳፯፣ ሁለት፡ አመትም፡ ከሆነ፡ በኋላ፡ *ጶርቅዮስ፡ ፊስጦስ፡ የፊልክስን፡ሹመት፡ወሰደ። ፊልክስም፡ †አይሁድን፡ደስ፡ ለማሰኘት፡ በወደደ፡ ጊዜ፡ጳውሎስን፡ እንደ፡ታሠረ፡ተወው። *ምዕ፡ ፳፭፣ ፲፬፡፡ †ምዕ፡ ፳፭፣ ፱፡፡

## ምዕራፍ፡ ፳፭፡

፩፣ ፊስጦስም፡ ወደ፡ ሹመቱ፡ በመጣ፡ ጊዜ፡ ከሦስት፡ ቀን፡ በኋላ፡ ከቄሣርያ፡ ወደ፡ የሩሳሌም፡ ወጣ።

፪፣ የካህናቱ፡ አለቃም፡ የአይሁድም፡ ታላላቆች፡ ከጳውሎስ፡ ላይ፡ ተናገሩ። ምዕ፡ ፳፬፣ ፩፡፡

፫፣ ለመኑትም፡ሞገስ፡ያደርግላቸው፡ዘንድ፡ወደ፡ የሩሳሌምም፡ ያስመጣው፡ ዘንድ። በመንገድም፡ አደቡት፡ ይገሉት፡ ዘንድ። ምዕ፡ ፳፫፣ ፲፭፡፡

፬፣ ፊስጦስም፡ አለ። ጳውሎስ፡በቄሣርያ፡ ተጠብቋል። እኔም፡ አስቢያለሁ፡ ወደዚያ፡ ፈጥኜ፡እሔድ፡ ዘንድ።

፭፣ ከላንትም፡ የሚችሉ፡እንደሉ፡ ከኔ፡ ጋራ፡ ይውረዱ፡ በዚህም፡ ሰው፡ ያለበትን፡ ነገር፡ ሁሉ፡ ይክሰሱት።

፮፣ ከርሳቸውም፡ ዘንድ፡ ካሥር፡ ቀን፡ የበለጠ፡ በተቀመጠ፡ጊዜ፡ ወደ፡ ቄሣርያ፡ ወረደ። በነገውም፡ በዙፋን፡ *ተቀመጠ፡ ጳውሎስንም፡ ሊያመጡት፡ አዘዘ። *ዮሐ፡ ፲፱፣ ፲፫፡፡

፯፣ በመጣም፡ ጊዜ፡ አይሁድ፡ ከየሩሳሌም፡ የወረዱት፡ከበቡት፡በጳውሎስ፡ላይም፡ እጅግ፡ ታላቅና፡ ከባድ፡ ምክንያት፡አመጡ፡ እውነት፡ያደርጉት፡ ዘንድ፡ የማይችሉትን።

፰፣ እርሱ፡ሲማጐት፡እንደህም፡ ሲል። የአይሁድን፡ሕግ፡ *መቅደስንም፡ ቄሣርንም፡ እንደቾ፡ አልበደልሁም። *ምዕ፡ ፳፬፣ ፲፪፡፡

፱፣ ፊስጦስ፡ግን፡*ለአይሁድ፡መልካም፡ያደርግ፡ዘንድ፡በወደደ፡ጊዜ፡ለጳውሎስ፡መለሰለት፡አለም።ት

ወደለህን፡ወደ፡የሩሳሌም፡ትወጣ፡ዘንድ፡ከዚያም፡ በዚህ ፡ ነገር፡ በፊቴ ፡ ትፈራረድ ። ጳውሎስም ፡ አለ።
*ም፡ ፳፬፡ ፳፯።

፲፡ እኔ፡ በቄሣር፡ ዙፋን፡ ፊት፡ ቆሜያለሁ፡ ከዚያ፡ እፈራረድ፡ ዘንድ፡ የሚገባኝ ። አይሁድን፡ በምንም፡ አልበደልሁም ፡ አንተ ፡ ደግሞ ፡ ፈጽመህ ፡ እንደታውቅ።

፲፩፡ እኔ፡ በድዬ፡ ወይም፡ ለሞት ፡ የሚገባ፡ ነገር፡ አድርጌ፡እንደሆንሁ፡ ከመሞት፡ እምቢ፡ አልልም። እሌህ፡ ግን፡ የሚከሱኝ፡ መከሰሰ፡ከንቱ፡ እንደ፡ ሆነ፡ለማንም፡አይቻለውም፡ለርሳቸው፡አሳልፎ፡ይሰጠኝ፡ ዘንድ። እኔ፡ በቄሣር፡ ተማጽኛለሁ።

፲፪፡ የዚያን፡ጊዜም፡ ፊስጦስ፡ ከሚመክሩት፡ሰዎች፡ጋራ፡ተጫወተ፡መለሰም፡ አለም። በቄሣርስ፡ ከተማጸንህ፡ ወደ፡ ቄሣር፡ ትሔዳለህ።

፲፫፡ አያሌ፡ ቀንም፡ ካለፈ፡ በኋላ፡ አግሪጳ፡ ንጉሥ፡ በርኒቄም ፡ ወደ፡ ቄሣርያ ፡ ወረዱ ፡ ፊስጦስን ፡ ሊገናኙት።

፲፬፡ ከዚያም፡አጅግ፡ ቀን፡ በተቀመጡ፡ ጊዜ፡ ፊስጦስ፡በጳውሎስ፡የሆነውን፡ነገር፡ ለንጉሡ፡ አነሣለት፡ እንደዚህ፡ሲል።ከዚህ፡አንድ፡ሰው፡አለ፡ፊልክስ፡አሥሮ፡አኖረው።

፲፭፡ ስለርሱም፡ በየሩሳሌም፡ ሳለሁ፡ የካህናት፡አለቆች፡የአይሁድም፡ ሽማግሎች፡ መጥተው፡ ነገሩኝ፡ በርሱ፡ እፈርድላቸው፡ ዘንድ።

፲፮፡ መለስሁላቸውም፡ አልኋቸውም ። የሮማውያን፡ ወግ፡ አይደለም፡ *ሰውን፡ ለሞት፡ አሳልፎ፡ ይሰጡ፡ዘንድ፡ተከሳሹ፡በከሳሾች፡ፊት፡ለፊት፡ሳይቆም፡ ጊዜም፡ ሳያገኝ፡ በደሉን፡ የሚያነጻበት።
*ዘዳግ፡ ፲፯፡ ፬።

፲፯፡ ባንድም፡ ወደዚህ፡ በመጡ ፡ ጊዜ፡ አልዘገየሁም፡ በነገውም፡ በዙፋን፡ በተቀመጥሁ፡ ጊዜ፡ ያነን፡ ሰው፡ ያመጡት፡ ዘንድ፡ አዘዝሁ።

፲፰፡ ከሳሾቹም፡ ቀሙበት፡ አንድም ፡ ምክንያት፡ ስንኳ፡ አላመጡም፡ እኔ፡ አስበው፡ ከነበረው።

፲፱፡ ነገር ፡ ግን፡ ስለ፡ ሃይማኖታቸው ፡ ክርክር፡ ነበራቸው፡የሱስም፡ስለ፡ሞተ፡ ሰው፡ ጳውሎስም፡ ይላል፡ ሕያው፡ ነው። ሉቃ፡ ፳፬፡ ፳፫።

፳፡ እኔም፡ ስለዚህ ፡ ማሳጣት ፡ ብቸገር ፡ አልሁት፡ ይወድ፡ እንደሆን፡ ወደ፡የሩሳሌም፡ መሔድ፡ ከዚያ፡ ሒዶ፡ በዚህ፡ ነገር፡ ይፈራረድ ፡ ዘንድ።

፳፩፡ ጳውሎስ፡ግን፡ ወደ፡አውጉሥጦስ፡ ፍርድ፡ ይጠበቅ፡ዘንድ፡ስለተማጸነ፡ ይጠበቅ፡ ዘንድ፡ አዘዝሁ፡ ወደ፡ ቄሣር፡ እስክሰደው፡ ድረስ።

፳፪፡ አግሪጳም፡ ፊስጦስን፡አለው፡እኔም፡ ደግሞ፡ እወደለሁ፡ ያነን፡ ሰው፡ እሰማው፡ ዘንድ ። እርሱም፡ አለው፡ነገ፡ ትሰማዋለህ።

፳፫፡ በነገውም ፡ አግሪጳና፡ በርኒቄ ፡ በብዙ ፡ ሽልማት፡ያጌበቡ፡ በመጡ፡ጊዜ፡ወደ፡ፍርድ፡ቤትም፡ በገቡ፡ ጊዜ፡ ከሻለቆች፡ጋራ፡ ከታላላቆችም፡ ካገሩ፡ ሰዎች፡ጋራ፡ በፊስጦስ፡ትእዛዝ፡ጳውሎስን፡ አመጡት።

፳፬፡ ፊስጦስም፡አለ። አግሪጳ፡ ንጉሥ፡ሆይ፡ እላንትም፡ከኛ፡ዘንድ፡ የመጣችሁ፡ ሰዎች፡ ሁሉ። አያችሁት፡ይህ፡ ሰው፡እንደ፡ሆነ፡ ስለርሱ፡ የነገሩኝ፡ አይሁድ፡ ሁሉ፡ በየሩሳሌም፡ ከዚህም ፡ *ኢየጮሁ ፡ ሕይወት፡ እንደይገባው፡ እንጊደህ፡ ደግሞ። *ም፡ ፳፪፡ ፳፪።

፳፭፡ እኔም ፡ ባወቅሁ፡ ጊዜ ፡ ለሞት ፡ የሚያደርሰው፡ ነገር፡ እንዳልሰራ፡ እርሱም፡ በቄሣር ፡ በተማጸነ፡ ጊዜ ፡ ፈረድሁ ፡ ወደርሱ ፡ እሰደው ፡ ዘንድ።

፳፮፡ ስለርሱም፡ የታወቀ፡ ወሬ፡ የለኝም፡ ወደ፡ ጌታዬ፡የምጽፈበት።ስለዚህም፡ ወደላንት፡ አመጣሁት፡ይልቁንም፡ወደንተ፡ አግሪጳ፡ንጉሥ፡ ሆይ። በተመረመረ፡ጊዜ፡ ስለርሱ፡ ለመጻፍ፡ ይሆንልኝ፡ ዘንድ።

፳፯፡ ሞኝነት፡ ይመስለኛልና፡ ሰውን፡አሥሬ፡ እሰድ፡ ዘንድ፡ በላዩ፡ ያለበትን፡ ምክንያት፡ ሳልነግር።

## ምዕራፍ፡ ፳፮።

፩፡ አግሪጳም፡ ጳውሎስን፡ አለው። ተፈቅዶልሃል፡ ትናገር፡ዘንድ፡ስለ፡ራስህ።የዚያን፡ጊዜም፡ጳውሎስ፡ እጁን፡ ዘረጋ፡ይናገር፡ ዘንድ፡ አለም።

፪፡ ሰውነቴን፡የተመሰገነ፡ ሁና፡እቈጥራለሁ፡አግሪጳ፡ንጉሥ፡ሆይ። ዛሬ፡በፊትህ፡ እናገር፡ዘንድ፡ እንዲገባኝ፡ከአይሁድ፡ስለ፡ ተከሰስሁበት፡ነገር፡ ሁሉ።

፫፡ ይልቁንም፡ አውቃለሁና ፡ የአይሁድን፡ ልማድና፡ክርክር፡ ሁሉ፡ እንድታውቅ። ስለዚህም፡ እለምንሃለሁ፡ በትዕግሥት፡ ትሰማኝ፡ ዘንድ።

፬፡ አተዳደጌ፡ ከሕፃንነቴ፡ጀምሮ፡እንዴት፡እንደ፡ሆነ፡ቀድሞ፡የነበርሁበትን፡ ከወገኖቼ፡ ጋራ፡ በየሩሳሌም፡ አይሁድ፡ ሁሉ፡ ያውቁታል።

፭፡ አስቀድመው፡ የሚያውቁኝ፡ ቢወዱ፡ ይመስክሩ፡እኔ፡በአምልኳችን፡ በብርታት፡ እንደ፡ በለጠ፡ወገን፡ *ፈሪሳዊ፡ ሁኜ፡ እንደኖርሁ። *ም፡ ፳፫፡ ፮።
ፊል፡ ፫፡ ፭።

፮፡ አሁንም፡ከእግዚአብሔር፡ዘንድ፡ ላባቶቻችን፡ ስለ፡ ሆነው፡ ተስፋ፡ ተፈርዶብኝ፡ ቆሜያለሁ።
ም፡ ፳፰፡ ፳።

፯፡ ወደርሱም፡አሥራ፡ ሁለቱ፡ ወገኖቻችን፡ እግዚአብሔርን ፡ ኢያመለኩ፡ ሁልጊዜ፡ ሌትና፡ቀን፡ ይደርሱ፡ ዘንድ፡ ተስፋ፡ ያደርጋሉ ። ስለዚህም፡ ተስፋ፡ አግሪጳ፡ ንጉሥ፡ ሆይ፡ ከአይሁድ፡ እከሰሳለሁ።
ም፡ ፳፬፡ ፲፭።

፰፡ እንዴት፡በላንት፡ዘንድ፡የማይታመን፡ ነገር፡ ሆነ፡ ይቈጠራልን፡ እግዚአብሔር ፡ ሙታንን፡ እንዲያስነሣ።

፱፡ እኔ፡ግን፡በሰውነቴ፡ አሰብሁ፡ እጅግ፡ነገር፡ አደርግ፡ዘንድ፡እንዲገባኝ፡ የናዝሬቱን፡ የየሱስን፡ ስም፡ የሚጣላ። ም፡ ፱፡ ፩—፳፪። ም፡ ፳፪፡ ፫—፳፩።

፲፡ ይህነንም፡ደግሞ፡በየሩሳሌም፡ አደረግሁት፡ ከ

ቅዱሳንም፡ ብዙውን፡ ሰዎች፡ በግዞት፡ ጨመርኋቸው፡ትእዛዝ፡በውሰድሁ፡ ጊዜ፡ ከካህናቱ፡ አለቆች። ሲገልዋቸውም፡ ፍርድ፡ የማስፈርድባቸው፡እኔ፡ ነበርሁ።

፲፩፡ በመስጊዲም፡ ሁሉ፡ ብዙ፡ ጊዜ፡ ቀጣኋቸው፡ ይሰድቡትም፡ ዘንድ፡ የግድ፡ አልኋቸው፡ በላያቸውም፡ያለ፡ልክ፡ ወፈፍ፡ብዬ፡ ወደ፡ እንግዶች፡ አገር፡ ደግሞ፡ አሳደኋቸው፡ ነበርሁ።

፲፪፡ በዚህም፡ ነገር፡ ተይዤ፡ ወደ፡ ደማስቆ፡ ሔድሁ፡ በካህናት፡ አለቆች፡ ትእዛዝ፡ በፈቃዳቸውም።

፲፫፡ በኵል፡ቀንም፡በመንገድ፡አየሁ፡ ንጉሥ፡ ሆይ፡ ከሰማይ፡ ብርሃን፡ ከጸሓይ፡ ብልጫታ፡ የሚበልጥ፡በዙርያዬም፡ በራ፡ ከኔም፡ ጋራ፡ በነበሩት፡ ዙርያ።

፲፬፡ ሁላችንም፡ በምድር፡ ላይ፡ በወደቅነ፡ ጊዜ፡ ድምጽ፡ሰማሁ፡ሲናገረኝ፡ሲለኝም፡በዕብራይስጥ፡ ቋንቋ። ሳውል፡ሳውል፡ ለምን፡ ታሳድደኛለህ። በመውጊያ፡ ላይ፡ ብትራገጥ፡ ላንተ፡ ይብስሃል።

፲፭፡ እኔም፡አልሁ፡አንተ፡ማነህ፡አቤቱ። እርሱም፡ አለ፡እኔ፡የሱስ፡ነኝ፡ አንተ፡ የምታሳድደኝ።

፲፮፡ ነገር፡ግን፡ተነሣና፡ቁም፡ በግርህ፡ እኔ፡ ስለዚህ፡ ታይቼሃለሁና፡ እሾምህ፡ ዘንድ፡ አገልጋይ፡ ምስክርም፡ እንድትሆን፡ ባየኸው፡ ነገር፡ በምገልጥልህም።

፲፯፡ ከሕዝብ፡ሳድንህ፡ ከአሕዛብም፡ ዛሬ፡ ወደርሳቸው፡ከምሰድ።

፲፰፡ ዓይናቸውን፡ *ትከፍት፡ ዘንድ፡ ከጨለማ፡ ወደ፡ብርሃን፡ እንዲመለሱ። ለሰይጣንም፡ ከመገዛት፡ ወደ፡እግዚአብሔር። የኃጢአታቸውን፡ ስርየት፡ይወስዱ፡ዘንድ፡ተርስትም፡ ከቅዱሳን፡ ጋራ፡ በኔ፡በማመናቸው። *ኢሳ፡ ፴፪፡ ፯፡፡ ኤፌ፡ ፩፡ ፲፰፡፡ ተም፡ ፳፡ ፴፪፡፡ ኤፌ፡ ፩፡ ፲፩፡፡

፲፱፡ ስለዚህም፡ አግሪጳ፡ ንጉሥ፡ ሆይ፡ ዓመፀኛ፡ አልሆንሁም፡ከሰማይ፡ ለታየኝ፡ ነገር። ገላ፡ ፩፡ ፲፮፡፡

፳፡ ነገር፡ ግን፡ በደማስቆ፡ አስቀድሜ፡ *አስተማርሁ፡በየሩሳሌምም፡በይሁዳም፡አገር፡ሁሉ፡ከዚያም፡ በኋላ፡በአሕዛብ፡ንስሐ፡ ይገቡ፡ ዘንድ፡ ወደ፡ እግዚአብሔርም፡ይመለሱ፡ዘንድ፡ለንስሐ፡የሚገባ፡ነገር፡ኢያደረጉ። *ም፡ ፱፡ ፳፡፡

፳፩፡ ስለዚህም፡አይሁድ፡ በመቅደስ፡ ያዙኝ፡ሊገሉኝም፡ አሰቡ።

፳፪፡ ነገር፡ ግን፡ ከእግዚአብሔር፡ ዘንድ፡ ረድኤት፡ ተቀብዬ፡እስከዚህ፡ ቀን፡ ድረስ፡ ቆምሁ፡ ስመሰክር፡ ለታላቁ፡ ለታናሹም። ምንም፡ አልናገርም፡*ነቢያት፡ ከተናገሩት፡ነገር፡የወጣ፡ሙሴም፡ደግሞ፡ ይሆን፡ ዘንድ፡ እንደ፡ለው። *ሉቃ፡ ፳፬፡ ፵፬፡፡

፳፫፡ ለክርስቶስ፡ሊገባው፡እንደነበረ፡መከራ፡ሊቀበል፡ከሙታንም፡*አስቀድሞ፡እንዲነሣ፡ብርሃንም፡ እንዲገልጥ፡ለሕዝብና፡ለአሕዛብ። *፩፡ ቆሮ፡ ፲፭፡ ፳፡፡

፳፬፡ እርሱም፡ ይህነን፡ ሲናገር፡ ፊስጦስ፡ በታላቅ፡ ቃል፡ አለ። ፈጽመህ፡ አበድህ፡ ጳውሎስ፡ሆይ። ብዙ፡ ዕውቀት፡ አዛነጋህ፡ አስከታብድ፡ ድረስ።

፳፭፡ እርሱ፡ ግን፡ አለ። አላበድሁም፡ ጽኑ፡ ፊስጦስ፡ ሆይ፡ ነገር፡ ግን፡ እውነትና፡ የታሰበ፡ ነገር፡ እናገራለሁ።

፳፮፡ ንጉሥ፡ደግሞ፡ ይህነን፡ ሁሉ፡ያውቃልና፡ በፊቱ፡በግልጥ፡የምናገርበትን። ተረድቻለሁና፡ከዚህ፡ ነገር፡አንዳች፡ከርሱ፡*እንዳይሰውር። ይህ፡በስውር፡የተደረገ፡ አይደለምና። *ዮሐ፡ ፲፰፡ ፳፡፡

፳፯፡ አግሪጳ፡ንጉሥ፡ሆይ፡ነቢያትን፡ ታምናለህን። እኔ፡ አውቃለሁ፡ እንድታምናቸው።

፳፰፡ አግሪጳም፡ ጳውሎስን፡ አለው። ጥቂት፡ ቀረህ፡ ክርስቲያን፡ ልታደርገኝ።

፳፱፡ ጳውሎስም፡ አለ። ከእግዚአብሔር፡ ዘንድ፡ እለምናለሁ፡በጥቂት፡በጅግም፡ አንተ፡ብቻ፡አይደለህም፡ዛሬ፡ እኔን፡የሚሰሙኝ፡ ሁሉ፡ እንጂ፡ እንደ፡ህ፡ እንደኔ፡ይሆኑ፡ ዘንድ፡ ከዚህ፡ ከሥራቴ፡ በቀር።

፴፡ ይህነንም፡ነገር፡ባለ፡ጊዜ፡ ንጉሡ፡ ተነሣ፡ ሹሙም፡በርኒቄም፡ ከርሳቸውም፡ጋራ፡ ተቀምጠው፡ የነበሩት።

፴፩፡ ለብቻቸውም፡ በሆኑ፡ ጊዜ፡ እርሱ፡ በርሳቸው፡ አሉ። ይህ፡ሰው፡ ምንም፡ክፉ፡ ነገር፡ አላደረገም፡ ለሞት፡ ለሥራትም፡ የሚያደርሰው።

፴፪፡ አግሪጳም፡ ፊስጦስን፡አለው። ይህ፡ ሰው፡ ይፈታ፡ ዘንድ፡ ይገባ፡ ነበር፡ በቄሣር፡ ባልተማጸነ። ም፡ ፳፭፡ ፲፩፡፡

## ምዕራፍ፡ ፳፯፡

፩፡ ወደ፡ኢጣልያም፡ በባሕር፡እንሰር፡ ዘንድ፡ *በተቈረጠ፡ጊዜ፡ ጳውሎስን፡ አሳልፈው፡ ሰጡት፡ ሌሎችንም፡ የታሠሩትን፡ ሰዎች፡ ለመቶው፡ አለቃ፡ ስሙን፡ ዮልዮስ፡ የሚሉት፡ ከአውጉሥጦስ፡ ጭፍራ። *ም፡ ፳፭፡ ፲፪፡፡

፪፡ በአድራሚጢ፡መርከብም፡በገባን፡ጊዜ፡ አሰብን፡ በእስያ፡ወደሉቸው፡ አገር፡ እንሔድ፡ዘንድ። ከኛም፡ ጋራ፡ *አርስጠርኮስ፡ ነበር፡ የመቄዶንያው፡ የተሰሎንቄ፡አገር። *ም፡ ፲፱፡ ፳፱፡፡

፫፡ በነገውም፡ወደ፡ሲዶና፡ደረስን። ዮልዮስም፡ለጳውሎስ፡ ቸር፡ ነበረ፡ወደ፡ ወዳጆቹም፡ይሔድ፡ ዘንድ፡ ፈቀደለት፡ ከርሳቸው፡ የሚሻውን፡ ለመውሰድ። ም፡ ፳፬፡ ፳፫፡፡ ፳፰፡ ፲፮፡፡

፬፡ ከዚያም፡ ወጣን፡ ከቆብሮስም፡ ወደ፡ ግራችን፡ ሰረርን፡ ነፋስ፡ ጠሞብን፡ ነበርና።

፭፡ በባሕርም፡የቂልቅያና፡ጵምፌልያ፡ ዳር፡ ካለፍን፡ በኋላ፡ ወደ፡ ሚራ፡ በሊኪያ፡ ምድር፡ ወደለች፡ መጣን።

፮፡ ከዚያም፡የመቶው፡አለቃ፡የእስክንድርያ፡ መርከብ፡አገኘ፡ወደ፡ኢጣልያ፡ የሚሔድ። በርሱም፡ ተቀመጥን።

፯፤ እጅግ፡ ቀንም ፡ በዘገየነ፡ ጊዜ፡ በመንገዳችን፡ በ
ግድ፡ወደ፡ ክኒደስ፡ደረስነ፡ ነፋሱ፡ባይተወነ፡ ከቀሬጢ
ስም፡በታች፡ሰረርነ፡ በሰልሞና፡ ፊት፡ ለፊት።

፰፤ በግድም፡ባለፍናት፡ጊዜ፡ መልካም፡ ወደብ፡ ወ
ደሚሉት፡ ስፍራ፡ መጣነ፡ በላሲያ፡ አገር፡ አጠገብ፡ ያ
ለች።

፱፤ ብዙ፡ጊዜም፡ካለፈብነ፡በኋላ፡በባሕርም፡ የሚ
ሔደበት፡ወራት፡ *የሚያስጨንቅ፡ በሆነ፡ ጊዜ። ጾም
ም፡†አልፎ፡ ነበርና፡ ጳውሎስ፡ መከራቸው፡ አላቸው
ም።　*፪፤ ቆሮ፡ ፲፩፡ ፳፭፡ ፳፯፡፡ †ዘሌዋ፡ ፲፮፡ ፳፱፡፡

፲፤ እላንት፡ሰዎች፡እኔ፡አያለሁ፡አካሔዳችን፡በጭ
ንቅ፡ይሆን፡ዘንድ፡ እንደለው፡ በብዙም፡ ጥፋት፡ ለሽ
ክሙና፡ ለመርከቡ ፡ ብቻ ፡ አይደለም ፡ ለራሳችንም፡
እንጂ።

፲፩፤ የመቶው ፡ አለቃ፡ግን ፡ የመርከብ ፡ መሪውን፡
ነገር፡ይሰማ፡ነበረ፡የመርከቡንም፡ባለቤት፡ ከጳውሎ
ስ፡ነገር፡ይልቅ።

፲፪፤ ያም፡ወደብ፡ ባይሰማማቸው ፡ይከርሙበት፡
ዘንድ፡የሚልቁቱ፡ወደዚ፡ ከዚያ፡ ይሔዱ፡ ዘንድ፡ም
ናልባት፡ቢቻላቸው፡ወደ፡ፊንቄ፡ ደርሰው፡ ይከርሙ፡
ዘንድ፡የቀሬጢስ፡ ወደብ፡ የሚሆን። ወደ፡ ደቡብና፡
ምዕራብ፡ ነውና፡ ወደ፡ ሰሜንና፡ ወደ፡ ምዕራብ።

፲፫፤ የደቡብ ፡ ነፋስም ፡ በነፈሰ ፡ ጊዜ፡ የሚሹትን፡
ያገኙ፡መሰላቸው፡ መልሕቁንም፡አነሡ፡ በቀሬጢስ
ም፡አጠገብ፡ አለፉ።

፲፬፤ ከዚያም፡ በኋላ፡እጅግ፡ሳይዘገይ፡ ነፋስ፡ዓው
ሎ፡ ነፋስ፡ ዩርክሌደን፡ የሚሉት።

፲፭፤ መርከቡም፡ በተነጠቀ፡ ጊዜ፡ ነፋሱንም፡ ይቃ
ወም፡ ዘንድ፡ አልተቻለውም ፡ ተለቀቅነ፡ ተነዳነም።

፲፮፤ ወደ፡ደሴትም፡ ባለፍነ፡ጊዜ፡ ስምዋን፡ ከላው
ዳ፡ የሚሉዋት፡ በግድ፡ ቻልነ ፡ ታንኳዪቱን፡ እንይዝ፡
ዘንድ።

፲፯፤ ይህችንም፡ ነሥተው፡በዚህ፡ ረዳት፡መርከቡ
ን፡ በታች፡ አሠርዋት። ፈርተውም፡ ወደ ፡ አሸዋ፡ እን
ደይወድቁ ፡ መጋረጃውን ፡ አወረዱ ፡ እንደሁም፡ ተ
ውት።

፲፰፤ ዓውሎ፡ነፋሱም፡ በላያችን፡ ኢየከፋ፡ ሲወር
ድብነ፡በሁለተኛው፡ ቀን፡ መርከቡን፡ አቀለሉ።

፲፱፤ ብሶስተኛውም ፡ ቀን ፡ የመርከቡን፡ እቃ ፡ ጣ
ልነ፡ በጃችን።

፳፤ ከዚያም፡ በኋላ፡ አልታዮችነም፡ጸሓይ፡ ጨረቃ
ም፡ ከዋክብትም፡ ብዙ፡ ቀን፡ ነፋሱም፡ በረታብነ። ከ
ዚህም፡ የተነሣ፡ የደህንነታችን፡ ተስፋ፡ ሁሉ፡ ተቈረ
ጠብነ።

፳፩፤ እጅግም፡ ቀን፡ሳንበላ፡በተቀመጥነ፡ጊዜ፡የዚ
ያን፡ ጊዜም ፡ ጳውሎስ ፡ በመካከላቸው ፡ ቆመ ፡ አለ
ም። እላንት፡ ሰዎች፡ቀድሞ፡ ይገባችሁ፡ነበር፡ ምክሬ
ን፡ሰምታችሁ፡ ከቀሬጢስ ፡ እንዳትነሡ፡ ይህነንም፡
ድካም ፡ ይህነንም ፡ ጥፋት ፡ ባልተቀበልነም ፡ ነበር።

፳፪፤ አሁንም፡እኔ፡እመክራችኋለሁ፡ ደስ፡ ይላች
ሁ፡ዘንድ። ምንም፡ ጥፋት፡ ከራሳችሁ፡ አይሆንምና፡
ከመርከቡ፡ በቀር።

፳፫፤ የእግዚአብሔር፡መልአክ፡ በዚህች፡ ሌሊት፡
ከኔ፡ ጋራ፡ ቁሞ፡ ነበርና። እኔ፡ለርሱ፡ የምሆን፡ እርሱን
ም፡ የማመልክ።

፳፬፤ እንዲህ፡ሲል። አትፍራ፡ ጳውሎስ፡ ሆይ፡ በቄ
ሣር፡ ፊት፡ ትቀማለህና። እግዚአብሔርም፡ እነሆ፡ላ
ንት፡ ሰጥቶሃል፡ ካንተ፡ ጋራ፡ የሚሔዱትን፡ ሁሉ።
ም፡ ፳፫፡ ፲፩፡፡

፳፭፤ ስለዚህም፡ደስ፡ይበላችሁ፡ እላንት፡ ሰዎች።
እኔ፡በእግዚአብሔር፡አምናለሁና፡እንደሁ፡እንዲሆ
ን፡ እንደ፡ ነገረኝ።

፳፮፤ ነገር፡ ግን፡ ወደንዲት፡ ደሴት፡ እንወርዳለን።
ም፡ ፳፰፡ ፩፡፡

፳፯፤ አሥራ፡አራተኛ፡ሌትም፡ በሆነ፡ጊዜ፡እኛም፡
ወደያና፡ወደዚህ፡በአድሪያ፡ ባሕር፡ ስንገፋ፡ በእኩለ፡
ሌሊት፡ መርከበኞች፡ ወደገር፡ የቀረቡ ፡ መሰላቸው።

፳፰፤ የጥልቅም፡ መለኪያ፡ እርሳስ፡ ቢጥሉ ፡ ሀያ፡
ክንድ፡አገኙ፡ ከዚያም፡ ደግሞ፡ጥቂት፡ ሒደው፡ ቢለ
ኩ፡ አሥራ፡ አምስት፡ ክንድ፡ አገኙ።

፳፱፤ ደንጊያ፡ወደለበትም፡ ወደ፡ ክፉ፡ ስፍራ፡ እን
ደይወድቁ፡ፈሩ፡ከመርከቡም፡ኋላኛ፡ ክፍል፡አራት፡
መልሕቅ፡ ጣሉ፡ ቀንም፡ እንዲሆን፡ ተማለሉ።

፴፤ መርከበኞችም ፡ ከመርከብ ፡ መኰብለል ፡ አ
ሰቡ፡ታንኳዪቱንም፡ወደ፡ባሕር፡አወረዱ፡ በምክንያ
ት፡ ሊሔዱ፡ ከመርከብም፡ ፊተኛ፡ ክፍል ፡ መልሕቁ
ን፡ እንዲጥሉ።

፴፩፤ ጳውሎስም ፡ ለመቶው፡ አለቃ፡ ለጭፍራው
ም፡አለ። እሌህ፡ በመርከቡ፡ ካልተቀመጡ፡ አይቻላ
ችሁም፡ ትድኑ፡ ዘንድ።

፴፪፤ ከዚያ፡ ወዲያም፡ ጭፍሮች፡ የታንኳውን፡ ገ
መድ፡ቈረጡት፡ይሔድም፡ ዘንድ፡ ተውት።

፴፫፤ ሊጸባም፡ በጀመረ፡ ጊዜ፡ ጳውሎስ ፡ ልባቸው
ን፡አጽና፡እንጀራ፡ ይበሉ፡ዘንድ፡ እንዲህ፡ሲል። ዛሬ፡
ለላንት፡*አሥራ፡አራት፡ ቀናችሁ፡ ነው፡ ከቆያችሁ፡ጾ
መኞችም፡ ሁናችሁ ፡ እንዳች፡ መብል ፡ ሳትወስዱ።
*ቍ፡ ፳፯፡፡

፴፬፤ ስለዚህም፡እለምናችኋለሁ፡ መብል፡ትወስ
ዱ፡ዘንድ፡ እርሱ፡ለመድኃኒታችሁ፡ ይሆንላችኋልና።
ከላንትም፡ከራስ፡*አንዲት፡ ጸጕራችሁ፡ ስንኳ፡አት
ወድቅም።　*ማቴ፡ ፲፡ ፴፡

፴፭፤ ይህነንም፡ ብሎ፡ እንጀራም፡ ይዞ ፡ *እግዚአ
ብሔርን፡ አመሰገነ፡ በሁሉ፡ ፊት፡ ቈረሰውም፡ ይበላ
ም፡ጀመረ።　*ዮሐ፡ ፮፡ ፲፩፡፡ ፩፡ ጢሞ፡ ፬፡ ፬፡፡

፴፮፤ ሁሉም ፡ ደስ ፡ አላቸው ፡ እርሳቸውም ፡ ደግ
ሞ፡እንጀራ፡ ወሰዱ።

፴፯፤ በመርከቡም፡ላይ፡የነበርነው፡ሰዎች፡ሁለት፡
መቶ፡ ሰባ፡ ስድስት፡ ነበርነ።

፴፰፡ መብሉንም፡በጸገቡ፡ጊዜ፡ መርከቡን፡ አቀለሉት፡ ስንዴውንም፡ወደ፡ባሕር፡ ጣሉት።

፴፱፡ በጸባም፡ጊዜ፡ምድሩን፡ አላወቁትም፡ የባሕርን፡ጉበት፡ከደሩ፡ጋራ፡አዩ፡እንጂ። ቢቻላቸውም፡መርከቡን፡ ወደርሱ ፡ ያገቡት፡ ዘንድ፡ ፈቀዱ።

፵፡ መልሕቁንም ፡ አወጡት፡ ባሕሩም ፡ እንደመራቸው፡ራሳቸውን፡ተውት፡ የመቅዘፊቹንም፡ ማሠርያ፡ፈቱት፡ታናሹም፡መጋረጃ፡ለነፋስ፡ ሰቀሉ፡ወደ፡ዳርም፡እንሔድ፡ጀመርን።

፵፩፡ በሁለት፡ ባሕር፡ መካከልም፡ ወደላ፡ ስፍራ፡ በወደቁ፡ጊዜ፡መርከቡን፡ ወደ፡ ተሰወሩበት፡ ደንጎቹ፡ ሰደዷት ፡ የፊተኛውም፡ ደረቱ፡ ተያዘ፡ ተተክሎም፡ ቀረ፡ እንደ፡ደናወጥ፡ የኋለኛው፡ግን፡ ተሰባበረ፡ ከማዕበሉ፡ጽናት፡ የተነሣ። ፪፡ ቆሮ፡ ፲፩፡ ፳፭።

፵፪፡ ጭፍሮችም፡ ተማከሩ ፡ እሥረኞችን፡ ይገድሉ፡ ዘንድ ፡ ከርሳቸው ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ዋኝቶ ፡ እንዳያመልጥ።

፵፫፡ አለቃው፡ግን፡ ጳውሎስን፡ያድነው፡ ዘንድ፡ወደደ፡ይህነን፡ምክራቸውን፡ እምቢ፡አለ። ይዋኙ፡ ዘንድ፡የሚቻላቸውንም፡ አዘዘ፡ ዋኝተው፡ወደ፡ምድር፡ እንዲወጡ።

፵፬፡ የቀሩትም፡ ወጡ ፡ አኵሌቶቹ ፡ በእንጨት፡ ሳንቃ፡ላይ፡አኵሌቶቹም፡በመርከቡ፡ስባሪ። እንደዚሁም፡ሆነ፡ ሁሉ፡ በደህንነት፡ ወደ፡ ምድር፡ ደርሰው፡እንደደኑ። ቍ፡ ፳፪፡—፳፭።

ምዕራፍ፡ ፳፰፡

፩፡ በዳኑም፡ ጊዜ፡ ከዚያ፡በኋላ፡ አወቁ፡ ያቺ፡ ደሴት፡ ስምዋ፡ መሊጣ፡ እንድትባል።

፪፡ አረማውያንም፡እጅግ፡ አዘኑልን፡እሳት፡ አንድ ደውልናልና፡ ሁላችንንም፡ ወስደውናልና፡ ዝናም፡ ጽኑ፡ ስለ፡ ሆነ፡ስለ፡ ብርዱም። ፪፡ ቆሮ፡ ፲፩፡ ፳፯።

፫፡ ጳውሎስም፡እጅግ፡ጭራሮ፡ ሲለቅም፡ ወደሳትም፡ሲጨምር፡እፉኝት፡ ከሳቱ፡ ትኵሳት፡ የተነሣ፡ ወጣች፡ በእጁም፡ ተንጠለጠለች።

፬፡ አረማውያንም፡ ባዩ፡ጊዜ፡ እፉኝት፡ በጁ፡ ተንጠልጥላ፡ እርሱ ፡ በርሳቸው፡ አሉ ። ይህ፡ ሰው፡ አይጠረጠር፡ ነፍስ፡ ገዳይ፡ ነው። ከባሕርም፡ ቢድን፡በቀሉ፡ አልተወውም፡ በሕይወት ፡ ይኖር፡ ዘንድ።

፭፡ እርሱ፡ግን፡ እፉኝቱን፡ ወደሳት፡ አረገፋት፡ አንዳችም፡ክፉ፡ነገር፡አላገኘውም። ማር፡ ፲፮፡ ፲፰።

፮፡ እርሳቸው፡ግን፡ሲመለከቱት፡ዘገዩ፡አሁን፡ያብጣል፡አሁንም፡ ሙቶ፡ይወድቃል፡ ብለው። እጅግም፡ ጊዜ፡ ቢቈዩ ፡ ቢያዩትም ፡ አንዳች፡ እንዳላገኘው፡ ነገራቸውን፡ ለወጡ፡ አሉም። *አምላክ፡ ነው።

*ም፡ ፲፬፡ ፲፩።

፯፡ በዚያም፡ስፍራ፡ ዙርያ፡አገር፡ነበረ፡ለደሴቱ፡ አለቃ፡ስሙን፡ጶብልዮስ፡ የሚሉት። ይህም፡ እንግድነት፡ተቀበለነ፡ሦስት፡ቀንም፡ በቤቱ፡ አሳደረነ።

፰፡ የጶብልዮስም ፡ አባት፡ ወድቆ፡ ይኖር፡ ነበረ፡ ታሞ፡ምንሾ፡ያንጀትም፡ቍርጠት። ጳውሎስም፡ወደርሱ፡ገባ፡ጸለየለትም፡እጁንም፡ በላዩ፡ ጫነበት፡ ፈወሰውም።

፱፡ ይህም፡በሆነ፡ጊዜ፡የቀሩትም፡ደግሞ፡ደዌ፡ የነበረባቸው፡በደሴት፡ ይመጡ፡ ይፈወሱም፡ ነበር።

፲፡ ደግሞም፡በብዙ፡ክብር፡ አከበሩነ። በሔድነም፡ ጊዜ፡ የመንገድ፡ ሰንቅ፡አዘጋጁልነ።

፲፩፡ ከሦስት፡ ወርም፡ በኋላ ፡ ሔድነ ፡ በእስክንድርያ፡ መርከብ፡ በደሴት፡ ከርሞ፡ በነበረው፡ የዲዮስኮሬም፡ዓላማ፡ ነበረበት።

፲፪፡ ወደ፡ሲራኩሲም፡ወረድነ፡ሦስት፡ቀንም፡ተቀመጥነባት።

፲፫፡ ከዚያም፡ አለፍነ፡ ወደ፡ ሬጊዩምም ፡ ደረስነ። ካንድ፡ቀንም፡በኋላ፡የደቡብ፡ነፋስ፡በነፈሰ፡ጊዜ፡በሁለተኛው፡ ቀን፡ ወደ፡ ጵቴኦሊ፡ መጣነ።

፲፬፡ ወንድሞችንም፡ አገኘነባት፡ እርሳቸውም፡ በለመኑነ፡ ጊዜ፡ ከርሳቸው ፡ ዘንድ፡ ሰባት፡ ቀን፡ ተቀመጥነ፡እንደዚሁም፡ ወደ፡ ሮሜ፡ መጣነ።

፲፭፡ ከዚያም ፡ ወንድሞች ፡ ወሬያችነን ፡ በሰሙ፡ ጊዜ፡ ሊቀበሉነ፡ ወጡ፡ ወደ፡ አጲውስ፡ ገበያ፡ ወደ፡ ሦስት፡ ኾዋኒትም። ጳውሎስም፡ ባያቸው፡ ጊዜ፡ እግዚአብሔርን፡ አመሰገነ፡ ልቡም፡ በረታ።

፲፮፡ በሮሜም፡ በመጣነ፡ጊዜ፡ የመቶ፡ አለቃው፡እሥረኞችን፡ለሠራዊቱ፡አለቃ፡አሳልፎ፡ሰጠ። ጳውሎስ፡ ግን፡ተፈቅዶለት፡ ነበረ፡ለብቻው፡ይቀመጥ፡ ዘንድ፡ከሚጠብቀው፡ ወታደር፡ ጋራ። ም፡ ፳፯፡ ፫።

፲፯፡ ከሦስት፡ ቀን፡ በኋላም፡ ጳውሎስ ፡ የአይሁድን፡ታላላቆች፡ አስጠራ። በመጡም፡ ጊዜ፡አላቸው። እላንት፡ ወንድማማቾች፡ ሰዎች፡ እኔ፡ አንዳች፡ አላደረግሁም፡ሕዝቡን፡ ያባቶችንም፡ ሕግ፡ የሚጣላ። በሮማውያን፡ እጅ፡ ታሥሬ፡ ተሰጠሁ፡ ከየሩሳሌም።

ም፡ ፳፫፡ ፩።

፲፰፡ እርሳቸውም፡ሊፈርዱብኝ፡መረመሩኝ፡ምንም፡ምክንያት፡ለሞት፡የሚያደርስ፡ ባያገኙ፡ ሊተውኝ፡ ወደዱ።

፲፱፡ አይሁድ፡ ግን፡ በተቃወሙኝ፡ ጊዜ ፡ *በቄሣር፡ እማጸን፡ዘንድ፡የግድ፡ አሉኝ። ወገኖቼንም፡ የምከስበት፡ ነገር፡ ኖሮኝ፡ አይደለም። *ም፡ ፳፭፡ ፲፪።

፳፡ ስለዚህም፡ ምክንያት ፡ ጸራኋችሁ ፡ እያችሁ፡ አጫውታችሁም፡ዘንድ። እኔ፡ ስለ፡ እሥራኤል፡ *ተስፋ፡በዚህ፡ሰንሰለት፡ታሥርያለሁና። *ም፡ ፳፮፡ ፮፡፯።

፳፩፡ እርሳቸው፡ግን፡አሉት። እኛ፡ስላንተ፡ጽፈት፡ አልተቀበልነም፡ ከይሁዳ፡ አገር። ከወንድሞችም፡አንድ፡ሰንኳ፡ ወርደ፡ክፉ፡ ነገር፡ባንተ፡ላይ፡ አላወራም፡ አልተናገረምም።

፳፪፡ ነገር፡ግን፡ የምታምነውን፡ ሃይማኖት፡ካንተ፡ እንሰማ፡ዘንድ፡ እንሻለን። የዚህስ፡ የመናፍቃን፡ወገ

ንብኝ፡ ዘንድ፡ ታውቋል፡ ሰዎች፡ እንዲጣሉት፡ በየስፍራው። ም፡ ፳፬፡ ፲፬፡፡ ሉቃ፡ ፪፡ ፴፬፡፡

፳፫፤ ቀንም፡ቊረጡለት፡ የሚበልጡትም፡ ወደር ሱ፡ መጡ፡ ወደፍረቡ፡ ስፍራ። በእግዚአብሔር፡ መ ንግሥትም፡ ኢየመሰከረ ፡ አጫወታቸው፡ ስለ፡የሱስ ም፡ ተናገራቸው፡ ከሙሴ፡ ኦሪት ፡ ከነቢያትም፡ ምስ ክር፡ኢያመጣ፡ ማልደ፡ጀምሮ፡ እስከ፡ ማታ፡ ድረስ።

፳፬፤ ተከፍለውም፡ ለነገሩ ፡ ታዘዙ፡ ሌሎችም፡ አ ላመኑትም።

፳፭፤ እርሱ፡በርሳቸውም፡ ባልተስማሙ፡ጊዜ፡ ሔ ደ፡ጳውሎስ፡አንዲት፡ነገር፡ከተናገረ፡በኋላ፡እንደሀ፡ ሲል።መልካም፡ ተናገረ፡ መንፈስ፡ ቅዱስ፡ በኢሳይያ ስ፡ ቃል፡ ላባቶቻችን፡ እንደሀ፡ ሲል።

፳፮፤ ወደዚህ፡ ሕዝብ፡ ሒድ፡ *በላቸውም። መስ ማት፡ ትሰማላችሁ፡አታስተውሉም፡ ማየትም፡ ታያ ላችሁ፡ አትመለከቱምም። *ኢሳ፡ ፮፡ ፱፡ ፲፡፡

፳፯፤ የዚህ፡ ሕዝብ፡ ልብ፡ ደንድንዋልና። ጆሮዎቻ ውም፡ ከመስማት ፡ ተደፍንዋልና ፡ ዓይኖቸውንም፡ ጨፍንዋልና። ዓይኖቸው፡እንዳያዩ፡ በጆሮዎቸውም፡ እንዳይሰሙ፡ በልባቸውም ፡ እንዳያስተውሉ ። እን ዳይመለሱም ፡ እፈውሳቸው ፡ ዘንድ።

፳፰፤ እንግዲህም፡በላንት፡ ዘንድ፡*የታወቀ፡ ይሁ ን፡የእግዚአብሔር፡ መድኃኒት፡ ለአሕዛብ፡ እንደ፡ተ ላከ፡እርሳቸውም፡ይሰሙታል። *ም፡ ፲፫፡ ፵፮፡ ፵፯፡፡

፳፱፤ ይህነንም፡ ነገር፡ በተናገረ፡ጊዜ፡ አይሁድ፡ ሔ ደ ፡ እጅግም ፡ መከራከር ፡ ነበረባቸው፡ እርሱ፡ በርሳ ቸው።

፴፤ ጳውሎስም፡ ሁለት፡አመት፡ ምሉ፡ ተቀመጠ፡ በክራይ፡ በተስማማው፡ቤት። ወደርሱም፡ ይመጡ፡ የነበሩትን፡ ሁሉ፡ ይቀበል፡ ነበር።

፴፩፤ የእግዚአብሔርን፡ መንግሥት፡ ኢየሰበከ፡የ ጌታንም ፡ የየሱስ ፡ ክርስቶስን ፡ ትምህርት ፡ ኢያስተ ማረ፡ በግልጽ፡ ሳይከለከል። ቍ፡ ፳፫፡፡

ተፈጸመ ፡ የሐዋርያት ፡ ስራ።

# የሐዋርያ ፡ የጳውሎስ ፡ መልእክት ፡ ወደ ፡ ሮሜ ፡ ሰዎች ።

ምዕራፍ፡ ፩፤

፩፤ ከጳውሎስ፡ ከየሱስ፡ ክርስቶስ፡ *ባርያ፡ ሐዋር ያ፡ ተብሎ፡ የተጸራ፡ የእግዚአብሔርን፡ ልጅ፡ ወንጌ ል፡ ለማስተማር፡ የተለየ። *የሐዋ፡ ፡ ፱፡ ፲፭፡፡ የሐዋ፡ ፲፫፡ ፪፡፡ ገላት፡ ፩፡ ፲፭፡፡

፪፤ አስቀድሞ፡ተስፋ፡ ያስደረገባት፡ በነቢያቱ፡በቅ ዱሳን፡ መጻሕፍት። ቲቶስ፡ ፩፡ ፪፡፡ ሮሜ፡ ፲፮፡ ፳፭፡ ፳፮፡፡

፫፤ ስለ፡ ልጁ፡ ከዳዊት፡ ዘር፡ የተወለደ፡ *በሥጋ። *፪፤ ሳሙ፡ ፯፡ ፲፪፡፡ ማቴ፡ ፳፪፡ ፵፪፡—፵፮፡፡ ሮሜ፡ ፱፡ ፭፡፡

፬፤ የእግዚአብሔር፡ ልጅም፡ ሁኖ፡ ተገለጠ፡ በኃይ ል፡እንደ፡ቅዱስነት፡መንፈስ፡ከሙታን፡ *በመነሣቱ። እርሱም፡ የሱስ፡ክርስቶስ፡ ጌታችን። *የሐዋ፡ ፲፫፡ ፴፫፡፡

፭፤ በርሱ፡ጸጋ፡የወሰድነ፡ *መልእክትም፡አሕዛብ፡ ሁሉ፡ ሊሰሙት፡ በስሙም፡ ሊያምኑበት። *የሐዋ፡ ፱፡ ፲፭፡፡ ሮሜ፡ ፲፭፡ ፲፰፡፡ ገላት፡ ፪፡ ፯፡ ፱፡፡

፮፤ ከርሳቸውም፡ደግሞ፡እላንት፡ ናችሁ፡ከየሱስ፡ ክርስቶስ፡ የተጸራችሁ።

፯፤ በሮሜ፡ ወደሚኖሩ፡ ሰዎች፡ ሁሉ፡ የእግዚአብ ሔር፡ ወዳጆች፡ *የተጸራችሁና፡ የተቀደሳችሁ። ጸጋ፡ ይሁንላችሁ፡ ሰላምም፡ ካምላክ፡ካባታችን፡ በጌታች ንም፡ከየሱስ፡ ክርስቶስ። *፩፡ ቆሮ፡ ፩፡ ፪፡፡ ኤፌ፡ ፪፡ ፩፡ ፪፡፡

፰፤ እኔ፡ ግን፡ አስቀድሜ፡ አምላኬን፡ አመሰግናለ ሁ፡ በየሱስ፡ ክርስቶስ፡ ስለ፡ ሁላችሁ፡ *ሃይማኖታች ሁ፡ ተሰምትዋልና፡በዓለሙ፡ ሁሉ። *ሮሜ፡ ፲፮፡ ፲፱፡፡ ፩፡ ተሰ፡ ፩፡ ፰፡፡

፱፤ እርሱ፡ *እግዚአብሔር፡ ይመሰክርልኛልና፡ ለር ሱ፡የምገዛ፡ በመንፈሴ፡ በልጁ፡ወንጌል። *ፊል፡ ፩፡ ፰፡፡ ኤፌ፡ ፩፡ ፲፮፡፡

፲፤ ሁልጊዜ፡እንደስባችሁ፡ቃል፡ሳልል፡በጸሎቴ፡ኢ የተማለልሁ፡ ምናልባት፡ መንገድ፡ ቢሆንልኝ፡ በእግ ዚአብሔር፡ ፈቃድ፡ ወደላንት፡ እመጣ፡ዘንድ። የሐዋ፡ ፲፱፡ ፳፩፡፡ ሮሜ፡ ፲፭፡ ፳፫፡ ፴፪፡፡

፲፩፤ እላንትን፡ ማየት፡እወዳለሁና፡መንፈሳዊ፡ስ ጦታ፡ አካፍላችሁ፡ ዘንድ፡ ስለ፡ መጽናናታችሁ። እር ስዋም፡ ይህችኛት፡በላንት፡ ባንድ፡ ደስ፡ይለኝ፡ዘንድ፡ በሃይማኖታችሁና፡ በሃይማኖቴ፡ *በመካከላችን፡ ያ ለች። የሐዋ፡ ፳፰፡ ፴፩፡፡ *፪፡ ጴጥ፡ ፩፡ ፩፡፡

፲፪፤ እኔም፡ እወዳለሁ፡ ታውቁ፡ ዘንድ፡ ወንድሞ ቼ፡ ሆይ፡ ብዙ፡ ጊዜ፡ እንደሰብሁ፡ ወደላንት፡ *እመ ጣ፡ ዘንድ፡ ነገር፡ ግን፡ እስከ፡ ዛሬ፡ ተከለከልሁ። ፩፡ ተሰ፡ ፪፡ ፲፰፡፡

፲፫፤ ደግሞ፡ በላንት፡ ፍሬ፡ ይሆንልኝ፡ ዘንድ፡ በሌ ሎች፡ አሕዛብ፡ እንደ፡ ሆነልኝ።

፲፬፤ የግድ፡ አለብኝ፡ የፅርዕን፡ ሰዎች፡ አስተምር፡ ዘንድ፡ አረማውያንንም፡ጠቢባንንም፡ ሰነፎችንም።

፲፭፤እንደሁም፡ደግሞ፡ደገባኛል፡አስተምራችሁ፡ ዘንድ፡ እላንት፡ በሮሜ፡ ያላችሁ።

፲፮፡ በክርስቶስ፡ ወንጌል፡ *አላፍርምና፡ የእግዚአ ብሔር፡ †ኃይል፡ ነውና፡ ለመድኃኒት፡ ለሚያምኑ፡ ሁ ሉ፡ ለአይሁድ፡ አስቀድሞ፡ ለአረማውያንም፡ ደግ ሞ። *መዝ፡ ፻፲፱፡ ፵፮። የሐዋ፡ ፲፫፡ ፵፮።
†፩፡ ቆሮ፡ ፩፡ ፲፰፡—፳፬።

፲፯፡ የእግዚአብሔር፡ *ጽድቅ፡በርሱ፡ይገለጣልና፡ ከሃይማኖት፡ ወደ፡ሃይማኖት። እንደ፡ ተጻፈ። †ጻድ ቅ፡ በሃይማኖት፡ ይድናል። *ሮሜ፡ ፫፡ ፳፩፡ ፳፪።
†አንባቆ፡ ፪፡ ፬።

፲፰፡ የእግዚአብሔር፡ ቍጣ፡ ከሰማይ፡ ይገለጣል ና፡ በሰው፡ ግፍ፡ ሁሉ፡ ላይ፡ በኃጢአታቸውም፡ እውነ ቱን፡ ኢያወቁ፡ የሚበድሉ።

፲፱፡ እግዚአብሔርን፡ማወቅ፡*ተገልጦላቸዋልና። እግዚአብሔር፡ እርሱ፡ ገልጦላቸዋልና።
*የሐዋ፡ ፲፬፡ ፲፭፡—፲፰። ፲፯፡ ፳፭፡—፳፯።

፳፡ የማትታወቅ፡ ባሕርዩ፡ ዓለም፡ ሳይፈጠር፡አስ ቀድሞ፡ በፍጥረት፡ ትታወቃለች፡ ትገለጣለችምና። እርስዋም፡ የዘላለም፡ ብርታቱ፡ አምላክነቱም፡ያለ፡ ምክንያት፡ ይሆኑ፡ ዘንድ። መዝ፡ ፲፱፡ ፪።
ዕብ፡ ፲፩፡ ፫።

፳፩፡ እግዚአብሔርን፡አውቀው፡እንደምላክነቱ፡ መጠን፡ አላከበሩትምና፡ አላመሰገኑትምም፡ ባሳባ ቸው፡ ጠፉ፡ እንጂ፡ *የማያስተውለውም፡ልባቸው፡ ጨለማ፡ ሆነ። *ኤፌ፡ ፬፡ ፲፰።

፳፪፡ *አስተዋዮች፡ ነን፡ ሲሉ፡ ሰነፉ። *ኤር፡ ፲፡ ፲፬።
፩፡ ቆሮ፡ ፩፡ ፳።

፳፫፡ የማይጠፋውንም፡ የእግዚአብሔርን፡ ክብ ር፡ በሚጠፋ፡ በሰው፡ መልክ፡ ምሳሌ፡ *ለወጡ፡ በወ ፎችም፡ በእንስሳም፡ በተንቀሳቃሾችም።
*ዘዳግ፡ ፬፡ ፲፭፡—፳፬።

፳፬፡ ስለዚህም፡እግዚአብሔር፡ *በልባቸው፡ፈቃ ድ፡ ወደ፡ ርኩስነት፡ አሳልፎ፡ ሰጣቸው፡ ሥጋቸውን፡ ሊያጐስቍሉ፡ በራሳቸው። *የሐዋ፡ ፲፬፡ ፲፮።
መዝ፡ ፹፩፡ ፲፫።

፳፭፡ የእግዚአብሔርን፡ እውነት፡በሐሰት፡ *ለው ጠዋልና፡ ለፍጥረትም፡ ሰገዱ፡ አመለኩትም፡ በፈጣ ሪዋ፡ ፈንታ፡ ለዘላለም፡ †የተመሰገነ። አሜን።
*መዝ፡ ፻፮፡ ፳። ሕዝ፡ ፰፡ ፲። †ም፡ ፱፡ ፭።

፳፮፡ ስለዚህም፡ እግዚአብሔር፡ ወደ፡ ኃፍረት፡ አሳልፎ፡ ሰጣቸው፡ወደ፡ጐስቍልናም። *ሴቶቻቸው ም፡ ለባሕርያቸው፡ የተሰራውን፡ ትተው፡ ለባሕርያ ቸው፡ የማይገባውን፡ አደረጉ። *ዘሌዋ፡ ፲፰፡ ፳፫።

፳፯፡ እንደሁም፡ ወንዶች፡ *ለባሕርያቸው፡ የሚ ገባውን፡ ሴቶችን፡ማድረግ፡ ትተው፡በፍትወታቸው፡ ተቃጠሉ፡እርስ፡በርሳቸው። *ወንዶችም፡በወንዶች፡ ነውር፡ አደረጉ፡ ለነውረኝነታቸውም፡ የሚገባውን፡ ብድራት፡በራሳቸው፡ ተቀበሉ።
*ዘሌዋ፡ ፲፰፡ ፳፪፡—፴። †፩፡ ቆሮ፡ ፮፡ ፱።

፳፰፡ እግዚአብሔርንም፡ለማወቅ፡ባልወደዱት፡ መጠን፡ እግዚአብሔር፡ ለማያስተውል፡ አእምሮ፡ አሳልፎ፡ ሰጣቸው፡ የማይገባውን፡ ያደርጉ፡ ዘንድ።

፳፱፡ እርሳቸውም፡ የመላባቸው፡ ግፍ፡ ሁሉ። ዝ ሙትም፡ ጽልም፡ንፍገትም፡ ክፋትም። ቅናት፡ የመ ላባቸው፡ ነፍስ፡ መግደልም። ክደትም፡ ሽንግላም፡ ክፉ፡ ልማድም፡ ማንጐርጐርም።

፴፡ ሐሜትም፡እግዚአብሔርን፡ የሚጸሉ፡ ተሳደ ቦች። ትዕቢተኞች፡ ተጓደጀች፡ አታላዮች፡ ክፋት፡ የ ሚያስቡ። ላባቶቻቸው፡ የማይታዘዙ።

፴፩፡ ማስተዋም፡ የሌለባቸው። ባልንጀርነትን፡ የማይወደ። ፍቅር፡የሌላቸው። መሐላ፡የማያጸኑ፡ ይቅር፡ የማይሉ።

፴፪፡ *የእግዚአብሔርን፡ ፍርድ፡የሚያውቁ፡እን ዲህ፡ያለውን፡ ስራ፡ የሚሰሩ፡ ሰዎች፡ ሞት፡ እንዲገ ባቸው፡እርስዋን፡ ብቻ፡ አይሰሩም፡ በሚሰርዋትም፡ ደስ፡ ይላቸዋል፡ እንጂ። *ሆሴ፡ ፯፡ ፪፡ ፫።

## ምዕራፍ፡ ፪።

፩፡ ስለዚህም፡ ምክንያት፡ ያለህም፡ አንተ፡ሰው፡ ሆይ፡ የምትፈርድ፡ ሌላውን፡ *በምትፈርድበት፡ ፍር ድ፡በራስህ፡ ትፈርዳለህና። አንተ፡ ያችን፡ስራ፡ ትሰራ ለህና፡ የምትፈርድባትን። *ማቴ፡ ፯፡ ፪።
ዮሐ፡ ፰፡ ፯።

፪፡ እናውቃለን፡ ግን፡ የእግዚአብሔር፡ ፍርድ፡ እ ውነት፡ እንደ፡ ሆነ፡ እንዲህ፡ ያለውን፡ ነገር፡ በሚሰ ሩ፡ሰዎች፡ ላይ።

፫፡ ምን፡ ይመስልሃል፡አንተ፡ ሰው፡ ይህነን፡በሚያ ደርግ፡ የምትፈርድ፡ አንተም፡ ትሰራታለህ። ወይስ፡ ከእግዚአብሔርን፡ ፍርድ፡ ታመልጣለህ።

፬፡ ደግሞስ፡ የቸርነቱንን፡ ባለጣግነት፡ ታቃላለህ፡ ርኅራኄም፡ ትዕግሥቱንም። ሳታውቅ፡ የእግዚአብ ሔር፡ ቸርነት፡ አንተን፡ ወደ፡ንስሐ፡ እንዲመራህ።
፪፡ ጴጥ፡ ፫፡ ፲፭።

፭፡ ነገር፡ ግን፡ ንስሐ፡ በማይገባ፡ በልብህ፡ ጽናት፡ መቅሠፍት፡ ታከማቻለህ፡ በቍጣ፡ ቀን፡የእግዚአብ ሔርም፡ እውነተኛ፡ ፍርድ፡ በሚገለጥበት፡ ቀን።

፮፡ ለሁሉ፡ ፍዳውን፡ *የሚሰጥ፡ ኢያንዳንዱ፡ እን ደ፡ ስራው፡ መጠን። *ኢሳ፡ ፵፡ ፲። ኤር፡ ፲፯፡ ፲።
መዝ፡ ፷፪፡ ፲፫። ማቴ፡ ፲፮፡ ፳፯። ፪፡ ቆሮ፡ ፭፡ ፲።
ዮሐ፡ ፭፡ ፳፱።

፯፡ በመልካም፡ ስራ፡ የሚታገሡ፡ ክብርም፡ ምስ ጋናም፡ የሚሹ፡ የማጠፋም፡ሕይወት፡ ለርሳቸው፡ የ ዘላለም፡ ሕይወት፡ ይሰጣቸዋል።

፰፡ *የማይታዘዙ፡ ግን፡ ከውነት፡ ጋራም፡ የማይተ ባበሩ፡ ለግፈኝነት፡ የሚታዘዙ፡ እንጂ። ለርሳቸው፡ †ቍጣ፡ መቅሠፍትም። *፪፡ ተሰ፡ ፩፡ ፰።
ሆሴ፡ ፬፡ ፬። †ዕዝ፡ ፰፡ ፳፪።

፱፡ አዘንም፡ ጭንቀትም፡ በሰው፡ሁሉ፡ነፍስ፡ ላይ፡

ነው፡ ክፉ፡ በሚያደርግ። *አይሁዳዊም፡ ቢሆን፡ አስቀድሞ፡ ወይም፡ አረማዊ። *ም፡ ፩፡ ፲፮፡፡ ፫፡ ፱፡፡

፲፡ ክብርም፡ ምስጋናም፡ ሰላም፡ መልካም፡ ለሚያደርግ፡ ነው። አይሁዳዊም፡ቢሆን፡አስቀድሞ፡ ወይም፡ አረማዊ።

፲፩፡ እግዚአብሔር፡ *የሰውን፡ፊት፡ አይቶ፡ አያደላምና። *የሐዋ፡ ፲፡ ፴፬፡፡ ፩፡ ጴጥ፡ ፩፡ ፲፯፡፡

፲፪፡ ሕግ፡ ሳይሰራላቸው፡የበደሉ፡ሁሉ፡ያለ፡ ሕግ፡ ይጠፋሉና። ሕግም፡ ተሰርቶላቸው፡ የበደሉ፡ በሕግ፡ ይፈረድባቸዋል።

፲፫፡ ሕግ፡የሚሰሙ፡ በእግዚአብሔር፡ ዘንድ፡ ጻድቃን፡ አይደሉምና፡ ሕግን፡ *የሚሰሩ፡ እርሳቸው፡ይጸድቃሉ፡እንጂ። *ማቴ፡ ፯፡ ፳፩፡፡ ፩፡ ዮሐ፡ ፫፡ ፯፡፡

፲፬፡ ሕግም፡ የሌላቸው፡ አሕዛብ፡ከባሕርያቸው፡ ሕግ፡ ቢያደርጉ። እለዚያ፡ ሕግ፡ ባይኖራቸው፡ ለራሳቸው፡ ሕግ፡ ናቸው። የሐዋ፡ ፲፡ ፴፭፡፡

፲፭፡ ሕግንም፡ ማድረግ፡ ይገልጣሉ፡ በልባቸው፡ የተጻፈውን። ልባቸውም፡ ይመሰክርላቸዋል፡ አሳባቸውም፡ይገሥጻቸዋል፡እርሱ፡በርሳቸው። ም፡ ፩፡ ፴፪፡፡

፲፮፡ ፍርዳቸውም፡ ይሆናል፡ እግዚአብሔር፡ በሰው፡ ምሥጢር፡ በሚፈርድበት፡ *ቀን፡ በየሱስ፡ ክርስቶስ። እኔ፡ በወንጌል፡ እንደስተማርሁ።
*መክ፡ ፲፪፡ ፲፬፡፡ ማቴ፡ ፳፭፡ ፴፩፡፡

፲፯፡ ነገር፡ ግን፡ አንተ፡ሰው፡አይሁዳዊ፡ የምትባል፡ በኦሪትም፡ የምታርፍ፡ በእግዚአብሔርም፡ የምትመካ።

፲፰፡ ፈቃዱንም፡ የምታውቅ፡ በኦሪትም፡ የተሰራውን፡ ለይተህ፡ የምታስተውል።

፲፱፡ ፈጽመህም፡ በራስህ፡ ታምነሃል፡ የዕውራን፡ መሪ፡ እንደ፡ ሆንህ፡ ብርሃን፡ በጨለማ፡ ላሉ።
ማቴ፡ ፲፭፡ ፲፬፡፡

፳፡ ለሰነፎች፡ ገሣጺ፡ ለሕፃናት፡ አስተማሪ። የእውቀትና፡የእውነትም፡መልክ፡በኦሪት፡ላንት፡ የሆነ።

፳፩፡ አንተ፡ ሆይ፡ሌላውን፡ *የምታስተምር፡ በውኑ፡ ራስህን፡ አታስተምር። አትሰረቁ፡ ትላለህ፡ አንተም፡ ትሰርቃለህን። *መዝ፡ ፶፡ ፲፮—፳፫፡፡
ማቴ፡ ፳፫፡ ፫፡ ፬፡፡

፳፪፡ አታመንዝሩ፡ ትላለህ፡ አንተም፡ ታመነዝራለህን። ጣዖት፡ ትጸየፋለህ፡ አንተም፡ የቤተ፡ እግዚአብሔርን፡ እቃ፡ ትሰርቃለህን።

፳፫፡ በኦሪት፡ *ትጓደዳለህ፡ አንተም፡ ኦሪትን፡ በመተላለፍህ፡ እግዚአብሔርን፡ ትንቃለህን።
*ም፡ ፱፡ ፱፡፡

፳፬፡ የእግዚአብሔር፡ ስም፡ *ስለአንተ፡ ይሰደባል፡ በአሕዛብ፡ ዘንድ፡ እንደ፡ ተጻፈ። *ኢሳ፡ ፶፪፡ ፭፡፡
ሕዝ፡ ፴፮፡ ፳—፳፫፡፡ ፩፡ ጢሞ፡ ፮፡ ፩፡፡

፳፭፡ ግዝረት፡ ይረባልና፡ በሕግ፡ ያለውን፡ የጠበቅህ፡ እንደ፡ ሆንህ። ሕግንስ፡ ከተላለፍህ፡ *ግዝረትህ፡ ሸፍን፡ ይሆንብሃል። *ኤር፡ ፬፡ ፬፡፡ ፱፡ ፳፭፡ ፳፮፡፡

፳፮፡ ሰውም፡በሸፍን፡ተቀምጦ፡ሕግ፡ቢጠብቅ፡ሸፍንነቱ፡ለግዝረት፡ይቈጠርለት፡የለምን። የሐ፡ ፳፡ ፮፡፡

፳፯፡ ሳይገዘርም፡ ሕግ፡ የሚጠብቅ፡ አይፈርድብህን፡ ባንተ፡ በመጽሐፍና፡ በግዝረት፡ ሕግ፡ አፍራሽ፡ የምትሆን።

፳፰፡ በግልጽ፡አይሁዳዊ፡የሆነ፡ አይሁዳዊ፡ አይደለምና። ግዝረትም፡ በሥጋ፡ የተገለጠ፡ ግዝረት፡ አይደለምና። ዮሐ፡ ፰፡ ፴፱፡፡

፳፱፡ በሥውር፡ አይሁዳዊ፡ የሆነ፡ እርሱ፡ አይሁዳዊ፡ ነው፡ እንጂ። ግዝረትም፡ *የልብ፡ ግዝረት፡ ነው፡ በመንፈስ፡ በመጽሐፍም፡አይደለም። †ምስጋናውም፡ ከሰው፡ አይደለም፡ ከእግዚአብሔር፡ ነው፡ እንጂ። *ዘዳግ፡ ፴፡ ፮፡፡ ቈላ፡ ፪፡ ፲፩፡፡ †ዮሐ፡ ፭፡ ፵፬፡፡

## ምዕራፍ፡ ፫፡

፩፡ የአይሁዳዊ፡ ጥቅሙ፡ ግን፡ ምንድር፡ ነው። የግዝረትስ፡ ትርፉ፡ ምንድር፡ ነው።

፪፡ ትርፍነቱ፡ በሁሉ፡ ታላቅ፡ ነው። ከዚያም፡ *አስቀድሞ፡ የእግዚአብሔር፡ ነገር፡ ለርሳቸው፡አደራ፡ ተሰጥትዋልና። *ም፡ ፱፡ ፬፡፡ ዘዳግ፡ ፬፡ ፯፡ ፰፡፡
መዝ፡ ፻፵፯፡ ፲፱፡ ፳፡፡

፫፡ ከርሳቸው፡ ወገንስ፡ የማያምን፡ ቢኖር፡ ምን፡ ይጐዳል። የርሳቸው፡ *አለማመንን፡ የእግዚአብሔርን፡ እውነት፡ ያስቀራል። *ም፡ ፱፡ ፮፡፡ ፲፩፡ ፳፱፡፡
፪፡ ጢሞ፡ ፪፡ ፲፫፡፡ ዘኍል፡ ፳፫፡ ፲፱፡፡

፬፡ አይደለምን፡ ነገር፡ ግን፡ *እግዚአብሔር፡እውነተኛ፡ ይሁን፡ ሰውም፡ ሁሉ፡ †አሰተኛ፡ እንደ፡ ተጻፈ። በነገርህ፡ እውነተኛ፡ ትሆን፡ ዘንድ፡ በተፈረድህም፡ ጊዜ፡ ታሸንፍ፡ ዘንድ። *ዮሐ፡ ፫፡ ፴፫፡፡ ቲቶ፡ ፩፡ ፪፡፡
†መዝ፡ ፶፩፡ ፮፡፡ ፳፪፡ ፲፡፡ ፻፲፮፡ ፲፩፡፡

፭፡ የኛ፡ ኀጢአት፡ግን፡የእግዚአብሔርን፡ ጽድቅ፡ የሚገልጥ፡ከሆነ፡ ምን፡ እንላለን። እንጃ፡ እግዚአብሔር፡ ቍጣ፡ ቢያመጣ፡ ግፈኛ፡ ይሁንን። እንደ፡ሰው፡ እናገራለሁ።

፮፡ አይደለም። እንኪያስ፡ እግዚአብሔር፡ *እንዴት፡ በዓለም፡ ይፈርዳል። *ዘፍ.ጥ፡ ፲፰፡ ፳፭፡፡

፯፡ እግዚአብሔርም፡እውነተኝነት፡ለክብሩ፡ በሐሰቴ፡ ከላቀ፡ ስለ፡ ምን፡ ይፈረድብኛል፡ደግሞ፡እ'ነደ፡ ኀጢአተኛ።

፰፡ እንደሚሰድቡኑ፡አይደለም፡ሰዎችም፡ እንዲጠረጥሩ፡ እንድንል፡ *ክፉ፡እናድርግ፡ መልካም፡ እንዲመጣ። ለለዚያም፡ ፍርዳቸው፡ የሚገባ፡ ነው።
*ም፡ ፮፡ ፩፡ ፪፡፡

፱፡ እንጊዲህ፡ ምንድር። እኛን፡ ከርሳቸው፡ እንበልጣለን። አይደለም። አስቀድሞ፡ ፈርደናልና፡ በአይሁድ፡በአረማውያንም፡ደግሞ፡ *ሁሉ፡ከኀጢአት፡ በታች፡ እንደ፡ ሆኑ። *ም፡ ፩፡ ና፡ ፪፡፡ ፲፩፡ ፴፪፡፡
ገላት፡ ፫፡ ፳፪፡፡

፲፡ እንደ፡ ተጻፈ*። ጻድቅ፡ የለምን፡አንድ፡ስንኳ።
፲፩፡ የሚያስተውል፡ የለም፡ እግዚአብሔርንም፡ የሚሻ። *መዝ፡ ፲፬፡ ፫፡፡ ፶፫፡ ፬፡፡
፲፪፡ ሁሉ፡ ዓመፁ፡ ጠመመሙም። መልካም፡ የሚያደርግ፡ የለም፡ አንድ፡ ስንኳ።
፲፫፡ *ጕሮሮዋቸው፡ የተከፈተ፡ መቃብር፡ ነው። ባንደበታቸው፡ሸነገሉ፡የእርጉ፡ †መርዝ፡በከንፈራቸው፡ ነው። *መዝ፡ ፭፡ ፲፡፡ †መዝ፡ ፻፵፡ ፬፡፡
፲፬፡ *አፋቸውም፡ መርገም፡ መራራም፡ መልተበታል። *መዝ፡ ፲፡ ፯፡፡
፲፭፡ *እግራቸው፡ የፈጠነ፡ ነው፡ ደም፡ ለማፍሰስ። *ኢሳ፡ ፶፱፡ ፯፡፡
፲፮፡ መጥፋት፡ ጕስቍልናም፡ በመንገዳቸው።
፲፯፡ የሰላምንም፡ መንገድ፡ አለወቋትም።
፲፰፡ እግዚአብሔርንም፡ *መፍራት፡ ባደናቸው፡ ፊት፡ የለም። *መዝ፡ ፴፮፡ ፩፡፡ ዘፍ.ጥ፡ ፳፡ ፲፩፡፡
፲፱፡ እኛ፡ ግን፡ እናውቃለን፡ በኦሪት፡ የተነገረው፡ ሁሉ፡ ለኦሪት፡ ሰዎች፡ እንደ፡ ተናገረ። *አፍ፡ ሁሉ፡ እንዲዘጋ፡ ዓለሙም፡ ሁሉ፡ ከእግዚአብሔር፡ ፍርድ፡ በታች፡ እንዲሆን። *ም፡ ፪፡ ፲፪፡፡ ገላት፡ ፫፡ ፳፪፡፡ ሕዝ፡ ፲፮፡ ፷፫፡፡
፳፡ ኦሪትን፡ በማድረግ፡ *አይጸድቅምና፡ ሰው፡ ሁሉ፡ በፊቱ። በኦሪት፡ ኀጢአት፡ ትታወቃለች። *መዝ፡ ፻፵፫፡ ፪፡፡ ገላት፡ ፪፡ ፲፮፡፡
፳፩፡ ዛሬ፡ ግን፡ ያለ፡ኦሪት፡ የእግዚአብሔር፡ ጽድቅ፡ ተገለጠ፡ *ከኦሪት፡ ከነቢያትም፡ ተመስክሮለት። *የሐዋ፡ ፲፡ ፵፫፡፡
፳፪፡ የእግዚአብሔር፡ጽድቅ፡በሃይማኖት፡ነውና፡ በየሱስ፡ ክርስተስ፡ በርሱ፡ ላመኑ፡ ሁሉ፡ በርሱም፡ ባመኑ፡ ሁሉ፡ ላይ።
፳፫፡ በዚህም፡ *ልዩ፡ የለም። ሁሉ፡ †በድለዋልና፡ የእግዚአብሔርንም፡ ክብር፡ አጥዋልና። *ቈ፡ ፱፡፡ ገላት፡ ፫፡ ፳፪፡ ፳፫፡፡ ፩፡ ነገሥ፡ ፰፡ ፵፮፡፡
፳፬፡ *በከንቱም፡ ጸደቁ፡ በጸጋው። በየሱስ፡ ክርስተስ፡ በሚሆን፡ በማዳኑ። *ኤፌ፡ ፪፡ ፰፡፡
፳፭፡ እግዚአብሔር፡ አስቀድሞ፡ *መስተስረያ፡ ያደረገው፡ በሃይማኖት፡ በደሙ። ጽድቁ፡ ይገለጥ፡ ዘንድ፡ ስለ፡ ቀደመችው፡ ኀጢአት፡ ስርየት፡ በእግዚአብሔር፡ ትዕግሥት። *ዘሌዋ፡ ፲፮፡ ፲፪፡—፲፭፡፡ ዕብ፡ ፬፡ ፲፮፡፡
፳፮፡ ጽድቁ፡እንዲታወቅ፡በዚህ፡ዘመን። እርሱ፡ ጻድቅ፡ ይሆን፡ ዘንድ፡ በየሱስ፡ ክርስተስ፡ የሚያምንንም፡ የሚያጸድቅ።
፳፯፡ ትምክህት፡ *ወዴት፡ ነው። ቀረ፡ እንጅ። በምን፡ ሕግ፡ በማድረግን፡ ሕግ፡ ነው። አይደለም። በሃይማኖት፡ ሕግ፡ እንጅ። *፩፡ ቆሮ፡ ፩፡ ፳፱፡ ፴፩፡፡
፳፰፡ እኛም፡ *እንላለን፡ሰው፡በሃይማኖት፡እንዲጸድቅ፡ ሕግንም፡ በመሰራት፡ አይደለም። *ገላት፡ ፪፡ ፲፮፡—፳፩፡፡
፳፱፡ በውኑ፡ እግዚአብሔር፡ለአይሁድን፡ ብቻ፡ አምላክ፡ ነው። እርሱ፡ *ለአሕዛብም፡አይደለምን፡ ደግሞ። አዎን፡ ደግሞ፡ ለአሕዛብ፡ ነው። *ም፡ ፲፡ ፲፪፡፡ መል፡ ፪፡ ፲፡፡ ፩፡ ቆሮ፡ ፲፪፡ ፮፡፡
፴፡ አንድ፡ እግዚአብሔር፡ ነውና፡ ግዙርን፡ ከሃይማኖት፡ የሚያጸድቅ፡ ያልተገዘረንም፡ በሃይማኖት። ም፡ ፬፡ ፲፩፡ ፲፪፡፡
፴፩፡ ሕግን፡እንሻርን፡ስለ፡ሃይማኖት፡አይደለም። ሕግን፡ *እናጸናለን፡ እንጅ። *ም፡ ፰፡ ፬፡፡ ማቴ፡ ፭፡ ፲፯፡—፵፰፡፡

ምዕራፍ፡ ፬፡

፩፡ እንኪያስ፡ምን፡ እንላለን፡ አብርሃም፡ አባታችን፡ እንዳገኘው፡ እንደ፡ ሥጋ።
፪፡ አብርሃምስ፡ በምግባሩ፡ ቢጸድቅ፡ ትምክህት፡ አለው፡ ነገር፡ ግን፡ ከእግዚአብሔር፡ ዘንድ፡ አይደለም።
፫፡ *መጽሐፍም፡ ምንድር፡ ይላል። አብርሃም፡ በእግዚአብሔር፡አመነ፡ጽድቅም፡ሁና፡ተቈጠረለት። *ዘፍ.ጥ፡ ፲፭፡ ፮፡፡ ገላት፡ ፫፡ ፮፡፡
፬፡ የሚሰራ፡ ግን፡ ዋጋው፡ አይቈጠርለትም፡ እንደ፡ያው፡ እንደ፡ ሰጠው፡ እንደ፡ *ዕዳ፡ ነው፡ እንጅ። *ም፡ ፲፩፡ ፮፡፡ ማቴ፡ ፳፡ ፯፡ ፲፬፡፡
፭፡ የማይሰራ፡ ግን፡ ኀጢአተኛውንም፡ *በሚያጸድቅ፡ የሚያምን፡ ሃይማኖቱ፡ ጽድቅ፡ ሁና፡ ይቈጠርለታል። ም፡ ፫፡ ፳፰፡፡
፮፡ ዳዊት፡ እንዳለ፡ ደግሞ፡ ሰውን፡ *ሲያመስግን፡ እግዚአብሔር፡ ጽድቅ፡ የሚቈጥርለት፡ ሳይሰራ። *መዝ፡ ፴፪፡ ፩፡ ፪፡፡
፯፡ እንዲህ፡ ሲል፡ የተመሰገኑ፡ ናቸው፡ ኀጢአታቸው፡ የተሰረየላቸው። ስሕተታቸውም፡ የተሠወረላቸው። መዝ፡ ፴፪፡ ፩፡ ፪፡፡
፰፡ ምስጉን፡ሰው፡እግዚአብሔር፡ኀጢአቱን፡የማይቈጥርበት።
፱፡ ይህ፡ ምስጋና፡ ግን፡ ለግዙራንን፡ ብቻ፡ ነው፡ ወይስ፡ ላልተገዘሩ፡ ደግሞ። እንላለንና፡ ሃይማኖት፡ ለአብርሃም፡ጽድቅ፡ ሁና፡ ተቈጠረለት።
፲፡ እንዴትም፡ ተቈጠረለት። በግዝረትን፡ ሳለ፡ ነው፡ ወይስ፡ በቍላፍነት። በግዝረት፡ አይደለም፡ በቍላፍነት፡ እንጅ።
፲፩፡ የግዝረትንም፡ ምልክት፡ወሰደ፡ *ማሕተም፡ እንዲሆን፡ በቍላፍነት፡ ሳለ፡ ለሆነው፡ ለሃይማኖቱ፡ ጽድቅ። አባት፡ ይሆን፡ ዘንድ፡ በቍላፍነት፡ ላመኑ፡ ሁሉ፡ ለርሳቸው፡ ደግሞ፡ ጽድቅ፡ ይቈጠርላቸው፡ ዘንድ። *ዘፍ.ጥ፡ ፲፯፡ ፲፡ ፲፩፡፡
፲፪፡ አባትም፡ ለግዙራን፡ ለተገዘሩ፡ ብቻ፡ *አይደለም። ያባታችነን፡ የአብርሃምን፡ ሃይማኖቱን፡ ፍለጋ፡ ለሚከተሉ፡ እንጅ፡ ደግሞ፡ በቍላፍነት፡ የነበረውን። *ማቴ፡ ፫፡ ፱፡፡

፲፫፡ *ተስፋ፡ ለአብርሃም፡ በኦሪት፡ የመጣለት፡ አይደለምና፡ ለዘሩም፡ ዓለምን፡ ይወርስ፡ ዘንድ፡ በሃይማኖቱ፡ ጽድቅ፡ እንጂ። *ዘፍ፡ ፲፯፡ ፲፯፡፡

፲፬፡ የኦሪት፡ ሰዎችስ፡ *ወራሾች፡ ቢሆኑ፡ ሃይማኖት፡ ከንቱ፡ ሆነ፡ ተስፋም፡ አይጠቀመም።
*ገላት፡ ፫፡ ፲፰፡፡

፲፭፡ ኦሪት፡ *ቍጣ፡ ታመጣላችና። ኦሪትስ፡ ባትኖር፡ ኃጢአት፡ ባልኖርም። *ም፡ ፫፡ ፳፡፡ ፭፡ ፲፫፡፡
፯፡ ፳፡ ፲፡፡

፲፮፡ ስለዚህም፡በሃይማኖት፡ ሆነ፡በጸጋው፡ይሆን፡ ዘንድ፡ ተስፋም፡ ጸንቶ፡ ይኖር፡ ዘንድ፡ *ለዘሩ፡ ሁሉ። ከኦሪት፡ ወገን፡ ለሆነ፡ብቻ፡ አይደለም፡ከአብርሃም፡ ሃይማኖት፡ ወገን፡ ለሆነ፡ እንጂ፡ ደግሞ፡ ለሁላችን፡ አባት፡ የሆነ። *ገላት፡ ፫፡ ፲፰፡፡

፲፯፡ እንደ፡ ተጻፈ። *አባት፡ አደረግሁህ፡ ለብዙ፡ አሕዛብ፡ ባመነበት፡ በእግዚአብሔር፡ ፊት። ሙታንን፡ የሚያስነሣ፡ ያልነበረውንም፡ እንደ፡ ነበረ፡ የሚጠራ። *ዘፍ፡ ፲፯፡ ፭፡፡

፲፰፡ ተስፋ፡ ባልሆነው፡ ጊዜ፡ በተስፋ፡ ያመነ፡ ለብዙ፡ አሕዛብ፡ አባት፡ ይሆን፡ ዘንድ። እንደ፡ ነገረው፡ ዘርህ፡ *እንደሀ፡ ይሁን፡ ብሎ። *ዘፍ፡ ፲፭፡ ፭፡፡

፲፱፡ በሃይማኖቱም፡ አልደከመም፡ ሙቶ፡ የነበረውንን፡ ሥጋውን፡ *አላየምም፡ የመቶ፡ አመት፡ ነበረና። እንደሁም፡ የሳራን፡ የሞተውንን፡ ማሕፀን።
*ዘፍ፡ ፲፯፡ ፲፯፡፡

፳፡ በእግዚአብሔርም፡ተስፋ፡አልተጠራጠረም፡ ካለማመን፡ በሃይማኖት፡ጸና፡እንጂ፡ለእግዚአብሔርም፡ ምስጋና፡ *ሰጠ። *ዕብ፡ ፲፩፡ ፯፡ ፲፩፡፡

፳፩፡ ልቡም፡ ታመነ፡ እግዚአብሔር፡ተስፋ፡የሰጠውን፡ *ይሰራ፡ ዘንድ፡ እንዲችል። *መዝ፡ ፻፲፭፡ ፫፡፡
ኢሳ፡ ፵፱፡ ፩፡፡

፳፪፡ ስለዚህም፡ ጽድቅ፡ ሁኖ፡ ተቈጠረለት።
ቍ፡ ፫፡፡

፳፫፡ ለርሱም፡ *ለብቻው፡አልተጻፈም፡ እንደ፡ ተቈጠረለት። *ም፡ ፲፭፡ ፬፡፡

፳፬፡ ለኛም፡ እንጂ፡ ለተቈጠረልን፡ እኛ፡ ያመነ፡ ጌታችንን፡ የሱስ፡ ክርስቶስ፡ ከሙታን፡ *ባስነሣው።
*የሐዋ፡ ፪፡ ፳፬፡፡

፳፭፡ እግዚአብሔር፡ አሳልፎ፡የሰጠው፡ስለ፡ኃጢአታችን፡ ሊያጸድቀነም፡ የተነሣ። ኢሳ፡ ፶፫፡ ፬፡ ፭፡፡
፩፡ ቆሮ፡ ፲፭፡ ፲፯፡፡

· ምዕራፍ፡ ፭፡

፩፡ በሃይማኖትም፡ ከጸደቅን፡ *ሰላም፡ አለን፡ ከእግዚአብሔር፡ ዘንድ፡ በጌታችን፡ በየሱስ፡ ክርስቶስ።
*ኢሳ፡ ፶፫፡ ፭፡፡ ዮሐ፡ ፲፮፡ ፲፫፡፡

፪፡ በርሱ፡ *መግባት፡ የሆነልን፡ በሃይማኖት፡ ወደዚች፡ ጸጋ፡ እኛ፡ የቆምንባት። በእግዚአብሔርም፡ ክብር፡ ተስፋ፡ እንመካለን። *ኤፌ፡ ፫፡ ፲፪፡፡

፫፡ ይህም፡ ብቻ፡ አይደለም፡ *በሐዘን፡ እንመካለን፡ እንጂ፡ ደግሞ። ሐዘን፡ ትዕግሥት፡ እንደ፡ ያመጣልን፡ አውቀን። *ያዕ፡ ፩፡ ፪፡፡

፬፡ *ትዕግሥትም፡መፈተን፡መፈተንም፡አለኝታ።
ያዕ፡ ፩፡ ፫፡፡

፭፡ *አለኝታም፡ አያሳፍርም፡ የእግዚአክሔር፡ ፍቅር፡ በልባችን፡ ፈሳለችና፡ በመንፈስ፡ ቅዱስ፡ ለኛ፡ የተሰጠ። *ዕብ፡ ፮፡ ፲፰፡ ፲፱፡፡

፮፡ በድካማችን፡ ሳለን፡ በዚህ፡ ዘመን፡ ክርስቶስ፡ ስለኛ፡ ስለ፡ ኃጢአተኞች፡ ሙትዋልና።

፯፡ አንድ፡ ሰውስ፡ ስለ፡ ጻድቅ፡ *የሚሞት፡ ይገኛልን። እጅግ፡ የሚደፍር፡ ቢገኝ፡ ስለ፡ በጎ፡ ሰው፡ ይሞታልና። *ዮሐ፡ ፲፭፡ ፲፫፡፡

፰፡ በዚህም፡እግዚአብሔር፡በኛ፡ *ፍቅሩን፡አስታወቀው፡ ገና፡ ኃጢአተኞች፡ ስንሆን፡ክርስቶስ፡ ስለኛ፡ ሙትዋልና። *ዮሐ፡ ፫፡ ፲፮፡—፳፩፡፡

፱፡ እንዴትም፡ እጅግ፡ ከጸደቅን፡ በደሙ፡ ዛሬ፡ በርሱ፡ እንድናለን፡ ከቍጣ። ም፡ ፩፡ ፲፰፡ ፲፱፡፡ ፪፡ ፳፡፡

፲፡ እግዚአብሔርም፡ ጸላቶቹ፡ስንሆን፡ በልጁ፡ ሞት፡ ከታረቅን። የግድ፡ እንዴት፡ ከታረቅን፡ በኋላ፡ያድነን፡ በሕይወቱ። ም፡ ፳፡ ፯፡፡

፲፩፡ ይህም፡ ብቻ፡ አይደለውም፡ በእግዚአብሔርም፡ደግሞ፡ እንመካለን፡ እንጂ። በጌታችን፡ በየሱስ፡ ክርስቶስ፡ ዛሬ፡ በርሱ፡ መታረቅ፡ የወሰድን።

፲፪፡ ስለዚህም፡ ኃጢአት፡ ወደ፡ ዓለም፡ እንደ፡ ገባች፡ ባንድ፡ ሰው፡ ምክንያት፡ በኃጢአትም፡ ሞት፡ ገባ። እንደሁም፡ *ሞት፡ አለፈ፡በሰው፡ ሁሉ፡ላይ፡ ሁሉ፡ በድለዋልና። *ም፡ ፮፡ ፳፫፡፡ ዘፍ፡ ፪፡ ፲፯፡፡

፲፫፡ ኦሪት፡ እስክትመጣ፡ ድረስ፡ ኃጢአት፡ በዓለም፡ ነበረችና፡ ኃጢአት፡ ግን፡ ሁና፡ አትቈጠርም፡ *ኦሪት፡ ባትሆን። *ም፡ ፬፡ ፲፭፡፡

፲፬፡ ነገር፡ ግን፡ ሞት፡ ሠለጠነ፡ከአደም፡ ጀምሮ፡ እስከ፡ ሙሴ፡ደግሞ፡ ኃጢአትም፡ ባልሰሩት፡ ላይ፡ *በአደም፡ ኃጢአት፡ ምሳሌ። እርሱም፡ ያለን፡ ይመጣ፡ ዘንድ፡ ያለውን፡ የሚመስል።
*፩፡ ቆሮ፡ ፲፭፡ ፳፩፡ ፳፪፡ ፵፭፡ ፶፭፡፡

፲፭፡ ነገር፡ግን፡ጸጋው፡ እንደ፡ኃጢአቱ፡መጠን፡አይደለም፡ *ባንድ፡ ሰው፡ ኃጢአት፡ ብዙ፡ ሰዎች፡ ሙተዋልና። እጅግም፡ደግሞ፡ የእግዚአብሔር፡ ጸጋ፡ ስጦታውም፡ ባንድ፡ ሰው፡ †ጸጋ፡ በየሱስ፡ ክርስቶስ፡ እጅግ፡ ትበዛለች፡ በብዙ፡ ሰዎች፡ ላይ።
*፩፡ ቆሮ፡ ፲፭፡ ፳፪፡፡ †ዮሐ፡ ፩፡ ፲፮፡ ፲፯፡፡

፲፮፡ ስጦታዪቱም፡ እንደንድ፡ ሰው፡ ኃጢአት፡ መጠን፡ አይደለችም። ፍርድ፡ ካንድ፡ ሰው፡ ነበረና፡ ለኲነኔ፡ ጸጋ፡ ግን፡ ከብዙ፡ ኃጢአት፡ ለመጸደቅ።

፲፯፡ ባንድም፡ ሰው፡ ኃጢአት፡ሞት፡ከሠለጠነ፡ እንዴት፡ እጅግ፡ የጸጋን፡ ብዛት፡ የወሰዱ፡ የጽድቅንም፡ ስጦታ፡ በሕይወት፡ ይነግሣሉ፡ ባንድ፡ ሰው፡ በየሱስ፡ ክርስቶስ።

፲፰፥ ባንድ፡ሰውም፡ በሆነች፡ ኃጢአት፡ በሰው፡*ሁሉ፡ ላይ፡ ፍርድ፡እንደ፡ መጣ፡ለኵነኔ፡እንደሁ፡ባንድ፡ ሰው፡ ጽድቅ፡ ጸጋ፡ በሁሉ፡ ላይ፡ መጣ፡ ለጽድቅና፡ ለሕይወት።
*፩፥ ቆሮ፡ ፲፭፥ ፳፪፡፡

፲፱፥ ባንድ፡ ሰውም፡ አለመታዘዝ፡ ብዙ፡ ኃጢአተኞች፡ እንደ፡ ሆኑ። እንደሁም፡ ባንድ፡ ሰው፡ መታዘዝ፡ ብዙ፡ ጻድቃን፡ ይሆናሉ።
ኢሳ፥ ፶፫፥ ፲፩፥
ፊል፡ ፪፥ ፰፡፡

፳፥ *ኦሪትም፡ገባች፡ ኃጢአት፡ትበዛ፡ ዘንድ። ኃጢአት፡ግን፡ ከበዛች፡ ዘንድ፥ ከዚያ፡ ተረፈች፡ ጸጋ፡ በዛችም። *ም፡ ፬፥ ፲፭፡፡ ፯፥ ፰፡፡ ገላት፡ ፫፥ ፲፱፡፡ ሮሜ፡፮፥፲፬፡፡

፳፩፥ *ኃጢአት፡ በሞት፡እንደ፡ ገዛች፡ እንደሁም፡ ጸጋ፡በጽድቅ፡ትገዛ፡ ዘንድ፡ ለዘላለም፡ ሕይወት፡ በጌታችን፡በየሱስ፡ ክርስቶስ። ቆ፡ ፲፯፡፡ *ም፡ ፮፥ ፳፫፡፡

## ምዕራፍ፡ ፮፥

፩፥ ምን፡እንላለን፡እንኪያህ። በኃጢአት፡ *እንኖርን፡ጸጋ፡እንድትበዛ። *ም፡፫፥ ፭፥—፰፡፡ ገላት፡፪፥፲፯፡፡

፪፥ አይደለም። እኛ፡ ለኃጢአቱ፡ ፈጽመን፡ *የሞትነ፡ እንደት፡ ደግሞ፡ በርስዋ፡ እንኖራለን።
*ገላት፡ ፮፥ ፲፬፡፡

፫፥ ወይስ፡ *አታውቁምን፡እኛ፡ በየሱስ፡ክርስቶስ፡ የተጠመቅነ፡ በሞቱ፡ እንደ፡ ተጠመቅነ።
*ገላት፡ ፫፥ ፳፯፡፡ ቆለ፡ ፪፥ ፲፪፡፡

፬፥ እንኪያህ፡በጥምቀት፡ከርሱ፡ጋራ፡ ተቀበርነ፡ ለሞት፡*ክርስቶስ፡ከሙታን፡ እንደ፡ተነሣ፡በአብ፡ ክብር፡እንደሁ፡እኛም፡ ደግሞ፡ ባዲስ፡ ሕይወት፡ እንሔድ፡ ዘንድ።
*፩፥ ጴጥ፡ ፫፥ ፳፩፡፡ ቆለ፡ ፫፥ ፳፡፡

፭፥ ከርሱም፡ጋራ፡*የተተከልነ፡ከሆነ፡በሞቱ፡ ምሳሌ፡እንደሁም፡ ደግሞ፡ እንሆናለን፡ በትንሣኤው።
*ፊል፡ ፫፥ ፲፥ ፲፩፡፡ ፪፥ ጢሞ፡ ፪፥ ፲፩፡፡

፮፥ እናውቃለንም፡ ያረጀው፡ ሰውነታችን፡ ከርሱ፡ ጋራ፡ እንደ፡*ተሰቀለ፡ የኃጢአት፡ሥጋ፡ ይሻር፡ ዘንድ፡ ለኃጢአት፡ ባሮች፡ እንዳንሆን።
*ገላት፡ ፭፥ ፳፬፡፡
ቆለ፡ ፪፥ ፲፩፥

፯፥ የሞተ፡ ከኃጢአት፡ አርነት፡ ወጥትዋልና።
ገላት፡ ፪፥ ፲፱፡፡

፰፥ ከክርስቶስ፡ጋራም፡ ከሞትነ፡እንመን፡ ከርሱ፡ ጋራ፡ በሕይወት፡ እንድንኖር።

፱፥ አውቀናልና፡ክርስቶስ፡ከሙታን፡እንደ፡ተነሣ፡ ደግሞም፡ *አይሞትም። ሞትም፡ ደግሞ፡ አይገዛውም።
ራእ፡ ፩፥ ፲፰፡፡

፲፥ በሞቱ፡ ለኃጢአት፡ *እንደ፡ግዜ፡ ሙትዋልና፡ በሕይወቱ፡ ግን፡ ለእግዚአብሔር፡ †ሕያው፡ ነው።
*ዕብ፡ ፱፥ ፳፮፥—፳፰፡፡ †ኢሳ፡ ፶፫፥ ፲፡፡

፲፩፥ እንደሁም፡እላንተ፡ደግሞ፡ ራሳችሁን፡ ቍጠሩ፡ከኃጢአት፡እንደ፡ሞታችሁ፡በሕይወትም፡ እንድትኖሩ፡ ለእግዚአብሔር፡ በክርስቶስ፡ የሱስ፡ በጌታችን።
፪፥ ቆሮ፡ ፭፥ ፲፭፡፡ ፩፥ ጴጥ፡ ፪፥ ፳፬፡፡

፲፪፥ ስለዚህም፡ የሚሞተውን፡ ሥጋችሁን፡ *ለኃጢአት፡ አታስገዙ፡ ፈቃዱንም፡ በጁ፡ አትበሉ።
*ዘፍ፡ ፬፥ ፯፡፡ መዝ፡ ፻፲፱፥ ፻፴፫፡፡

፲፫፥ ሕዋሳታችሁንም፡ አታዘጋጁ፡ ለኃጢአት፡ እቃ፡ነገር፡ ግን፡ ራሳችሁን፡ ለእግዚአብሔር፡ አዘጋጁ፡ ከሞት፡ እንደ፡ ዳኑ፡ ሰዎች። ሕዋሳታችሁንም፡ እንደ፡ ጽድቅ፡ እቃ፡ ለእግዚአብሔር።
ም፡ ፲፪፥ ፩፡፡
ኤፌ፡ ፪፥ ፩፥—፲፡፡

፲፬፥ ኃጢአት፡ *አይገዛችሁምና፡ ከኦሪት፡ በታች፡ ስላልሆናችሁ፡ከጸጋ፡በታች፡እንጂ። *፩፥ ዮሐ፡ ፫፥ ፯፡፡
ሮሜ፡ ፭፥ ፳፡፡

፲፭፥ እንኪያህ፡ ምን፡ ይሁን። ኃጢአት፡ እንስራን፡ ከኦሪት፡በታች፡ ስላልሆነ፡ *ከጸጋ፡ በታች፡ እንጂ። አይደለም።
*ም፡ ፭፥ ፲፮፥ ፳፩፡፡ ዮሐ፡ ፩፥ ፲፮፡፡

፲፮፥ ወይስ፡አታውቁምን፡*ሰውነታችሁን፡ ለምታዘጋጁለት፡ለርሱ፡ባሮች፡ እንድትሆኑ፡ ልትሰሙት፡ እላንት፡ለርሱ፡ ባሮች፡ እንደ፡ ሆናችሁ፡ ለምትታዘዙለት። ለኃጢአትም፡ቢሆን፡ለሞት፡ለመታዘዝም፡ ቢሆን፡ለጽድቅ።
*ዮሐ፡ ፰፥ ፴፬፥—፵፭፡፡

፲፯፥ ለእግዚአብሔር፡ ግን፡ ምስጋና፡ ይሁነው፡ ለኃጢአት፡ ባሮች፡ ነበራችሁና፡ ከለልባችሁ፡ ግን፡ ታዛዦች፡ ሆናችሁ፡ ለተሰጣችሁ፡ ለትምህርት፡ ምሳሌ።

፲፰፥ ከኃጢአትም፡ *አርነት፡ወጥታችሁ፡ ለጽድቅ፡ ተገዛችሁ።
*ዮሐ፡ ፰፥ ፴፪፡፡

፲፱፥ እንደ፡ሰው፡ እላለሁ፡ስለ፡ ሥጋችሁ፡ ድካም። ሕዋሳታችሁን፡ እንደዘጋጃችሁ፡ ለርኵስነት፡ መገዛት፡ለኃጢአትም፡እንደሁም፡አሁን፡ ሕዋሳታችሁን፡ አዘጋጁ፡ *ለጽድቅ፡ ለቅድስናም።
*ም፡ ፲፪፥ ፩፡፡

፳፥ *ለኃጢአት፡ባሮች፡ ሳላችሁ፡ ከጽድቅ፡ አርነት፡ ወጥታችሁ፡ ነበራችሁና።
*ዮሐ፡ ፰፥ ፴፬፡፡

፳፩፥ ነገር፡ግን፡ምን፡ፍሬ፡ ነበራችሁ፡ የዚያን፡ጊዜ፡ በስራችሁ፡ዛሬ፡ ከርሱ፡ *የምታፍሩበት። የዚያ፡ስራ፡ †ፍጻሜ፡ ሞት፡ነውና።
*ሕዝ፡ ፲፮፥ ፷፩፥ ፷፫፡፡
†ም፡ ፰፥ ፮፡፡

፳፪፥ ዛሬ፡ግን፡ከኃጢአት፡አርነት፡ወጥታችሁ፡ለእግዚአብሔር፡ተገዝታችኋልና፡ ፍሬያችሁ፡ለቅድስና፡ አላችሁ፡ *ፍጻሜውም፡ የዘላለም፡ ሕይወት፡ ነው።
*፩፥ ጴጥ፡ ፩፥ ፱፡፡

፳፫፥ የኃጢአት፡ዋጋ፡ *ሞት፡ነውና፡የእግዚአብሔር፡ጸጋ፡ግን፡ የዘላለም፡ ሕይወት፡ ነው፡ በየሱስ፡ ክርስቶስ፡በጌታችን።
*ም፡ ፭፥ ፲፪፡፡ ያዕ፡ ፩፥ ፲፭፡፡
፩፥ ቆሮ፡ ፲፭፥ ፳፪፡፡ ፩፥ ዮሐ፡ ፭፥ ፲፩፡፡

## ምዕራፍ፡ ፯፥

፩፥ አታውቁምን፡ ወንድሞቼ፡ ሆይ፡ እኔ፡ ኦሪትን፡ ለሚያውቁ፡ እናገራለሁና። ኦሪት፡ሰውን፡እንድትገዛ፡ባለበቱ፡ ዘመን፡ሁሉ።
ም፡ ፮፥ ፲፬፡፡

፪፥ ሴት፡በሕግ፡ለባልዋ፡ታሥራ፡ትኖራለችና፡ ባለበ

ቱ፡ዘመን። ባልዋ፡ግን፡ከሞተ፡ በኋላ፡ አርነት፡ ትወጣለች፡ ከባልዋ፡ ሕግ። ዘዳግ፡ ፳፬፤ ፬።

፫፤ ባልዋም፡ በሕይወቱ፡ ሳለ፡ *ብታገባ፡ አመንዝራ፡ ትባላለች፡ ለሌላ፡ ወንድ፡ ብትሆን። ባልዋ፡ ግን፡ከሞተ፡በኋላ፡ከሕግ፡አርነት፡ወጣች፡ አመንዝራም፡አትባልም፡ ለሌላ፡ ወንድ፡ብትሆን። *ማቴ፡ ፭፤ ፴፪።

፬፤ አሁንም፡ወንድሞቼ፡ ሆይ፡ እላንተ፡ ደግሞ፡ፈጽማችሁ፡ከሕግ፡ ሞታችሁ፡ በክርስቶስ፡ ሥጋ፡ለሌላ፡ ትሆኑ፡ዘንድ፡ ከሙታን፡ ለተነሣው። ለእግዚአብሔር፡ፍሬ፡እናፈራ፡ ዘንድ። ኤፌ፡ ፯፤ ፴፩፤ ፴፪። ም፡ ፯፤ ፷፪።

፭፤ በሥጋም፡ በሆንነ፡ ጊዜ፡ የኃጢአት፡ ሕማማት፡ ከሕግ፡ያለች፡ በሕዋሳታችን፡ ትታወክ፡ ነበረችና፡ *ለሞት፡ ፍሬ፡ ስለ፡ ማፍራት። *ቆ፡ ፯፤—፳፫። ም፡ ፯፤ ፳፩።

፮፤ ዛሬ፡ግን፡ከሕግ፡አርነት፡ ወጣን፡ይዞን፡ ከነበረውም፡ሞትን፡ በመንፈስ፡አዲስነት፡ እንገዛ፡ ዘንድ፡ በፊደልም፡ አረጅነት፡ አይደለም። ም፡ ፰፤ ፩፤—፲፪። ፯፤ ፪፤ ፬።

፯፤ ምን፡ እንላለን፡ እንግዲህ። ኦሪት፡ ኃጢአትን፡ ናት። አይደለም። ነገር፡ግን፡ ኃጢአትን፡ አላወቅሁም፡ *በኦሪት፡ እስካውቃት፡ ድረስ። ምኞትንም፡ ባላወቅሁም፡ ነበርሁ፡ ኦሪት፡ አትመኝ፡ ባላለች። *ዘፀአ፡ ፳፤ ፲፯።

፰፤ ኃጢአትም፡በትእዛዝ፡ ምክንያት፡በወሰደች፡ ጊዜ፡ምኞትን፡ሁሉ፡አደረገችብኝ። *ኦሪት፡ሳትመጣ፡ ኃጢአት፡ ሙታ፡ነበረችና። ቆ፡ ፲፩። ም፡ ፭፤ ፲፫። *ዮሐ፡ ፲፭፤ ፳፪።

፱፤ እኔም፡ ሕያው፡ ነበርሁ፡ ያለ፡ ኦሪት፡ አስቀድሚ። ትእዛዝ፡ግን፡በመጣች፡ጊዜ፡ኃጢአት፡ደነች፡እኔም፡ ሞትሁ።

፲፤ ትእዛዚቱንም፡ *ለሕይወት፡ የነበረችውን፡ ለሞት፡ሆና፡አገኘኋት። ያዕ፡ ፩፤ ፲፭። *ዘሌዋ፡ ፲፰፤ ፭።

፲፩፤ ኃጢአትም፡ በትእዛዝ፡ ምክንያት፡ በወሰደች፡ ጊዜ፡ አታለለችኝ፡ በርሱዋም፡ ገደለችኝ። ዕብ፡ ፫፤ ፲፫።

፲፪፤ እንግዲህ፡ ኦሪት፡ ቅድስት፡ ናት፡ ትእዛዚቱም፡ ቅድስት፡ ናት፡ የቀናችም፡ ያማረችም፡ ናት። ፩፤ ጢሞ፡ ፩፤ ፰።

፲፫፤ መልካሙ፡ ግን፡ ሞትን፡ ይሁንብኝ። አይደለም። ነገር፡ግን፡ኃጢአት፡ኃጢአት፡ሁና፡ትገለጥ፡ዘንድ፡ ሞት፡ፈጽማ፡ አመጣችብኝ፡ በመልካሙ፡ ኃጢአት፡ እጅግ፡ኃጢአተኛ፡ትሆን፡ዘንድ፡ከትእዛዝ፡ የተነሣ። ም፡ ፭፤ ፳።

፲፬፤ ኦሪት፡መንፈሳዊት፡ እንደ፡ ሆነች፡ አውቀናልና። እኔ፡ ግን፡ *ሥጋዊ፡ ነኝ፡ ከኃጢአት፡ ተበታች፡ የተሸጥሁ። *ቆ፡ ፲፰። ማቴ፡ ፭፤ ፳፰፤ ፳፰። ዮሐ፡ ፫፤ ፮። †፩፤ ነገሥ፡ ፳፩፤ ፳፤ ፳፭።

፲፭፤ የማደርገውን፡አላውቀውምና። የምወደውን፡አላደርገውምና። የምጸላውን፡ እርሱን፡ አደርጋለሁ፡እንጂ።

፲፮፤ የማልወደውንም፡ እርሱን፡ የማደርግ፡ ከሆንሁ፡እላለሁ፡ኦሪት፡መልካም፡እንደ፡ሆነች። ቆ፡ ፲፪።

፲፯፤ አሁንም፡ እኔ፡ ያነን፡ የማደርገው፡ አይደለሁም፡ በኔ፡ ያደረቸው፡ ኃጢአት፡ እንጂ።

፲፰፤ እኔ፡ አውቃለሁና፡ መልካም፡ ነገር፡ እንደ፡ *ሌለብኝ፡በሥጋዬ። ፈቃድስ፡አለብኝ፡ መልካም፡ለማድረግ፡ ነገር፡ ግን፡ መልካም፡ ማድረግን፡ አላገኘውም። *ዘፍ.ጥ፡ ፮፤ ፭። ም፡ ፰፤ ፳፩።

፲፱፤ በጎ፡ አላደርግምና፡ የምወደውን፡ ክፉውን፡የማልወደው፡ እርሱን፡ አደርጋለሁ፡ እንጂ።

፳፤ እኔም፡የማልወደውን፡የማደርገው፡ከሆንሁ፡ ደግሞ፡እኔ፡የማደርገው፡አይደለሁም፡በኔ፡ የምታድረው፡ ኃጢአት፡ ናት፡ እንጂ።

፳፩፤ እንግዲህ፡ እኔ፡ ሕግን፡ አገኛለሁ፡ መልካም፡ አደርግ፡ ዘንድ፡ በወደድሁ፡ ጊዜ፡ *ክፉ፡ እንደለብኝ። *ዘፍ.ጥ፡ ፬፤ ፯። መዝ፡ ፶፩፤ ፯።

፳፪፤ እኔ፡በእግዚአብሔር፡ ሕግ፡ *ደስ፡ ይለኛልና፡ በውሥጡ፡ሰውነቴ። ም፡ ፪፤ ፲፬፤ ፲፭። *መዝ፡ ፩፤ ፪።

፳፫፤ በሕዋሳቴ፡ግን፡ያለው፡ሌላ፡ ሕግ፡ የልቤን፡ሕግ፡ሲጻላ፡አያለሁ፡በሕዋሳቴ፡ወደለውም፡ወደ፡ኃጢአት፡ ሕግ፡ ይማርከኛል። *ገላት፡ ፭፤ ፲፯።

፳፬፤ እኔ፡ ጎስቋላ፡ ሰው። ማነው፡ የሚያድነኝ፡ ከዚህ፡ከሞት፡ ሥጋ። ም፡ ፰፤ ፲፤ ፳፫።

፳፭፤ እግዚአብሔርን፡*አመሰግናለሁ፡በጌታችን፡ በየሱስ፡ክርስቶስ። እንግዲህ፡ እኔ፡ በልቤ፡ ለእግዚአብሔር፡ሕግ፡ እገዛለሁ፡ በሥጋዬ፡ ግን፡ ለኃጢአት፡ ሕግ። *፩፤ ቆር፡ ፲፭፤ ፶፯።

## ምዕራፍ፡ ፰፤

፩፤ ዛሬ፡ግን፡ኩነኔ፡የላቸውም፡ በክርስቶስ፡ የሱስ፡ ላሉ፡ሁሉ፡በሥጋ፡ የማንመላለስ፡ በመንፈስ፡ እንጂ። ቆ፡ ፴፩፤—፴፱። ገላት፡ ፭፤ ፲፮፤ ፳፭።

፪፤ የሕይወት፡መንፈስ፡ *ሕግ፡ በየሱስ፡ ክርስቶስ፡ ነውና፡ አርነትም፡ አወጣችኝ፡ ከኃጢአትና፡ ከሞት፡ ሕግ። *ም፡ ፫፤ ፳፯።

፫፤ ለሕግም፡ኃይል፡አልነበራትምና፡ስለ፡ሥጋ፡ *ድካም፡እግዚአብሔር፡ ልጁን፡ሰደደ፡ በኃጢአት፡ሥጋ፡ ምሳሌ፡ ስለ፡ ኃጢአትም፡ ኃጢአትን፡ ኰነነ፡ በሥጋው። *የሐዋ፡ ፲፫፤ ፴፰። ዕብ፡ ፪፤ ፲፯።

፬፤ የሕግ፡ ጽድቅ፡ በኛ፡ ይፈጸም፡ ዘንድ፡ በሥጋ፡ የማንመላለስ፡ በመንፈስ፡ እንጂ።

፭፤ እርሳቸው፡በሥጋ፡የሚሔዱ፡ የሥጋን፡ ነገር፡ ያስባሉና። በመንፈስ፡ግን፡ የሚሔዱ፡ የመንፈስን፡ ነገር፡ ያስባሉ።

፮፤ የሥጋ፡አሳብ፡ *ሞት፡ነውና። የመንፈስ፡አሳብ፡ ግን፡ ሕይወትና፡ ሰላም፡ ነው። *ም፡ ፮፤ ፳፩።

፯፤ የሥጋ፡ አሳብ፡ የእግዚአብሔር፡ ጸላት፡ ነውና፡

ለእግዚአብሔርም፡ ሕግ፡ አይገዛም። ያነን፡ አይችል
ምና። *ያዕ፡ ፬፡ ፬።
፰፡ በሥጋም፡ያሉ፡እግዚአብሔርን፡ደስ፡ ያሰኙት፡
ዘንድ፡አይችሉም።
፱፡ እላንት፡ ግን፡ በሥጋ፡ አይደላችሁም፡ በመንፈ
ስ፡እንጂ፡ የእግዚአብሔር፡*መንፈስ፡ ካደረባችሁ።
የክርስቶስ፡መንፈስ፡ግን፡የሌለበት፡ ያ፡እርሱ፡ ለርሱ፡
አይደለም። *፩፡ ቆሮ፡ ፫፡ ፲፮።
፲፡ ክርስቶስ፡ግን፡ካደረባችሁ፡ሥጋ፡ የሞተ፡ ነው፡ስ
ለ፡ኀጢአት፡መንፈስም፡ ሕያው፡ ነው፡ ስለ፡ ጽድቅ።
፲፩፡ የሱስ፡ክርስቶስንም፡ ከሙታን፡ ያስነሣ፡ መን
ፈስ፡በላንት፡ ካደረባችሁ፡ እርሱ፡ የሱስ፡ ክርስቶስን፡
ከሙታን፡ ያስነሣ፡ የሚሞተውን፡ ሥጋችሁን፡ ደግ
ሞ፡ ሕያው፡ ያደርገዋል፡ ስለሚያድርባችሁ፡ መን
ፈሱ።
፲፪፡ አሁንም፡ ወንድሞቼ፡ ሆይ፡በሥጋ፡ እንሔድ፡
ዘንድ፡ *አይገባነም፡ በሥጋ፡ እንኖር፡ ዘንድ።
*ም፡ ፮፡ ፯፡ ፲፰።
፲፫፡ እላንት፡በሥጋ፡*ብትኖሩ፡የግድ፡ትሞታላችሁ
ና። †በመንፈስ፡ ግን፡ የሥጋን፡ ስራ፡ብትገድሉ፡ በሕይ
ወት፡ትኖራላችሁ። *ገላት፡ ፮፡ ፰። †ኤፌ፡ ፬፡ ፳፪።
፲፬፡ በእግዚአብሔር፡መንፈስ፡ ተመርተው፡ የሚ
ሆኑ፡ሰዎች፡ እርሳቸው፡ የእግዚአብሔር፡ልጆች፡ ናቸ
ውና።
፲፭፡ የባርነትን፡*መንፈስ፡ አልወሰዳችሁምና፡ደግ
ሞ፡ለፍርሃት፡ †የልጅነትን፡ መንፈስ፡ወሰዳችሁ፡ እን
ጂ፡የምትጸራበት፡ አባ፡ አባታችን፡ ሆይ።
*፪፡ ጢሞ፡ ፩፡ ፯። †ገላት፡ ፬፡ ፭፡ ፮።
፲፮፡ ያም፡*መንፈስ፡ለመንፈሳችን፡ ይመሰክራል፡
እኛ፡ የእግዚአብሔር፡ልጆች፡እንደ፡ሆነ።
*፪፡ ቆሮ፡ ፩፡ ፳፪።
፲፯፡ *ልጆችም፡ ከሆነ፡ እኛ፡ወራሾች፡ ነን፡ የእግዚአ
ብሔር፡ወራሾችና፡ የክርስቶስ፡ ባልንጀሮች፡ ወራሾች፡
ነን፡ ከርሱ፡ ጋራ፡ †መከራ፡ብንቀበል፡ ከርሱ፡ ጋራ፡ ደግ
ሞ፡ እንከብር፡ ዘንድ። *ገላት፡ ፬፡ ፯።
†ራእ፡ ፳፩፡ ፯። የሐዋ፡ ፲፬፡ ፳፪።
፲፰፡ እኔ፡ አምናለሁና፡ *የዚህ፡ ዘመን፡ መከራ፡ የ
ሚመጣውን፡ ክብር፡ እንደይተካከለው፡ በኛ፡ ይገለ
ጥ፡ ዘንድ፡ ያለውን። *፪፡ ቆሮ፡ ፬፡ ፲፯።
፲፱፡ የፍጥረቱ፡ የሚያሳር፡ አለኝታ፡ የእግዚአብሔ
ርን፡ልጆች፡*መግለጥ፡ተስፋ፡ያደርጋልና። *ቆል፡ ፫፡ ፬።
፳፡ ፍጥረት፡ ለከንቱ፡ ተገዝትዋልና፡ በፈቃዱ፡ አ
ይደለም፡ ነገር፡ ግን፡ ስላስገዛው፡ በተስፋ።
ዘፍ፡ ፫፡ ፲፯። ም፡ ፭፡ ፲፱።
፳፩፡ ፍጥረት፡ ሁሉ፡ ደግሞ፡ አርነት፡ ይወጣልና፡ ከ
ጥፋት፡ ባርነት፡ በእግዚአብሔር፡ ልጆች፡ ክብር፡ አር
ነት። ፪፡ ጴጥ፡ ፫፡ ፲፫።
፳፪፡ እናውቃለንና፡ ፍጥረት፡ሁሉ፡ ከኛ፡ጋራ፡ውዝ
ዋዜ፡እንደለው፡ባንድም፡እንደ ጣጣር፡እስከ፡ዛሬ።

፳፫፡ እርሱም፡ብቻ፡ አይደለም፡ እኛም፡ እንጂ፡የ
መንፈስ፡ቅዱስ፡መጀመርያ፡ ያለነ፡ እኛም፡ እንጣጣ
ራለን፡ በራሳችን፡ ልጅነትንም፡ ተስፋ፡ እናደርጋለን፡
የሥጋችነን፡ መዳን። ፪፡ ቆሮ፡ ፭፡ ፪።
፳፬፡ በተስፋ፡ ድነናልና። የሚታየው፡ ተስፋ፡ ግን፡
ተስፋ፡ አይደለም። ማንም፡ የሚያየው፡ ከሆነ፡ እን
ዴት፡ይጠብቀዋል። ፪፡ ቆሮ፡ ፭፡ ፯።
፳፭፡ የማናየውን፡ ግን፡ተስፋ፡ ብናደርገው፡ በትዕ
ግሥት፡ እንጠብቀዋለን።
፳፮፡ እንዲሁም፡ ደግሞ፡ መንፈስ፡ ቅዱስ፡ ለድካ
ማችን፡ኃይል፡ ይሰጣል። እንዴት፡ እንድንጸልይ፡ እን
ደሚገባነ፡አናውቅምና። ነገር፡ግን፡እርሱ፡መንፈስ፡ቅ
ዱስ፡ይጸልይልናል፡በማይነገር፡ ቍዘማ።
፳፯፡ ልብንም፡ መርምሮ፡ የሚያውቅ፡ የመንፈስ
ን፡ፈቃድ፡ ያውቃል፡እርሱ፡ እንደ፡ እግዚአብሔር፡ ፈ
ቃድ፡ ስለ፡ ቅዱሳን፡ ይለምናልና።
፳፰፡ ፈጽመንም፡ እናውቃለን፡ እግዚአብሔርን፡
የሚወዱን፡ ሰዎች፡ ነገር፡ ሁሉ፡ ያግዛቸዋል፡ መልካ
ም፡እንዲሆንላቸው፡ *ለተጸራቸው፡ በፈቃዱ።
*ኤፌ፡ ፩፡ ፲፩። ፫፡ ፲፩።
፳፱፡ አስቀድሞም፡ ያወቃቸውን፡ እርሳቸውን፡
መረጠ፡በልጁ፡መልክ፡ ምሳሌ፡ ይመስሉ፡ ዘንድ፡ እር
ሱ፡ በብዙ፡ ወንድሞች፡ *በኵር፡ ይሆን፡ ዘንድ።
*ቆላ፡ ፩፡ ፲፰። ዕብ፡ ፩፡ ፮።
፴፡ እርሳቸውንም፡ አስቀድሞ፡ የመረጣቸውን፡
ጸራ፡ደግሞ።የጸራቸውንም፡ እርሳቸውን፡ አጸደቀ።
ያጸደቃቸውንም፡ እርሳቸውን፡ አከበረ።
፴፩፡ ምን፡ እንላለን፡ እንግዴህ። *እግዚአብሔር፡
†ከኛ፡ጋራ፡ከሆነ፡ የሚቃወመነ፡ ማነው።
መዝ፡ ፻፲፰፡ ፮። †ዘኍል፡ ፲፬፡ ፱።
፴፪፡ ለልጁ፡ የማይራራ፡ ስለ፡ *ሁላችን፡ አሳልፎ፡
ሰጠው፡ እንጂ። እንዴትስ፡ሁሉን፡ አይሰጠነ፡ ከርሱ፡
ጋራ። *ዮሐ፡ ፫፡ ፲፮።
፴፫፡ በእግዚአብሔር፡ ምርጦችስ፡ ላይ፡ *ማነው፡
ነገር፡የሚሰራ። እግዚአብሔር፡ ነውን፡ የሚያጸድቅ።
*ኢሳ፡ ፶፡ ፰፡ ፱። ና፡ ፶፬፡ ፲፯።
፴፬፡ ማነው፡ የሚኰንን። ክርስቶስ፡ የሱስ፡ የሞ
ተ፡ነውን። ከሙታንም፡ እንኳ፡ የተነሣ፡ በእግዚአብ
ሔርም፡ ቀኝ፡ የተቀመጠ፡ እርሱም፡ ያስምረናል።
ቍ፡ ፩። ፩፡ ዮሐ፡ ፪፡ ፩።
፴፭፡ ማነውስ፡ ከክርስቶስ፡ ፍቅር፡ *የሚለየነ። ኀ
ዘንን። ጭንቀትን። ሰደትን። ራብን። ራቁትነትን፡ ፍር
ሃትን። ሰይፍን። *ዮሐ፡ ፲፡ ፳፰።
፴፮፡ እንደ፡*ተጻፈ። ስላንተ፡ እንሞታለን፡ዕለት፡
ዕለት። እንደሚታረዱ፡ በጎች፡ ተቈጠርነ።
*መዝ፡ ፵፬፡ ፳፪። ፪፡ ቆሮ፡ ፬፡ ፲፩።
፴፯፡ ነገር፡ግን፡ከዚህ፡ሁሉ፡ጋራ፡ እጅግ፡*እናሸንፋ
ለን፡በርሱ፡ በወደደነው። *፩፡ቆሮ፡ ፲፭፡ ፶፯።
፴፰፡ እኔ፡ በልቤ፡አምናለሁና፡ ሞትም፡ቢሆን፡ ሕ

ይወትም፡ መላእክትም፡ አለቆችም፡ ኃይላትም፡ የ
ሆነውም። የሚሆነውም። ፪፡ ጢሞ፡ ፩፡ ፲፪።

፴፱፡ ከፍታም፡ ዝቅታም፡ሌላም፡ ፍጥረት፡ ሁሉ፡
ሊለየኝ፡አይችልም፡ከእግዚአብሔር፡ ፍቅር፡ በክርስ
ቶስ፡ የሱስ፡ በጌታችን። ፪፡ ቆሮ፡ ፲፡ ፭።

ምዕራፍ፡ ፱፡

፩፡ እውነት፡ እላለሁ፡ በክርስቶስ፡ አስትም፡ አልና
ግርም። ሕሊናዬም፡ *ይመሰክርልኛል፡ በመንፈስ፡ ቅ
ዱስ። *ም፡ ፩፡ ፱።

፪፡ የልብ፡አዘን፡እጅግ፡እንደሌብኝ፡ልቅሶም፡ ከል
ቤም፡ አይቋረጥም። ም፡ ፲፡ ፩።

፫፡ *እኻም፡ነበርሁ፡እኔ፡ራሴ፡ከክርስቶስ፡ እለይ፡ዘ
ንድ፡ ስለ፡ ወንድሞቼ፡ ስለ፡ ዘመዶቼም፡ ብሥጋ።
*ዘፀአ፡ ፴፪፡ ፴፪።

፬፡ እርሳቸውም፡ የእሥራኤል፡ ወገን፡ *ልጅነት
ም፡ለርሳቸው፡ ነው፡ ክብርም፡ ኪዳንም፡ ኦሪትም፡ የ
እግዚአብሔርም፡ ማገልገል፡ ተስፋውም።
*ዘፀአ፡ ፬፡ ፳፪። ዘዳግ፡ ፯፡ ፮።

፭፡ አባቶችም፡ከርሳቸው። ከርሳቸውም፡ ክርስቶ
ስ፡ *መጣ፡ በሥጋ። እርሱ፡ ከሁሉ፡ የሚበልጥ፡ አምላ
ክ። ለርሱ፡ በረከት፡ የሚገባው፡ ለዘላለም። አሜን።
*ማቴ፡፩፡፩—፲፫። ሉቃ፡፫፡፳፫—፴፰። ዮሐ፡፩፡፩።

፮፡ የእግዚአብሔር፡ *ነገር፡ ግን፡ አልወደቀም፡ ከ
ቶ።ከእሥራኤል፡†ወገን፡ የሆኑ፡ ሁሉ፡ እሥራኤል፡አ
ይደሉምና። *ዘኍል፡ ፳፫፡ ፲፱። †ሮሜ፡ ፪፡ ፳፰።
ዮሐ፡ ፰፡ ፴፱።

፯፡ ከአብርሃምም፡ዘር፡ የሆኑ፡ሁሉ፡ እርሳቸው፡ል
ጆች፡አይደሉም፡ነገር፡ግን፡ ተባለ፡ *በይስሐቅ፡ ዘር፡ይ
ጸራልሃል። *ዘፍ፡ ፳፩፡ ፲፪። ዕብ፡ ፲፩፡ ፲፰።

፰፡ እርሳቸው፡ የሥጋ፡ ልጆች፡ የእግዚአብሔር፡ ል
ጆች፡አይደሉምና፡ ነገር፡ግን፡ የተስፋ፡ልጆች፡ ዘር፡ ሁነ
ው፡ ይቈጠራሉ። ገላት፡ ፬፡ ፳፫።

፱፡ የተስፋውም፡ ቃል፡ ይህ፡ ነው። *እንደዚህ፡ጊ
ዜ፡ እመጣለሁ፡ ሳራም፡ ልጅ፡ ትወልዳለች።
*ዘፍ፡ ፲፰፡ ፲።

፲፡ ለርስዋም፡ ብቻ፡ አይደለም፡ *ለርብቃም፡ ደግ
ሞ፡ ካንዱ፡ ከይስሐቅ፡ ካባታችን፡ ባረገዘች፡ ጊዜ።
*ዘፍ፡ ፳፭፡ ፳፩።

፲፩፡ ሳትወልድ፡ ልጆችም፡ በጎም፡ ክፉም፡ ሳያደር
ጉ። የእግዚአብሔር፡ ፈቃድ፡ በመምረጥ፡ ትጸና፡ ዘ
ንድ።

፲፪፡ በምግባር፡አይደለም፡ነገር፡ግን፡ ከጸሪው፡ተገ
ለላት፡*ታላቁ፡ለታናሹ፡ይገዛል። *ዘፍ፡ ፳፭፡ ፳፫።

፲፫፡ እንደ፡ተጻፈ። *ያዕቆብን፡ ወደድሁ፡ ዔሳውን
ም፡ጸላሁ። *መል፡ ፩፡ ፪፡ ፫።

፲፬፡ እንግዴህ፡ምን፡ እንላለን። ወይስ፡ እግዚአብ
ሔር፡ ግፍን፡ ያደርጋል። አይደለም።

፲፭፡ ለሙሴ፡ብሎታልና፡*የምምረውን፡እምራለ
ሁ፡ለምራራለትም፡እራራለሁ። *ዘፀአ፡ ፴፫፡ ፲፱።

፲፮፡ አሁንም፡ ይህ፡ ለወደደ፡ ለሮጠም፡ አይደለ
ም። እግዚአብሔር፡ ይቅር፡ ላለው፡ ነው፡ እንጂ።
ኤፌ፡ ፪፡ ፰።

፲፯፡ መጽሐፍ፡ፈርዖንን፡*ይላልና። ስለዚህ፡ አስነ
ሣሁህ፡ኃይሌን፡እገልጥብህ፡ ዘንድ፡ ስሜም፡ ይጸራ፡
ዘንድ፡ በምድር፡ ሁሉ። *ዘፀአ፡ ፱፡ ፲፮።

፲፰፡ እንግዴህ፡ተገለጠ፡የወደደውን፡ይምራል፡ያ
ልወደደውንም፡ ልቡን፡ ያጸናል።

፲፱፡ አንተ፡ግን፡ትለኛለህ፡ እንኪያ፡ ለምን፡ ይነቅ
ፋል። ማነው፡ ፈቃዱን፡ የሚቀወም።

፳፡ ነገር፡ግን፡አንተ፡ ሰው፡ አንተ፡ማነህ፡ ለእግዚአ
ብሔር፡ የምትመልስ። ወይስ፡ስራ፡*ሰሪዋን፡ትለዋለ
ችን። ለምን፡እንደዚህ፡ ሰራህኝ። *ኢሳ፡ ፵፭፡ ፱።

፳፩፡ ወይስ፡ጭቃ፡ ሰሪ፡ሥልጣን፡ የለውምን፡ በጭ
ቃ፡ላይ፡እቃ፡ይሰራ፡ ዘንድ፡ አንዱን፡ለክብር፡ አንዱን
ም፡ ላለመክበር።

፳፪፡ እግዚአብሔርም፡ በወደደ፡ጊዜ፡ ቍጣውን፡
ይገልጥ፡ዘንድ፡ኃይሉንም፡ያሳይ፡ዘንድ፡በብዙ፡ *ትዕ
ግሥቱ፡የቍጣ፡እቃ፡ታገሠ፡ †ለማጥፋት፡ የተዘጋጀ።
*ም፡ ፪፡ ፬። †፪፡ ጴጥ፡ ፪፡ ፱።

፳፫፡ የክብሩንም፡ ባለጸግነት፡ *ያሳይ፡ዘንድ፡ በም
ሕረት፡እቃ፡አስቀድሞ፡ ለክብር፡ባዘጋጀው።
*ኤፌ፡ ፩፡ ፫—፲፪። ም፡ ፰፡ ፳፱።

፳፬፡ እኛን፡ የጸራነንም፡ከአይሁድ፡ብቻ፡ አይደለ
ም። ከአሕዛብም፡ ደግሞ፡ እንጂ።

፳፭፡ ደግሞ፡*በሆሴዕ፡በነቢዩ፡እንዲል። ወገኔ፡ያይ
ደለውን፡ ወገኔ፡ ብዬ፡ እጸራዋለሁ፡ ያልተወደደችው
ንም፡ የተወደደች። *ሆሴ፡ ፪፡ ፳፫። ፩፡ ጴጥ፡ ፪፡ ፲።

፳፮፡ አላንተ፡ ወገኖቼ፡ አይደላችሁም፡ *በተባሉ
በትም፡ስፍራ፡ከዚያ፡ይባላሉ፡የሕያው፡ የእግዚአብ
ሔር፡ ልጆች። *ሆሴ፡ ፩፡ ፲። ኢሳ፡ ፳፭፡ ፩።

፳፯፡ ኢሳይያስም፡ይጮሃል፡ ስለ፡እሥራኤል፡እን
ደዚህ፡ሲል። *የእሥራኤል፡ልጆች፡ቍጥራቸው፡እንደ፡
ባሕር፡ አሸዋ፡ቢሆን፡ ከርሳቸው፡ †ቅሬታ፡ ይድናል።
*ኢሳ፡ ፲፡ ፳፪፡ ፳፫። †ሮሜ፡ ፲፩፡ ፭።

፳፰፡ ነገሩን፡ ይፈጽማል፡ በጽድቅም፡ ይቈርጣል
ና። እግዚአብሔር፡ የተቈረጠ፡ ነገር፡ በምድር፡ላይ፡ ያ
ደርጋልና።

፳፱፡ *ኢሳይያስም፡አስቀድሞ፡እንደለ። እግዚአ
ብሔር፡ፀባዖትስ፡ ዘር፡ባላስቀረልን። እንደ፡ †ሶዶም፡
በሆንነ፡ነበርነ፡ገሞራንም፡ በመሰልነ። *ኢሳ፡ ፩፡ ፱።
†ዘፍ፡ ፲፱፡ ፳፬።

፴፡ እንግዴህ፡ምን፡እላለሁ። *ጽድቅን፡የማይሹ፡
አሕዛብ፡ጽድቅን፡አገኙ። በሃይማኖት፡የሚሆነውን፡
ጽድቅ። *ም፡ ፲፡ ፳።

፴፩፡ እሥራኤል፡ግን፡ *የጽድቅን፡ ሕግ፡ ሲከተሉ፡
ጽድቅን፡አላገኙም። *ም፡ ፲፡ ፪።

፴፪፤ ይህስ፡ ለምንድር፡ ነው። በሃይማኖት፡ አልፈ ለጉትምና። ሕግን፡ በመስራት፡ እንጂ፡ በንቅፋትም፡ ደንጊያ፡ ተሰናከሉ።

፴፫፤ እንደ፡*ተጻፈ።እነሆ፡በጽዮን፡የንቅፋት፡ደን ጊያ፡ አኖራለሁ፡ የመጠራጠርም፡ አለት።የሚያምን በትም፡ ሁሉ፡ አያፍርም። *ኢሳ፡ ፰፡ ፲፬፡፡
ኢሳ፡ ፳፰፡ ፲፮፡፡ ማቴ፡ ፳፩፡ ፵፪፡—፵፮፡፡

## ምዕራፍ፡ ፲፤

፩፤ ወንድሞቼ፡ ሆይ፡ የልቤ፡ፈቃድ፡ ወደ፡ እግዚአ ብሔርም፡ መለመኔ፡ ለእሥራኤል፡ ነው፡ ይድኑ፡ ዘ ንድ።

፪፤ እኔ፡ እመሰክርላቸዋለሁና፡ ለእግዚአብሔር፡ ቅናት፡እንዳላቸው፡ነገር፡ግን፡ በውቀት፡ አይደለም።

፫፡ የእግዚአብሔርን፡ ጽድቅ፡ *አላወቁምና፡ ለራ ሳቸውም፡የሰሩትን፡ያጸኑ፡ዘንድ፡ሽተዋልና፡ለእግዚ አብሔር፡ጽድቅ፡አልተገዙም። *ም፡ ፱፡ ፴፩፡ ፴፪፡፡

፬፡ የኦሪት፡ፍጻሜዋ፡ *ክርስቶስ፡ነውና፡ እርሱም፡ ጽድቅ፡ ነውና፡ †ለመነበት፡ ሁሉ። *ማቴ፡ ፭፡ ፲፯፡፡
ዕብ፡ ፰፡ ፲፫፡፡ †ዮሐ፡ ፫፡ ፲፰፡፡

፭፤ ሙሴ፡ግን፡ስለ፡ ኦሪት፡ ጽድቅ፡ *ጻፈ፡ እንዲህ፡ ሲል። የሚሰራባት፡ ሰው፡ ይኖርባታል።
*ዘሌዋ፡ ፲፰፡ ፭፡፡ ገላት፡ ፫፡ ፲፪፡፡

፮፤ የሃይመኖት፡ጽድቅ፡ግን፡እንዲህ፡ *ይላል። በል ብህ፡ አትብል፡ ማን፡ ወደ፡ ሰማይ፡ ይወጣል። እርሱ ም፡ ክርስቶስን፡ ያወርደው፡ ዘንድ።
*ዘዳግ፡ ፴፡ ፲፪፡ ፲፫፡፡

፯፤ ወይስ፡ማነው፡ወደ፡ሲኦል፡ የሚወርድ። እርሱ ም፡ክርስቶስን፡ ከሙታን፡ ያወጣው፡ ዘንድ።

፰፤ ነገር፡ግን፡*ያለው፡ ምንድር፡ ነው። ቃል፡ ቅርብ፡ ነው፡ገፍህ፡ በልበህም። እርስዋም፡ የሃይማኖት፡ ተቃ ል፡ የምናስተምርባት። *ዘዳግ፡ ፴፡ ፲፬፡፡
†፩፡ ጢሞ፡ ፬፡ ፮፡፡

፱፤ ገፍህ፡ብትነግር፡የሱስ፡ጌታ፡እንደ፡ሆነ፡በልብህ ም፡ ብታምን፡ እግዚአብሔር፡ ከሙታን፡ እንደስነሣ ው፡ ትድናለህ። ፪፡ ቆር፡ ፬፡ ፭፡፡

፲፤ ሰው፡በልቡ፡ያምናልና፡ይጸድቅ፡ ዘንድ። *በአፋ ም፡ ያስታውቃል፡ ይድን፡ ዘንድ። *መዝ፡ ፻፲፮፡ ፲፡፡

፲፩፤ መጽሐፍ፡ይላልና። *የሚያምንበት፡ ሁሉ፡ አ ያፍርም። *ኢሳ፡ ፳፰፡ ፲፮፡፡ መዝ፡ ፳፭፡ ፫፡፡

፲፪፤ በአይሁዳዊና፡በአረማዊ፡መካከል፡*ልዩ፡የለ ምና።የሁላቸው፡ ጌታ፡አንድ፡ነውና፡ እርሱም፡ ለሚ ጸሩት፡ ሁሉ፡ ባለ፡ ጸጋ፡ ነው። *የሐዋ፡ ፲፡ ፴፬፡፡
ም፡ ፲፭፡ ፱፡፡

፲፫፤ የእግዚአብሔርን፡ስም፡*የሚጸራ፡ሁሉ፡ይድ ናልና። *ኢዮ፡ ፫፡ ፭፡፡

፲፬፤ ነገር፡ግን፡እንዴት፡ይጸሩታል፡የማያምኑበት። ወይስ፡እንዴት፡ያምናሉ፡ያልሰሙት። ወይስ፡ እንዴ ት፡ይሰማሉ፡ አስተማሪ፡ የሌላቸው።

፲፭፤ እንዴትስ፡ያስተምራሉ፡ሳይላኩ። *እንደ፡ተ ጻፈ። በሰላም፡ የሚያስተምሩ፡ እግራቸው፡ መልካ ም፡ ነው ። በመልካም፡ የምስረች፡ የሚነግሩ።
*ኢሳ፡ ፶፪፡ ፯፡፡

፲፮፤ ነገር፡ግን፡ሁሉ፡ለወንጌል፡አልታዘዙም፡ኢሳይ ያስ፡ ይላልና። አቤቱ፡ ማን፡ ምስክራችነን፡ ያምናል።
*ኢሳ፡ ፶፫፡ ፩፡፡ ዮሐ፡ ፲፪፡ ፴፰፡፡

፲፯፤ እንጊዲህ፡ *ሃይማኖት፡ከመስማት፡ነው። መ ስማትም፡ ከእግዚአብሔር፡ ቃል፡ ነው።
*ዮሐ፡ ፲፯፡ ፳፡፡

፲፰፤ ነገር፡ግን፡እላለሁ፡በውኑ፡ አልሰሙምን። እን ዴት፡ነው፡ያ፡ያለው፡ *በምድር፡ሁሉ፡ላይ፡ ነገራቸው፡ ወጣ ። ቃላቸውም ፡ እስከ፡ †ዓለም፡ ደርቻ፡ ድረስ።
*መዝ፡ ፲፱፡ ፭፡፡ †ኢሳ፡ ፵፱፡ ፮፡፡ ቆላ፡ ፩፡ ፳፫፡፡

፲፱፤ ነገር፡ግን፡ እላለሁ፡ የእሥራኤል፡ ልጆች፡ በው ኑ፡አላወቁም። አስቀድሞ፡ ሙሴ፡ ይላል፡ *አስቀናች ኋለሁ፡ወገን፡ባልሆነው፡ በማያስተውልም፡ ወገን፡አ ስቈጣችኋለሁ። *ዘዳግ፡ ፴፪፡ ፳፩፡፡

፳፤ ኢሳይያስ፡ግን፡በነገር፡ደፈረ፡አለም። ተገኘሁ፡ ወደ፡ ማይሹኝ። ተገለጥሁ፡ ላልጠየቁኝ።
ኢሳ፡ ፷፭፡ ፩፡፡

፳፩፤ ስለ፡እሥራኤል፡ግን፡ አለ። ቀኑን፡ሁሉ፡ እጄ ን፡ ዘረጋሁ፡ ባመፀኛ፡ ሕዝብ፡ ላይ፡ የማይሰማ።
ኢሳ፡ ፷፭፡ ፪፡፡

## ምዕራፍ፡ ፲፩፤

፩፤ እላለሁም፡እግዚአብሔር፡ወገኖቹን፡ *ፈጽሞ ን፡ተዋቸው። አይደለም፡ እኔ፡ ደግሞ፡ የእሥራኤል፡ ወገን፡ ነኝና ። ከአብርሃም፡ዘር፡ ከብንያሚን፡ ወገን።
ኤር፡ ፴፩፡ ፴፯፡፡ ፊል፡ ፫፡ ፬፡—፲፡፡

፪፤ እግዚአብሔር፡ ወገኑን፡ አስቀድሞ፡ ያወቀው ን፡ አልተወውም። ወይስ፡ አታውቁምን፡ መጽሐፍ፡ ምን፡ ይላል፡ በኤልያስ ። እሥራኤልን፡ ወደ፡ እግዚአ ብሔር፡ገሳጣ፡ጊዜ፡ እንዲህ፡ ሲል።

፫፤ አቤቱ፡ ነቢያትህን፡ *ገደሉ፡መሠዊያህንመ፡ አ ፈረሱ። እኔም፡ ብቻዬን፡ ቀረሁ፡ እርሳቸውም፡ ነፍሴ ን፡ ይሻሉ። *፩፡ ነገሥ፡ ፲፱፡ ፲፡ ፲፬፡፡

፬፤ ነገር፡ ግን ፡ ምን ፡ አለው ፡ እምላካዊ ፡ *ምላሽ። ለኔ፡ሰባት፡ሺህ፡ ሰው፡አስቀረሁ፡ ለብዔል፡ ያልሰገዱ።
*፩፡ ነገሥ፡ ፲፱፡ ፲፰፡፡

፭፤ እንደሁም ፡ ደግሞ፡ በዚህ፡ ዘመን፡ በጸጋ፡ የተ መረጡት፡ *ቅሬታ፡ ነው። *ም፡ ፱፡ ፳፯፡፡

፮፤ በጸጋም፡ ቢሆን ፡ በምግባራቸው ፡ አይደለም። እንኪያስ፡ጸጋ፡ጸጋ፡አትሆንም።በምግባርም፡ ቢሆን፡ በጸጋ፡አይደለውም። እንኪያስ፡ምግባር፡ደግሞ፡ ም ግባር፡ አይደለውም። ዘዳግ፡ ፱፡ ፬፡ ፭፡፡

፯፤ እንጊዲህ፡ምንድር፡ነው፡ *እሥራኤል፡ ይሹት፡ የነበረውን፡አልወሰዱም፡የተመረጡት፡ግን፡ወሰዱ፡ የቀሩትም፡ታወሩ። ም፡ ፱፡ ፴፩፡፡

፰፡ እንደ፡*ተጻፈ።እግዚአብሔር፡ የንቅልፍ፡መን
ፈስ፡ሰጣቸው።የማታይ፡ ዓይን፡የማትሰማም፡ጆሮ፡
እስከ፡ ዛሬ፡ ድረስ። *ኢሳ፡ ፮፡ ፲፡፡ ፳፱፡ ፲፡፡
፱፡ ዳዊትም፡*ይላል።ማዕዳቸው፡በፊታቸው፡ወ
ጥመድ፡ ትሁን፡ መሰናክልም፡ ፍዳም።
*መዝ፡ ፷፰፡ ፳፪፡ ፳፫፡፡
፲፡ ዓይናቸው፡ ትጨልም፡ እንዳያዩ። ጀርባቸው
ም፡ ይጕበጥ፡ ሁለጊዜ።
፲፩፡ እንግዲህም፡እላለሁ። በውኑ፡ ተሰናከሉ፡ ሊ
ወድቁ።አይደለም።ነገር፡ግን፡*በመሰናከላቸው፡ደህ
ንነት፡ ሆነ፡ ለአሕዛብ፡ እርሳቸውን፡ ለማስቀናት።
*የሐዋ፡ ፲፫፡ ፵፮፡፡ ሮሜ፡ ፲፡ ፲፱፡፡
፲፪፡ መሰናከላቸው፡ ግን፡ ለዓለም፡ ባለጸግነት፡ ከ
ሆነ፡መጕደላቸውም፡ክብር፡ለአሕዛብ።*ፍጻሜያቸ
ው፡ እንዴት፡ ከዚህ፡ ይብልጥ። *ሆሴ፡ ፩፡ ፲፡፡
፲፫፡ እኔ፡ለላንተ፡እላለሁ፡ እላንተ፡የአሕዛብ፡ ወገ
ን።እኔ፡ለአሕዛብ፡ሐዋርያ፡ ሁኜለሁና፡መልእክቴን፡
አከብር፡ዘንድ።
፲፬፡ ዘመዶቼን፡አስቀና፡ እንደሆን፡ ከርሳቸውም፡
ሰዎችን፡*አድን፡እንደሆን። *፩፡ ጢሞ፡ ፬፡ ፲፮፡፡
፲፭፡ መውደቃቸው፡ለዓለም፡መታረቅ፡ከሆነ።መ
ቀበላቸውስ፡ ምን፡ ይሆን፡ ከሙታን፡ መዳን፡ ሌላ።
፲፮፡ እርሾው፡የተቀደሰ፡ከሆነ፡ብሆውም፡የተቀደ
ሰ፡ ነው። ሥሩም፡ ንጹ፡ ከሆነ፡ ጫፎችም፡ እንዲሁ፡ና
ቸው።
፲፯፡ ከጫፎችም፡ተከፍለው፡*ቢሰበሩ፡ አንተም፡
በስፍራቸው፡ ተተከልህ። አንተ፡ መራራ፡ወይራ፡ በር
ስዋም፡ኣፈጥህ፡ ለዘይትም፡ ሥር፡ ባልንጀራ፡ሆንህ።
ኤፌ፡ ፪፡ ፲፩፡—፲፱፡፡ *ኤር፡ ፲፩፡ ፲፮፡፡
፲፰፡ በጫፎች፡ ላይ፡ አትኵራ። የኵራህ፡ ግን፡ እን
ደ፡ሆንህ፡አንተ፡ ሥሩን፡ የተሸከምህ፡ አይደለህም።
ነገር፡ግን፡ሥሩ፡አንተን፡ተሸክሞሃል። ዮሐ፡ ፬፡ ፳፪፡፡
፲፱፡ ወይስ፡ትለኛለህን፡ጫፎች፡ ተሰበሩ፡ እኔ፡ እተ
ከል፡ዘንድ። የሐዋ፡ ፲፫፡ ፵፮፡፡
፳፡ መልካም፡ አልህ።እርሳቸው፡ ሃይማኖት፡ ባይ
ኖራቸው፡ ተሰበሩ። አንተም፡ በሃይማኖት፡ ጸናህ። ል
ብህን፡*አታስታብይ፡ነገር፡ግን፡ፍራ። *፩፡ ቆሮ፡ ፲፡ ፲፪፡፡
፳፩፡ እግዚአብሔርም፡ በባሕርያቸው፡ ለተመረ
ጡ፡ ጫፎች፡ ያላዘነ፡ ከሆነ፡ ላንትም፡ እንዳያዝን፡ ተ
ጠበቅ።
፳፪፡ አሁንም፡የእግዚአብሔርን፡ቸርነት፡ ተመል
ከት፡መጽናቱንም። ጽናቱ፡ግን፡በወደቁት፡ላይ።*ቸር
ነቱም፡ ባንተ፡ላይ፡ ነው። በቸርነቱ፡ ብትጸና። እንኪያ
ስ፡አንተም፡ደግሞ፡ትቈረጣለህ። *ዮሐ፡ ፲፭፡ ፪፡ ፬፡፡
ዕብ፡ ፫፡ ፲፬፡፡
፳፫፡ እለዚያም፡ በኑፋቄ፡ ባይጸኑ፡ይተከላሉ፡ ደግ
ሞ። እግዚአብሔር፡ ሁለተኛ፡ *ይተክላቸው፡ ዘንድ፡
ይችላልና። *፪፡ ቆሮ፡ ፫፡ ፲፮፡፡
፳፬፡ አንተ፡ በባሕርይ፡ መራራ፡ከሆነ፡ ወይራ፡ ከተ
ቈረጥህ፡በለመለመ፡ ዘይትም፡ባሕርይ፡ *የተተከል
ህ፡ከሆንህ። እንዴት፡ይበልጡ፡እለዚያ፡በባሕርይ፡የ
ጸፈጡት፡ በዘይታቸው፡ ይተከሉ፡ ዘንድ።
*ኤር፡ ፲፩፡ ፲፮፡፡
፳፭፡ እኔም፡እወዳለሁ፡ ወንድሞቼ፡ ሆይ፡ ይህን፡
ምሥጢር፡ ታውቁ፡ ዘንድ፡ በራሳችሁ፡ ምክር፡ ጠቢባ
ን፡እንዳትሆኑ።የልብ፡ደንደንነት፡ በእሥራኤል፡ ሁና
ባቸዋልና፡ከርሳቸው፡ ተከፍሎ፡ *የአሕዛብ፡ ፍጻሜ፡
እስኪገባ፡ ድረስ። *ሉቃ፡ ፳፩፡ ፳፬፡፡ ዮሐ፡ ፲፡ ፲፮፡፡
፳፮፡ እንዲሁም፡ እሥራኤል፡*ሁሉ፡ ይድናል። እ
ንደ፡ተጻፈ።†መድኀኒት፡ከጽዮን፡ ይመጣልና፡ ከያዕ
ቆብም፡ ኃጢአት፡ **ይመልሳል። *ማቴ፡ ፳፫፡ ፴፱፡፡
†ኢሳ፡ ፳፯፡ ፱፡፡ ፶፱፡ ፳፡፡ **መዝ፡ ፲፬፡ ፯፡፡
፳፯፡ ይህም፡*ኪዳኔ፡ ይሆንላቸዋል፡ ኃጢአታቸ
ውንም፡እፍቅላቸዋለሁ። *ኤር፡ ፴፩፡ ፴፩፡—፴፬፡፡
፳፰፡ በወንጌልም፡እርሳቸው፡ ጸላት፡ ናቸው፡ ስለ
ላንት፡ በመመረጥ፡ ግን፡ ወዳጆች፡ ናቸው፡ ስላባቶች።
፳፱፡ እግዚአብሔር፡ ከመስጠቱ፡ ከመጽራቱም፡
አይመለስምና።
፴፡ እላንትም፡ ቀድሞ፡ ለእግዚአብሔር፡እንዳል
ታዘዛችሁ።ዛሬም፡ይቅር፡አላችሁ፡በለዚያ፡ ማመፅ፡
፴፩፡ እንዲሁ፡እርሳቸው፡ዛሬ፡አልታዘዙም፡በም
ህረታችሁ፡ ለርሳቸው፡ ደግሞ፡ ይቅር፡ ይላቸው፡ ዘን
ድ።
፴፪፡ እግዚአብሔር፡ ሁሉን፡ *በክሕደት፡ ዘግቶታ
ልና፡†ሁሉን፡ ይምር፡ ዘንድ። *ገላት፡ ፫፡ ፳፪፡፡
†፩፡ ጢሞ፡ ፪፡ ፬፡፡
፴፫፡ የጥበቡ፡ ጥልቅ፡ ሆይ፡ የባለጸግነቱም፡ የእግ
ዚአብሔርም፡እውቀት። ፍርዱም፡ሆይ፡የማትገኝ፡
መንገዱም፡ የማትመረመር። ም፡ ፱፡ ፳፫፡፡ ፲፡ ፲፪፡፡
ኢሳ፡ ፵፭፡ ፲፭፡፡
፴፬፡ ማነው፡ የእግዚአብሔርን፡ *አሳብ፡ የሚያ
ውቅ። ወይስ፡ማነው፡የመከረው። *ኢዮብ፡ ፲፭፡ ፰፡፡
ኢሳ፡ ፵፡ ፲፫፡፡ ኤር፡ ፳፫፡ ፲፰፡፡ ፩፡ ቆሮ፡ ፪፡ ፲፮፡፡
፴፭፡ ወይስ፡ ማነው፡*አስቀድሞ፡ የሰጠው፡ አን
ደች፡ ደግሞ፡ ከርሱ፡ ብድራቱን፡ ይወስድ፡ ዘንድ።
*ኢዮብ፡ ፵፩፡ ፪፡፡
፴፮፡ ሁሉ፡ ከርሱ፡ ነውና፡ በርሱም፡ነውና፡ወደርሱ
ም፡ ነው። ለርሱም፡ ምስጋና፡ ይገባዋል፡ ለዘላለም።
አሜን።

ምዕራፍ፡ ፲፪፡

፩፡ እኔ፡ ግን፡ እለምናችኋለሁ፡ ወንድሞቼ፡ ሆይ፡
በእግዚአብሔር፡ ምህረት። *ሥጋችሁን፡ ታቀርቡ፡ ዘ
ንድ፡ ሕያውት፡ መሥዋዕት፡ አድርጋችሁ፡ የተቀደሰ
ች፡እግዚአብሔርን፡ደስ፡የምታሰኝ። እርሱዋም፡በአ
እምሮ፡ ያለች፡ ማገልገላችሁ፡ ናት። *ም፡ ፮፡ ፲፫፡፡
፩፡ ጴጥ፡ ፪፡ ፭፡፡
፪፡ የዚህችንም፡ ዓለም፡ ሰዎች፡ አትምሰልዋቸ
ው፡ ነገር፡ ግን፡ መልካችሁን፡ ለውጡ፡ ወደ፡ አእምር

ዋችሁ፡ *መታደስ።የእግዚአብሔርን፡ †ፈቃድ፡ታው ቁ፡ ዘንድ፡ መልካሚቱን፡ ፍጹሚቱን፡ የተቀበለች ውን። *ኤፌ፡ ፬፤ ፳፫፡፡ †ኤፌ፡ ፭፤ ፲፤ ፲፯፡፡

፫፤ በተሰጠችኝም፡ጸጋ፡እላንትን፡ሁላችሁን፡እላ ለሁ። የማይገባውን፡ መጋደድ፡ እንዳትጋደዱ። አ ሳባችሁ፡ ባቅም፡ ይሁን፡ እንጂ፡ ኢያንዳችሁ፡ እግዚ አብሔር፡ እንደ፡ ከፈለው፡ *እንደ፡ ሃይማኖቱ፡ መ ጠን። *፩፤ ቆሮ፡ ፲፪፤ ፲፩፡፡ ኤፌ፡ ፬፤ ፯፡፡

፬፤ ለኛም፡ እጅግ፡ ብልት፡ እንዳለነ፡ *ባንድ፡ ሥጋ፡ የሥጋም፡ ብልት፡ ሁሉ፡ ስራው፡ አንድ፡ አይደለም። ኤፌ፡ ፬፤ ፳፭፡፡

፭፤ እንደሁ፡እኛ፡ ደግሞ፡ *እጅግ፡ ነነ፡ አንድ፡ ሥጋ ም፡ ነነ፡ በክርስቶስ። ከኛም፡ ኢያንዳንዳችን፡ እርሱ፡ በርሳችን፡ ብልት፡ ነነ። *፩፤ ቆሮ፡ ፲፪፤ ፳፯፡፡

፮፤ ነገር፡ግን፡የልዩ፡ ልዩ፡ ስጦታ፡ አለችነ፡ በተሰጠ ችነ፡ ጸጋ። ከኛም፡ ትንቢት፡ የተሰጠው፡ እንደ፡ ሃይ ማኖቱ፡ መጠን፡ ትንቢት፡ ይናገር። ፩፤ ቆሮ፡ ፲፪፤ ፬፡፡

፯፤ አገልጋይም፡ ቢሆን፡በማገልገሉ፡ይንቃ። አስተ ማሪም፡ ቢሆን፡ በማስተማሩ። ፩፤ ጴጥ፡ ፬፤ ፲፤ ፲፩፡፡

፰፤ ገሣጺም፡ ቢሆን፡ በመገሠጽ። *የሚሰጥ፡ደስ፡ ብሎት፡ ይስጥ። አለቅነት፡ ያለው፡ በልባምነት፡ ያድ ርግ፡ የሚመጸውትም፡ †በደስታ። *ማቴ፡ ፮፤ ፫፡፡ †፪፤ ቆሮ፡ ፰፤ ፪፡፡ ፱፤ ፯፡፡

፱፤ *ፍቅራችሁ፡በግብዝነት፡ አትሁን። †ክፉውን፡ ጥሉ፡ መልካሙንም፡ ተጠበቁ። ፩፤ ጢሞ፡ ፩፤ ፭፡፡ †መዝ፡ ፴፯፡ ፲፡፡

፲፤ በወንድም፡*ፍቅር፡ተዋደዱ፡እርሱ፡በርሳችሁ። እርሱ፡በርሳችሁ፡በማክብር፡ተቀዳደሙ።ፊል፡፪፤፫፡፡

፲፩፤ በስራም፡ አትስነፉ፡በመንፈሳችሁ፡ *የምትቃ ጠሉ፡ ሁኑ፡ ለእግዚአብሔርም፡ የተገዛችሁ። *ራእ፡ ፫፤ ፲፭፡፡ ኤፌ፡ ፭፤ ፲፮፡፡

፲፪፤ በተስፋችሁ፡ ደስ፡ ያላችሁ፡ ሁኑ። *በመከራ፡ የምትታገሡ። በጸሎት፡አትረፉ። *፩፤ ተሰ፡ ፭፤ ፲፯፡፡

፲፫፤ ለቅዱሳን፡ በሚሹት፡ ነገር፡ የምትራዱ፡ ሁኑ። ስደተኞችን፡ *ለመቀበል፡ የተቀዳደማችሁ፡ ሁኑ። *ዘፍ፡ ፲፰፤ ፫፤ ና፡ ፲፱፤ ፪፤ ፫፡፡ ዕብ፡ ፲፫፤ ፪፡፡

፲፬፤ የሚያሳድዋችሁን፡ *ባርኩ። መርኩ፡ አትርገ ሙም። *ማቴ፡ ፭፤ ፵፬፡፡ የሐዋ፡ ፯፤ ፶፱፡፡ ፩፤ ቆሮ፡ ፬፤ ፲፪፡፡

፲፭፤ ደስ፡ ካላቸው፡ ጋራ፡ ደስ፡ ይበላችሁ። *ከሚ ያለቅሱ፡ ጋራ፡ አልቅሱ። መዝ፡ ፴፭፤ ፲፫፡፡ *ማቴ፡ ፳፭፤ ፴፮፡፡

፲፮፤ *አንዲት፡ አሳብ፡ አስቡ፡ እርሱ፡ በርሳችሁ። የትዕቢትን፡ ነገር፡ አታስቡ። ከትሑታን፡ ጋራ፡ ተያያ ዙ፡ እንጂ። ም፡ ፲፭፤ ፭፡፡

፲፯፤ በራሳችሁ፡ ዘንድ፡ *ጠቢባን፡ አትሁኑ። ለማ ንም፡ †ክፉውን፡ በክፉ፡ አትመልሱ። ቅንን፡ ነገር፡ ለ ማድረግ፡ አስቡ፡እንጂ፡ በሰው፡ ሁሉ፡ ፊት። *ኢሳ፡ ፭፤ ፳፩፡፡ ፩፤ ተሰ፡ ፭፤ ፲፭፡—፳፬፡፡

፲፰፤ ቢቻላችሁስ፡ሰላም፡አድርጉ። በላንትና፡ *በሰ ው፡ ሁሉ፡ መካከል። *ማር፡ ፱፤ ፶፡፡ ዕብ፡ ፲፪፤ ፲፬፡፡

፲፱፤ *ቂምም፡ አትያዙ፡ ወደጀቼ፡ ሆይ። (ለእግዚ አብሔር፡) ቍጣ፡ ስፍራ፡ ስጡት፡ እንጂ። †ተጽፏዋ ልና። በቀል፡ ለኔ፡ ነው፡ እኔ፡ ፍዳውን፡ እከፍላለሁ፡ እግዚአብሔር፡ ይላል። *ዘሌዋ፡ ፲፱፤ ፲፰፡፡ ማቴ፡ ፭፤ ፴፱፡፡ †ዘዳግ፡ ፴፪፤ ፴፭፡፡

፳፤ እንጊዴህ፡ *ጸላትህ፡ ቢራብ። አብላው፡ ቢጠ ማም፡ አጠጣው። ይህነን፡ ያደረግህ፡ እንደ፡ ሆንህ፡ በራሱ፡ ላይ፡ የሳት፡ ፍም፡ ትሰበስባለህና። *ምሳ፡ ፳፭፤ ፳፩፡ ፳፪፡፡ ማቴ፡ ፭፤ ፵፬፡፡

፳፩፤ ክፉ፡ አያሸንፍህ። ክፉውን፡ በበጎ፡ አሸንፍ፡ እንጂ።

## ምዕራፍ፡ ፲፫፤

፩፤ ሰው፡ ሁሉ፡ ይገዛ፡ *ለተሾመው፡ መኰንን። ሹ መት፡ አይሆንምና፡ †ከእግዚአብሔር፡ ዘንድ፡ በቀ ር። እርሳቸውም፡ከእግዚአብሔር፡ዘንድ፡የተሾሙ፡ ናቸው። *ቲቶ፡ ፫፤ ፩፡፡ †ዮሐ፡ ፲፱፤ ፲፩፡፡ ምሳ፡ ፰፤ ፲፭፡፡

፪፤ እንጊዴህ፡ ሹሙን፡ የሚቋቋም፡ የእግዚአብ ሔርን፡ ሥርዓት፡ ይቋቋማል፡ተቋቋሞችም፡ ፍርድ፡ በራሳቸው፡ ላይ፡ ያመጣሉ።

፫፤ አለቆች፡ መልካም፡ በሚያደርግ፡ ላይ፡ ለፍርሃ ት፡ አይደሉምና፡ በክፉ፡ እንጂ። መኰነኑንስ፡ እንዳ ትፈራ፡ ብትወድ፡ መልካም፡ አድርግ፡ ከርሱ፡ ዘንድ ም፡ ክብር፡ ይሆንልሃል። ፩፤ ጴጥ፡ ፪፤ ፲፫፤ ፲፬፡፡

፬፤ የእግዚአብሔር፡ ሎሌ፡ ላንተ፡ነውና፡ ለበጎ። ክ ፉ፡ ግን፡ብታደርግ፡ፍራ፡በከንቱ፡ሰይፍ፡አይታጠቅም ና፡ *የእግዚአብሔር፡ ሎሌ፡ ስለ፡ ሆነ፡ ነው፡ እንጂ። ክፉ፡ የሚያደርገውን፡ በቅጣት፡ የሚበቀል።, *መዝ፡ ፹፪፤ ፯፡፡

፭፤ ስለዚህም፡ ለርሱ፡ *መገዛት፡ ይገባናል። ስለ፡ ቅጣት፡ ብቻ፡ አይደለም፡ ስለ፡ ሕሊናችን፡ ንጽሕና፡ ደግሞ፡ እንጂ። *፩፤ ጴጥ፡ ፪፤ ፲፫፡፡

፮፤ ስለዚህም፡ ደግሞ፡ ግብር፡ትሰጣላችሁና። የእ ግዚአብሔር፡ አገልጋዮች፡ ናቸውና፡ በዚህ፡ ነገር፡ ሁለ ግዜ፡ የሚያግለግሉ።

፯፡ ለሁሉም፡ *ኢያንዳንዱ፡ የሚገባውን፡ ስጡ። ግብር፡ ለሚገባው፡ ግብሩን። ካሥር፡ አንድ፡ለሚገባ ው፡ካሥር፡አንዱን። ፍርሃት፡ለሚገባው፡ፍርሃቱን። ክብር፡ ለሚገባው፡ ክብሩን። *ማቴ፡ ፳፪፤ ፳፩፡፡ ማር፡ ፲፪፤ ፲፯፡፡

፰፤ ከላንተ፡ ላንዳችሁ፡ ሌላ፡ ዕዳ፡ አይሁን፡እርሱ፡ በርሳችሁ፡ ከመዋደድ፡ በቀር። *ባልንጀራውን፡የሚ ወድ፡ ሕግን፡ ፈጽሞታልና። *ገላት፡ ፭፤ ፲፬፡፡ ፩፤ ጢሞ፡ ፩፤ ፭፡፡

፱፤ ይህም፡ የተባለው። አታመንዝር። አትግደል፡ አትስረቅ። ባሰት፡ አትመስክር፡ አትመኝ። ሌላም፡

ትእዛዝ፡ ብትኖር፡ በዚች፡ ቃል፡ ተደዛለች። *ባልንጀራህን፡ ውደድ፡ እንደ፡ ራስህ። *ዘሌዋ፡ ፲፱፡ ፲፰።

፲፡ *ፍቅር፡ ባልንጀራውን፡ ክፉ፡ አያደርግም። ስለዚህም፡ የሕግ፡ ፍጻሜው፡ ፍቅር፡ ነው።
*ማቴ፡ ፳፪፡ ፵። ፩፡ ቆሮ፡ ፲፫፡ ፬።

፲፩፡ ይህነንም፡ዘመን፡እወቁ፡ *ከምኝታችን፡ የምንነሣበት፡ ጊዜ፡ እንደለ፡ ዛሬ፡ †መድኃኒት፡ ወደኛ፡ የቀረበ፡ ነውና፡ ካመነበት፡ ጊዜ፡ ይልቅ።
*ኤፌ፡ ፭፡ ፲፬። ፩፡ ተሰ፡ ፭፡ ፮፡ ፯። †ዕብ፡ ፮፡ ፱።

፲፪፡ *ሌሊቱም፡ ሔደ፡ ቀኑም፡ ቀርብዋል። ስለዚህ፡ የጨለማውን፡ ስራ፡ ከኛ፡ †አውጥተን፡ እንጣል። የብርሃንም፡ ጋሻ፡ ጦር፡ እንልበስ። *፩፡ ዮሐ፡ ፪፡ ፰።
†ኤፌ፡ ፭፡ ፲፩።

፲፫፡ በቀኑም፡ እንሒድ፡ *በቅን፡ ነገር። በዘፈንና፡ በስካር፡ አይደለም። በዝሙትም፡ አይደለም፡ በሴሰኝነትም፡ †በፀብም፡በቅናትም። *ሉቃ፡ ፳፩፡ ፴፬።
†ኤፌ፡ ፭፡ ፲፰።

፲፬፡ ጌታን፡ የሱስ፡ ክርስቶስን፡ *ልበሱት፡ እንጂ። ሥጋውንም፡ለፍትወት፡አትደግፉ። *ገላት፡ ፫፡ ፳፯።

## ምዕራፍ፡ ፲፬።

፩፡ በሃይማኖት፡ *የደከመውን፡ ተቀበሉት፡ በክርክርም፡ በብዙም፡ አሳብ፡ አትሁኑ። *ም፡ ፲፭፡ ፩።
፩፡ ቆሮ፡ ፰፡ ፱።

፪፡ ከሰዎች፡ የሚያምን፡ አለ፡ ሁሉን፡ ይበላ፡ ዘንድ፡ እንዲገባው። ደካማ፡ ግን፡ *አታክልት፡ ይበላል።
*ዘፍ፡ ፩፡ ፳፱።

፫፡ *የሚበላ፡ የማይበላውን፡አይናቅ። የማይበላም፡ በሚበላው፡ አይፍረድ፡ እግዚአብሔር፡ ተቀብሎታልና። *ቆል፡ ፪፡ ፲፮።

፬፡ አንተ፡ *ምንድር፡ ነህ፡ በሌላው፡ ባርያ፡ የምትፈርድ። ቢቆምም፡ ለጌታው፡ ነው፡ ቢወድቅም። ይቆምማል፡ እግዚአብሔር፡ ያስነሣው፡ ዘንድ፡ ይችላልና። *ማቴ፡ ፯፡ ፩። ያዕ፡ ፬፡ ፲፩፡ ፲፪።

፭፡ ከሰዎች፡ ከቀን፡ ይልቅ፡ ቀን፡ *የሚጠብቅ፡ አለ። ከርሳቸውም፡ ቀኑን፡ ሁሉ፡ የሚይዝ፡ አለ። ሁሉ፡ ኢያንዳንዱ፡ ባሳቡ፡ ፈጽሞ፡ ይወቅ።
*ገላት፡ ፬፡ ፲።

፮፡ ላንድ፡ ቀን፡ ያስበ፡ለእግዚአብሔር፡ያስበዋል፡ ለቀንም፡ የማያስብ፡ ለእግዚአብሔር፡ አያስበውም። የሚበላውም፡ ለእግዚአብሔር፡ *ይበላል፡ እግዚአብሔር፡ አይበላም፡ እግዚአብሔርንም፡ ያመሰግናል። *ዘዳግ፡ ፰፡ ፲። ፩፡ ቆሮ፡ ፲፡ ፴፩።

፯፡ ከኛ፡ ሕይወቱ፡ ለራሱ፡ የሆነ፡የለም። ሞቱም፡ ለራሱ፡ የሆነ፡ የለም።

፰፡ *ብንኖርም፡ ለእግዚአብሔር፡ እንኖራለን። ብንሞትም፡ ለእግዚአብሔር፡ እንሞታለን። እንግዲህ፡ ሕያዋንም፡ ብንሆን፡ ወይም፡ ሙታን፡ እኛ፡ ለእግዚአብሔር፡ ነን። *ገላት፡ ፪፡ ፲። ፩፡ ተሰ፡ ፭፡ ፲።

፱፡ ስለዚህም፡ ክርስቶስ፡ *ሞተ፡ ተመልሶም፡ ሕያው፡ ሆነ፡ የሕያዋንና፡የሙታን፡ጌታ፡ይሆን፡ ዘንድ።
*የሐዋ፡ ፲፡ ፵፪።

፲፡ አንተስ፡ ለምን፡ በወንድምህ፡ *ትፈርዳለህ። አንተስ፡ ምንድር፡ ነህ፡ ወንድምህን፡ የምትንቅ። ሁላችን፡ በክርስቶስ፡ ወንበር፡ ፊት፡ እንቆማለንና።
*የሐዋ፡ ፲፯፡ ፴፩። ማቴ፡ ፳፭፡ ፴፩፡ ፴፪።

፲፩፡ ተጽፏልና። እኔ፡ሕያው፡ነኝ። እግዚአብሔር፡ ይላል። ጉልበት፡ *ሁሉ፡ ለኔ፡ ይንበረከካል፡መላስም፡ ሁሉ፡ ለእግዚአብሔር፡ ይገዛል።
*ኢሳ፡ ፵፭፡ ፳፫። ፊል፡ ፪፡ ፲።

፲፪፡ አሁንም፡ ከኛ፡ *ኢያንዳንዳችን፡ የእግዚአብሔር፡ ምላሽ፡ ይሰጣል። *ገላት፡ ፮፡ ፭።

፲፫፡ እንግዲህ፡ ደግሞ፡ እርሱ፡ በርሳችን፡ አንፍረድ። ይህነንስ፡ ፍረዱ፡ እንጂ። ዕንቅፋት፡ ወይም፡ ማሰናከያ፡ *ለወንድማችን፡ እንዳናደርግ።
*ማቴ፡ ፲፰፡ ፯።

፲፬፡ እኔ፡ አውቃለሁና፡ ኢምናለሁምና፡ በጌታ፡ በየሱስ፡ ርኩስ፡ እንደ፡ *ሌላ፡ በርሱ፡ ዘንድ። ነገር፡ ግን፡ ርኩስ፡ የሚመስለው፡ ማናቸውም፡ ሁሉ፡ እርሱ፡ ለሰው፡ ርኩስ፡ነው። *ማቴ፡ ፲፭፡ ፲፩። የሐዋ፡ ፲፡ ፲፭።
ቲቶ፡ ፩፡ ፲፭።

፲፭፡ አንተ፡ ሆይ፡ ወንድምህን፡ ስለ፡ መብል፡ የምታሳዝን፡ ከሆንህ፡ በፍቅር፡ መሔድህ፡ የታለ። *በመብልህ፡ ያን፡ አታጥፋው፡ ክርስቶስ፡ስለርሱ፡ የሞተለትን። *፩፡ ቆሮ፡ ፰፡ ፲፩—፲፫።

፲፮፡ እንግዲህ፡ በጎነታችሁ፡ አይሰደብ።
ቲጦ፡ ፪፡ ፭።

፲፯፡ የእግዚአብሔር፡ *መንግሥት፡ መብል፡ መጠጥም፡አይደለምና። ነገር፡ግን፡ጽድቅ፡ነው፡ሰላምም፡ ደስታም፡ በመንፈስ፡ቅዱስ። *ሉቃ፡ ፲፯፡ ፳።

፲፰፡ በዚህም፡ ለክርስቶስ፡ የሚገዛ፡ እርሱ፡ እግዚአብሔርን፡ *ደስ፡ ያሰኛል፡ በሰውም፡ ዘንድ፡ የተፈተነ፡ ነው። *፩፡ ተሰ፡ ፪፡ ፲፭።

፲፱፡ አሁንም፡እንቀደደም፡ ሰላምን፡ በመሻት፡ እርሱ፡ በርሳችነንም፡ በማነጽ። ም፡ ፲፪፡ ፲፰። ፲፭፡ ፪።

፳፡ ስለ፡ መብል፡ የእግዚአብሔርን፡ ስራ፡ አታፍርስ። ሁሉ፡ ንጹሕ፡ ነውና፡ ነገር፡ ግን፡ ለሰው፡ ክፉው፡ በእንቅፋት፡ የሚበላው፡ ነው። ቍ፡ ፲፬።

፳፩፡ ሥጋም፡ ባትበላ፡ ጸጅም፡ ባትጠጣ፡ *መልካም፡ ነው፡እንድስም፡ ባታደርግ፡ ወንድምህ፡ የሚሰናከልበት፡ ወይም፡ የሚያዝንበት፡ ወይም፡ የሚደክምበት። *፩፡ ቆሮ፡ ፰፡ ፲፫።

፳፪፡ አንተ፡ ሃይማኖት፡እንዳለህ፡ ለራስህ፡ ይሁንልህ፡ በእግዚአብሔር፡ ፊት። ምስጉን፡ ነው፡ በራሱ፡ *የማይፈርድ፡ በሚያደርገው፡ ነገር።
*፩፡ ዮሐ፡ ፫፡ ፳፩።

፳፫፡ ሲበላ፡ የሚጠራጠር፡ ግን፡ ራሱን፡ አስኰነነ።

ያው፡ በሃይማኖት፡ አይደለምና። *ከሃይማኖትም፡ ያልሆነው፡ ሁሉ፡ ኃጢአት፡ ነው። *ቲጦስ፡ ፩፡ ፲፭። ዕብ፡ ፲፩፡ ፮።

ምዕራፍ፡ ፲፭፡

፩፡ እኛም፡ ኃይለኞች፡ ይገባናል፡ የሚደክሙትን፡ *ድካም፡ እንሸከም፡ ዘንድ፡ ለራሳችንንም፡ አናድላ። *ም፡ ፲፬፡ ፩።

፪፡ ነገር፡ ግን፡ ኢያንዳንዷም፡ *ለባልንጀራው፡ ያድላ፡ በመልካም፡ ለመሥራት። *፩፡ ቆሮ፡ ፱፡ ፲፱። ፩፡ ቆሮ፡ ፲፡ ፳፬፡ ፴፪።

፫፡ ክርስቶስ፡ ደግሞ፡ ለራሱ፡ አላደላምና። እንደ፡ *ተጻፈ። የሚላገዲህ፡ መላገድ፡ በላዬ፡ ወደቀ። *መዝ፡ ፷፰፡ ፲።

፬፡ አስቀድሞ፡ *የተጻፈው፡ ሁሉ፡ እኛን፡ለማስተማር፡ ተጽፎዋልና። ተስፋ፡ ይሆንልን፡ ዘንድ፡ በትዕግሥት፡ በመጻሕፍትም፡ ባለ፡ ማጽናናት። *ም፡ ፬፡ ፳፫፡ ፳፬።

፭፡ እግዚአብሔርም፡የትዕግሥትና፡የደስታ፡አምላክ፡ *አንድ፡ አሳብ፡ ይሰጣችሁ፡ እርሱ፡ በርሳችሁ፡ በየሱስ፡ ክርስቶስ። *ፊል፡ ፫፡ ፲፮።

፮፡ ባንድ፡ ልብ፡ ባንድም፡ አፍ፡ እግዚአብሔርን፡ ታመሰግኑ፡ ዘንድ፡ የጌታችነን፡ የየሱስ፡ ክርስቶስን፡ አባት።

፯፡ ስለዚህም፡እርሱ፡ በርሳችሁ፡ ተቀባበሉ፡ ክርስቶስ፡ እንደ፡ ተቀበለን፡ ለእግዚአብሔር፡ ክብር።

፰፡ እላለሁም፡ ክርስቶስ፡ የግዝረት፡ *አገልጋይ፡ እንደ፡ ሆነ፡ ስለ፡ እግዚአብሔር፡ እውነት፡ ያባቶችን፡ †ተስፋ፡ያጸና፡ ዘንድ። *ማቴ፡ ፲፭፡ ፳፬። †የሐዋ፡ ፫፡ ፳፫።

፱፡ አሕዛብም፡ ስለ፡ *ምህረት፡ እግዚአብሔርን፡ ያመሰግኑ፡ ዘንድ፡ እንደ፡ †ተጻፈ። ስለዚህ፡ እገዛልሃለሁ፡ በአሕዛብ፡ ለስምህም፡ዝማሬ፡አቀርባለሁ። *ም፡ ፲፩፡ ፴። †መዝ፡ ፲፰፡ ፶። ፪፡ ሳሙኤ፡ ፳፪፡ ፶።

፲፡ ደግሞም፡ አለ። ደስ፡ ይበላችሁ፡ እላንተ፡ አሕዛብ፡ ከሕዝቡ፡ ጋራ። *ዘዳግ፡ ፴፪፡ ፵፫።

፲፩፡ ደግሞም፡ አለ። *አሕዛብ፡ ሁላችሁ፡ እግዚአብሔርን፡ አመስግኑ። ሕዝብም፡ሁሉ፡ ያመስግኑት። መዝ፡ ፻፲፮፡ ፩።

፲፪፡ *ኢሳይያስም፡ ደግሞ፡ አለ። †ሥር፡ለእሴይ፡ ይሆናል፡ ከርሱም፡ የሚነሣ፡ ለአሕዛብ፡ አለቃ፡የሚሆን፡አሕዛብም፡ተስፋ፡ያደርጉታልና። *ኢሳ፡ ፲፩፡ ፲። †ራእ፡ ፭፡ ፭።

፲፫፡ እግዚአብሔር፡ ግን፡ የተስፋ፡ አምላክ፡ *ደስታን፡ ሁሉ፡ ሰላምንም፡ ይምላባችሁ፡ በሃይማኖት። በተስፋ፡ ትበዙ፡ዘንድ፡ በመንፈስ፡ ቅዱስ፡ ኃይል። *ም፡ ፲፬፡ ፲፯።

፲፬፡ እኔም፡ ወንድሞቼ፡ አምኘችኋለሁ፡ መልካምን፡ ነገር፡ ሁሉ፡ እንደ፡ መላችሁ። *እውቀትንም፡ ሁሉ፡ እንደ፡ መላችሁ፡ እርሱ፡ በርሳችሁንም፡ መምከር፡ እንዲቻላችሁ። *፪፡ ጴጥ፡ ፩፡ ፲፪። ፩፡ ዮሐ፡ ፪፡ ፳፩።

፲፭፡ ነገር፡ ግን፡ በድፍረት፡ ጻፍሁላችሁ፡ ወንድሞቼ፡ ሆይ፡ እላንትን፡ ጥቂት፡ አሳስባችሁ፡ዘንድ፡ ከእግዚአብሔር፡ ዘንድ፡ በተሰጠኝ፡ *ጸጋ። *ም፡ ፩፡ ፭። ፲፪፡ ፫።

፲፮፡ ለየሱስ፡ ክርስቶስ፡ *አገልጋይ፡ እሆን፡ ዘንድ፡ በአሕዛብ። ለእግዚአብሔር፡ ወንጌልም፡ ካህን፡ እሆን፡ ዘንድ፡ የአሕዛብ፡ ቍርባን፡ የተቀበለ፡ ይሆን፡ ዘንድ፡ በመንፈስ፡ ቅዱስ፡ የተቀደሰ። *ም፡ ፲፩፡ ፲፫። ፊል፡ ፪፡ ፲፯።

፲፯፡ ትምክሕትም፡ አለኝ፡ በየሱስ፡ ክርስቶስ፡ ከእግዚአብሔር፡ ዘንድ።

፲፰፡ አንዲት፡ ነገርም፡ እል፡ ዘንድ፡ አልደፍርም፡ *ክርስቶስ፡ በጄ፡ ካላደረገው፡በቃል፡ በምግባርም፡ አሕዛብ፡ †ይሰሙ፡ዘንድ። *፪፡ቆሮ፡ ፫፡፭። †ም፡፩፡፭።

፲፱፡ በተአምራትና፡ በምልክት፡ *ኃይል፡ በመንፈስ፡ ቅዱስም፡ ኃይል። ከየሩሳሌም፡ ጀምሬ፡ እስከ፡ ኤሊሪቁን፡ ድረስ፡ እዞር፡ ዘንድ፡ ክርስቶስንም፡ ማስተማር፡ እፈጽም፡ ዘንድ። *ማር፡ ፲፮፡ ፲፯።

፳፡ እንደሁም፡ እጋደላለሁ፡ ወንጌልን፡ በማስተማር። *የክርስቶስ፡ ስም፡ ከተጻፈበት፡ስፍራ፡ አይደለም። በሌላው፡ መሠረት፡ ላይ፡ እንዳልሰራ። *፪፡ ቆሮ፡ ፲፡ ፲፭፡ ፲፮።

፳፩፡ ነገር፡ ግን፡ እንደ፡ *ተጻፈ። ወሬው፡ ያልደረሰላቸው፡ ያዩታል። ያልሰሙትም፡ ያስተውላሉ። *ኢሳ፡ ፶፪፡ ፲፭።

፳፪፡ *ስለዚህም፡ እጅግ፡ ጊዜ፡ ቀረቡ፡ ወደላንተ፡ ከመምጣት። *ም፡ ፩፡ ፲፫። ፩፡ ተሰ፡ ፪፡ ፲፰።

፳፫፡ አሁን፡ ግን፡ ስፍራ፡ የለኝም፡ወደዚች፡አገር። *እጅግም፡ እወድ፡ ነበርሁ፡ ወደላንተ፡ እመጣ፡ ዘንድ፡ ከብዙ፡ ዘመን፡ ጀምሬ። *ም፡ ፩፡ ፲፡ ፲፩።

፳፬፡ ወደ፡ እስጳንያም፡ በሔድሁ፡ ጊዜ፡ ተስፋ፡ አደርጋለሁ፡አያችሁ፡ ዘንድ፡ ወደዚያ፡ሳልፍ። *እላንተም፡ ትሸኙኝ፡ ዘንድ፡ አስቀድሜ፡ እላንትን፡ በማየት፡ ጥቂት፡ ከጸገብሁ፡ በኋላ። *፩፡ ቆሮ፡ ፲፮፡ ፮።

፳፭፡ *አሁን፡ ግን፡ ወደ፡ የሩሳሌም፡ እሔዳለሁ፡ ለቅዱሳን፡ አገለግል፡ ዘንድ። *የሐዋ፡ ፲፰፡ ፳፩። የሐዋ፡ ፲፱፡ ፳፩። ፳፡ ፳፪።

፳፮፡ በመቄዶንያና፡ በአካይያ፡ያሉት፡ፈጽመው፡ ወደዋልና፡ *መቀራመጥ፡ ያደርጉ፡ ዘንድ፡ በየሩሳሌም፡ ከሚኖሩ፡ ከድኆች፡ ከቅዱሳን፡ ጋራ። *፩፡ ቆሮ፡ ፲፮፡ ፩። ፪፡ ቆሮ፡ ፰፡ ፩—፬።

፳፯፡ ይህነንም፡ ለመስራት፡ ወደዋል፡ እርሱም፡ ይገባቸዋል። *አሕዛብም፡ ከርሳቸው፡ ጋራ፡ በመንፈሳዊ፡ነገር፡ ከተካፈሉ፡በሥጋዊ፡ነገር፡ያገለግልዋቸው፡ ዘንድ፡ ይገባቸዋል። *ም፡ ፱፡ ፬። ፩፡ ቆሮ፡ ፱፡ ፲፩።

፳፰፡ ይህነንም፡ በፈጸምሁ፡ ጊዜ፡ ይህችንም፡ ፍ

ሬ፡ ለርሳቸው፡ባተምሁ፡ ጊዜ፡ በላንት፡ አልፌለሁ፡ ወደ፡ እስጳንያ።

፳፱፤ እኔም፡ አውቃለሁ፡ ወደላንት፡ በመጣሁ፡ ጊዜ፡ አደርስባቸኋለሁ፡ በፍጹም፡በክርስቶስ፡ወንጌል፡ *በረከት። *ም፡ ፩፤ ፲፩፡፡

፴፤ እለምናችኋለሁ፡ ግን፡ ወንድሞቼ፡ ሆይ፡ በጌታችን፡ በየሱስ፡ ክርስቶስ፡ *በመንፈስ፡ ቅዱስም፡ ፍቅር፡ ከኔ፡ ጋራ፡ ትጋደሉ፡ ዘንድ፡ በጸሎት፡ ስለኔ፡ ወደ፡ እግዚአብሔር። *፪፤ ቆሮ፡ ፩፤ ፲፩፡፡ ፊል፡ ፩፡ ፲፱፡፡ ፪፤ ተሰ፡ ፫፤ ፩፡፡

፴፩፤ ከማይታዘዙ፡ በይሁዳ፡ ምድር፡ እንድን፡ ማገልገሌም፡ በየሩሳሌም፡ ለሚኖሩ፡ ቅዱሳን፡ የተቀበለች፡ ትሆን፡ ዘንድ።

፴፪፤ ወደላንት፡ በደስታ፡ እመጣ፡ ዘንድ፡ በእግዚአብሔር፡ ፈቃድ፡ ከላንትም፡ ጋራ፡ አርፍ፡ ዘንድ።

፴፫፤ *የሰላምም፡ አምላክ፡ ከላንት፡ ከሁላችሁ፡ ጋራ፡ ይሁን። አሜን። ም፡ ፯፤ ፴፡፡

ምዕራፍ፡ ፲፮፤

፩፤ አማጽኛችኋለሁ፡ ፊቤንን፡ እታችነን፡ በክንህርኤስ፡ ላለችው፡ ቤተ፡ ክርስቲያን፡ አገልጋይ፡ የምትሆን።

፪፤ በጌታችን፡ ትቀበልዋት፡ ዘንድ፡ ለቅዱሳን፡ እንዲገባ፡ ታግዝዋትም፡ ዘንድ፡ ከላንት፡ በምትሻው፡ ነገር፡ ሁሉ፡እርስዋ፡ ብዙን፡ አግዛለችና፡ እኔም፡ደግሞ።

፫፤ *ጵርስኪላን፡አኪላስንም፡እንዴት፡ናችሁ፡በክርስቶስ፡የሱስ፡የሚያግዙኝን። *የሐዋ፡ ፲፰፤ ፪፤ ፳፮፡፡

፬፤ እለዚህ፡ ስለ፡ ነፍሴ፡ አንገታቸውን፡ ሰጥተዋልና። እኔም፡ብቻዬን፡የማመሰግናቸው፡አይደለሁም፡ የአሕዛብም፡ ጉባዔ፡ ሁሉ፡ እንጅ።

፭፤ እንደሁም፡ በቤታቸው፡ ያሉትን፡ *ማኅበር፡ሁሉ። ኤጲኔጦስን፡ ወደጄን፡ እንዴት፡ ነህ፡ በሉት፡ የእካያ፡ መጀመርያ፡ የሚሆን፡ በክርስቶስ። ፩፤ ቆሮ፡ ፲፮፤ ፲፭፤ ፲፱፡፡

፮፤ ማርያምን፡ እንዴት፡ ነሽ፡ በልዋት፡ ስለኛ፡ እጅግ፡ የደከመች።

፯፤ አንድሮኒኮስን፡ እንዴት፡ ነህ፡ በሉት፡ ዩንያስንም፡ ዘመዶቼን፡ ከኔ፡ ጋራ፡ ባንድ፡ የታሠሩትን። እርሳቸውም፡የታወቁ፡ ናቸው፡ በሐዋርያት፡ ዘንድ፡ እርሳቸውም፡ በክርስቶስ፡ ሣይማኖት፡ ቀደሙኝ። ፪፤ ቆሮ፡ ፰፤ ፳፫፡፡

፰፤ አምጵሊያስን፡ እንዴት፡ ነህ፡በሉት፡ ወዳጄን፡ በጌታችን።

፱፤ ኡውርባኖስን፡ አጋዣችነን፡ በክርስቶስ፡ እንዴት፡ ነህ፡ በሉት። አስጣኩስንም፡ ወዳጄን።

፲፤ አጵሌስን፡ እንዴት፡ነህ፡በሉት፡በክርስቶስ፡ የተፈተነውን። የአርስጦቡሉስን፡ ሰዎች፡ እንዴት፡ ናችሁ፡ በሉ።

፲፩፤ ሄሮድዮንን፡ዘመዴን፡ እንዴት፡ ነህ፡ በሉት፡ የነርኪሰስን፡ ሰዎች፡ እንዴት፡ ናችሁ፡ በሉ፡ እርሳቸውም፡ በእግዚአብሔር፡ያሉ።

፲፪፤ ጥራፊናንና፡ ጠሪፎሳን፡ ስለ፡ እግዚአብሔር፡ የደከሙ፡ እንዴት፡ ናችሁ፡ በሉ። ጵርሲስን፡ የተወደደችውን፡ እንዴት፡ ነሽ፡በልዋት፡ስለ፡እግዚአብሔር፡ እጅግ፡ የደከመች።

፲፫፤ *ሩፎስን፡ እንዴት፡ ነህ፡በሉት፡በእግዚአብሔር፡ ዘንድ፡ የተመረጠውን። እናቱንም፡ ለኔም፡ ደግሞ፡ እናቴ፡ የምትሆን። *ማር፡ ፲፭፤ ፳፩፡፡

፲፬፤ አሲንክሪጦስን፡ እንዴት፡ ነህ፡ በሉት፡ አፍሌጎንንም። ሔርማስንም፡ ጳጥሮባስንም፡ ሔርሜስንም። ከርሳቸው፡ ጋራ፡ ያሉትንም፡ ወንድሞች።

፲፭፤ ፊሎሎጎስን፡ ዩልያንም፡ እንዴት፡ ናችሁ፡ በሉ፡ ኒርዮስንና፡ እኅቱንም፡ ኦሊምጳስንም፡ ከርሳቸውም፡ ጋራ፡ ያሉትን፡ ቅዱሳን፡ ሁሉ።

፲፮፤ እርሱ፡ በርሳችሁ፡ *በሰላም፡ ተገናኙ፡ በተቀደሰ፡ መሳም። የክርስቶስ፡ ቤተ፡ክርስቲያኖች፡ እንዴት፡ ናችሁ፡ ይልዋችኋል። *፩፤ ቆሮ፡ ፲፮፤ ፳፡፡

፲፯፤ እለምናችኋለሁ፡ግን፡ወንድሞቼ፡ሆይ፡ *ትጠባበቋቸው፡ዘንድ፡መለየት፡ መጠራጠርም፡ የሚያደርጉን፡ከተማራችሁት፡ትምህርት፡የወጣ፡ ከርሳቸውም፡ †ትለዩ፡ ዘንድ። *ማቴ፡ ፯፤ ፲፭፡፡ †ቲቶ፡ ፫፤ ፲፡፡

፲፰፤ እርሳቸው፡ እንዲህ፡ የሚያደርጉ፡ ለጌታችን፡ ለየሱስ፡ክርስቶስ፡ባሮች፡ አይደሉምና፡ *ለሆዳቸው፡ እንጅ። †በጻፈጠም፡ ነገር፡ በመልካምም፡ የየዋሃን፡ ልብ፡ ያጠፋሉ። *ፊል፡ ፫፤ ፲፱፡፡ †ሕዝ፡ ፲፫፤ ፲፰፡፡ ቆል፡ ፪፤ ፬፡፡

፲፱፤ *የመታዘዛችሁ፡ ወሬ፡ በሁሉ፡ ዘንድ፡ ደርሶዋልና። እኔንም፡በላንት፡ ደስ፡ይለኛል። እወድማለሁ፡ ለመልካም፡ ነገር፡ ጠቢባን፡ ትሆኑ፡ ዘንድ፡የዋሃንም፡ ለክፉ፡ ነገር፡ ሁሉ። *ም፡ ፩፤ ፰፡፡ ፩፤ ቆሮ፡ ፲፬፤ ፳፡፡

፳፤ እግዚአብሔርም፡ *የሰላም፡አምላክ፡ ሰይጣንን፡ ከግራችሁ፡ በታች፡ ፈጥኖ፡ ይቀጥቅጠው። የጌታችን፡ የየሱስ፡ ክርስቶስ፡ ጸጋ፡ ከላንት፡ ጋራ፡ ይሁን። አሜን። *ም፡ ፲፭፤ ፴፫፡፡

፳፩፤ *ጢሞቴዎስ፡ ባልንጀራዬ፡ በማድረግ፡ እንዴት፡ ናችሁ፡ ይላችኋል። ሉኪዮስም፡ ያሶንም፡ ሶሲጳጥሮስም፡ዘመዴ። *የሐዋ፡ ፲፮፤ ፩፤ ፪፡፡ ፊል፡ ፪፤ ፲፱፡፡

፳፪፤ እንዴታላችሁ፡እላችኋለሁ፡ እኔ፡ ጠርጥዮስ፡ ይህቺን፡ መልእክት፡ የጻፍሁ፡ በእግዚአብሔር።

፳፫፤ እንዴት፡ ናችሁ፡ ይላችኋል፡ *ጋይዮስ፡ እንግድነት፡የተቀበለኝ፡ ቤተ፡ ክርስቲያንንም፡ ሁሉ፡ የሚቀበል። እንዴት፡ናችሁ፡ ይላችኋል፡†ኤራስጦስ፡ ያገሩ፡ አለቃ፡ ቁአርጦስም፡ ወንድም። *፩፤ ቆሮ፡ ፩፤ ፲፬፡፡ †የሐዋ፡ ፲፱፤ ፳፪፡፡

፳፬፤ የጌታችን፡ የየሱስ፡ ክርስቶስ፡ጸጋ፡ከሁላችሁ፡ ጋራ፡ ይሁን፡ አሜን።

፳፭፤ አሁንም፡ በወንጌሌ፡ በየሱስ፡ ክርስቶስም፡ ትምህርት፡ ያጸናችሁ፡ ዘንድ፡ ለሚችል፡ *ምሥጢር

ን፡ በመግለጽ፡ ተከፍንት፡ ጀምር፡ ተሠውሮ፡ የነበረውን። *ኤፌ፡ ፩፡ ፱፡፡ †ኤፌ፡ ፫፡ ፭፡ ፱፡፡

፳፮፡ ዛሬም፡ ፈጽሞ፡ የተገለጠ፡ ከነቢያትም፡ መጻሕፍት፡ በዘላለም፡ በእግዚአብሔር፡ ትእዛዝ፡ በአሕዛብ፡ ሁሉ፡ የታወቀ፡ በሃይማኖት፡ ለመታዘዝ። ፪፡ ጢሞ፡ ፩፡ ፲፡፡ ሮሜ፡ ፩፡ ፲፡፡

፳፯፡ እርሱ፡ እግዚአብሔር፡ *ብቻውን፡ጥበብ፡ ያለው። ለርሱ፡ ምስጋና፡ ይሁን፡ በየሱስ፡ ክርስቶስ፡ ለዘላለም። አሜን። *፩፡ ጢሞ፡ ፩፡ ፲፯፡፡ ይሁ፡ ፳፭፡፡

ተፈጸመች፡ መልክት፡ ወደ፡ሮሜ፡ ሰዎች፡ በቆሮንቶስም፡ ተጻፈች፡ በክንህርኤስም፡ ባለችው፡ ቤተ፡ ክርስቲያን፡ አገልጋይ፡ በፊቤን፡ እጅ፡ ተላከች።

# የሐዋርያው ፡ የጳውሎስ ፡ መልእክት ፡ መጀመርያይቱ ፡ ወደ ፡ ቆርንቶስ ፡ ሰዎች ።

## ምዕራፍ፡ ፩፡

፩፡ ከጳውሎስ፡ *የተጸራ፡ የየሱስ፡ ክርስቶስ፡ ሐዋርያ፡ በእግዚአብሔር፡ ፈቃድ፡ ከሶስቴኔስም፡ ወንድም። *ገላት፡ ፩፡ ፩፡፡

፪፡ ወደ፡እግዚአብሔር፡ ቤተ፡ ክርስቲያን፡ በቆርንቶስ፡ ያለች፡ በክርስቶስ፡ የሱስ፡ ወደ፡ *ተቀደሱት፡ ወደ፡ ተጸሩት፡ ቅዱሳን። የጌታችነን፡ የየሱስ፡ ክርስቶስን፡ ስም፡ ከሚጸሩት፡ ሁሉ፡ ጋራ፡ በስፍራቸው፡ ሁሉ፡ በኛም። *ምዕ፡ ፮፡ ፲፩፡፡ የሐዋ፡ ፱፡ ፲፬፡፡

፫፡ *ጸጋ፡ ለላንት፡ ይሁን፡ ሰላምም፡ ካባታችን፡ ካምላክ። ከጌታም፡ከየሱስ፡ክርስቶስ። *ሮሜ፡ ፩፡ ፯፡፡

፬፡ አምላኬን፡*አመሰግናለሁ፡ሁልጊዜ፡ስለላንት፡ በተሰጣችሁ፡ በእግዚአብሔር፡ ጸጋ፡ በክርስቶስ፡ የሱስ። *ኤፌ፡ ፩፡ ፲፭፡ ፲፮፡፡

፭፡ በሁሉ፡ባለ፡ ጸጋ፡ሁናችኋልና፡በርሱ። በነገርም፡ ሁሉ፡ *በውቀትም፡ ሁሉ። *ምዕ፡ ፲፪፡ ፰፡፡

፮፡ የክርስቶስ፡ ምስክር፡ በላንት፡ እንደ፡*ጸና። *ሮሜ፡ ፩፡ ፲፮፡፡

፯፡ *አልጐደላችሁምና፡ ስጥወታው፡ አንድ፡ ስንኳ። ነገር፡ ግን፡ የጌታችነን፡ የየሱስ፡ ክርስቶስን፡ †መገለጥ፡ ደጅ፡ ትጸናላችሁ። *መዝ፡ ፴፬፡ ፲፩፡፡ †ፊል፡ ፫፡ ፳፡፡

፰፡ እርሱ፡ እስከ፡ ፍጻሜ፡ *የሚያጸናችሁ፡ ያለ፡ †ነውር፡ እንድትሆኑ፡ በየሱስ፡ ክርስቶስ፡ ቀን። *ፊል፡ ፩፡ ፮፡፡ †፩፡ ተሰ፡ ፫፡ ፲፫፡፡

፱፡ እግዚአብሔር፡*እውነተኛ፡ነው፡ወደ፡ጌታችን፡ ወደ፡ የሱስ፡ክርስቶስ፡ ወደ፡ ልጁ፡ አንድነት፡ የጸራችሁ። *፩፡ ተሰ፡ ፭፡ ፳፬፡፡

፲፡ እለምናችኋለሁ፡ግን፡ ወንድሞቼ፡ ሆይ፡ በጌታችን፡ በየሱስ፡ ክርስቶስ፡ ስም፡ የምትናገርዋት፡ ነገር፡ አንዲት፡ ትሆን፡ ዘንድ፡ ለሁላችሁ። በላንትም፡ መካከል፡መለያየት፡ አይሁን። የጸናችሁም፡ ትሆኑ፡ ዘንድ፡ *ባንድ፡ ልብ፡ ባንድም፡ ምክር። *ፊል፡ ፪፡ ፪፡ ፫፡ ፲፮፡፡

፲፩፡ ስለላንትም፡ ፈጽሜ፡ አወቅሁ፡ ወንድሞቼ፡ ሆይ፡ ከቀሎኤ፡ ሰዎች፡ ሰምቻለሁና፡ በላንት፡ዘንድ፡ ክርክር፡ እንዳለ።

፲፪፡ እነግራችሁማለሁ፡ ከላንት፡ ኢያንዳንዱ፡እንዲል። *እኔ፡ለጳውሎስ፡ነኝ። †እኔም፡ለአጵሎስ፡ነኝ። እኔም፡ ለኬፋ፡ እኔም፡ ለክርስቶስ። *ምዕ፡ ፫፡ ፬፡፡ †የሐዋ፡ ፲፰፡ ፳፬፡፡ ዮሐ፡ ፩፡ ፵፪፡፡

፲፫፡ በውኑ፡ክርስቶስ፡ተከፈለ።ወይስ፡ጳውሎስን፡ ስለላንት፡ ተሰቀለ፡ ወይስ፡ በጳውሎስን፡ ስም፡ ተጠመቃችሁ።

፲፬፡ እግዚአብሔርን፡ አመሰግናለሁ፡ ከላንት፡ አንድ፡ ስንኳ፡ አላጠመቅሁም፡ *ከክሪስጶስና፡ ከጋይዮስ፡ በቀር። *የሐዋ፡ ፲፰፡ ፰፡፡

፲፭፡ ማንም፡ እንዳይል፡ እኔ፡ በስሜ፡ እንዳጠመቅሁ።

፲፮፡ ደግሞም፡ *የእስጢፋኖስን፡ ቤት፡ አጠመቅሁ። ከርሳቸውም፡ ሌላ፡ አንድ፡ ሰው፡ ያጠመቅሁትን፡ አላውቅም። *ምዕ፡ ፲፮፡ ፲፭፡ ፲፯፡፡

፲፯፡ ክርስቶስ፡ አላከኝምና፡ አጠምቅ፡ ዘንድ፡በወንጌል፡ አስተምር፡ ዘንድ፡ እንጂ። በነገር፡ *ጥበብ፡ አይደለም፡ የክርስቶስ፡ መስቀል፡ ከንቱ፡እንዳይሆን። *ዮሐ፡ ፬፡ ፪፡፡ ማቴ፡ ፳፰፡ ፲፱፡፡ ምዕ፡ ፪፡ ፬፡፡

፲፰፡ የመስቀሉ፡ነገር፡*በጥፎች፡ዘንድ፡ስንፍና፡ነውና። በኛ፡ግን፡በዳነው፡ዘንድ፡ የእግዚአብሔር፡ †ኃይል፡ ነው። *፪፡ ቆሮ፡ ፬፡ ፫፡፡ †ሮሜ፡ ፩፡ ፲፮፡፡

፲፱፡ *ተጽፏልና፡የጠቢባንን፡ጥበብ፡አጠፋለሁ። ያዋቆችንም፡ እውቀት፡ እንቃለሁ። *ኢሳ፡ ፳፱፡ ፲፬፡፡

፳፡ *ጠቢብ፡የታለ። ጸፊስ፡የታለ። የዚህ፡ዓለም፡ መርማሪስ፡ የታለ። እግዚአብሔር፡ የዚህን፡ዓለም፡ ጥበብ፡ ስንፍና፡ ያደረገ፡ አይደለምን። *ኢዮብ፡ ፲፪፡ ፲፯፡፡ ኢሳ፡ ፴፫፡ ፲፰፡፡

፳፩፡ በእግዚአብሔርም፡ ጥበብ፡ ዓለም፡ *በጥበቡ፡ እግዚአብሔርን፡ ባላወቀ፡ ጊዜ። እግዚአብሔር፡ በትምህርቱ፡ ስንፍና፡ የሚያምኑትን፡ ያድን፡ ዘንድ፡ ወደደ። *ማቴ፡ ፲፩፡ ፳፭፡፡

፳፪፡ አይሁድ፡ *ምልክት፡ይጠይቃሉና፡የፅርዕም፡ ሰዎች፡ ጥበብ፡ ይሻሉና። *ማቴ፡ ፲፪፡ ፴፰፡፡ ዮሐ፡ ፬፡ ፵፰፡፡ የሐዋ፡ ፲፯፡ ፲፰፡ ፴፪፡፡

፳፫፡ እኛ፡ ግን፡በክርስቶስ፡እናስተምራለን፡ በተሰ

ቀለው። *ያውም፡በአይሁድ፡ዘንድ፡እንቅፋት፡ነው፡ በአሕዛብም፡ ዘንድ፡ ስንፍና፡ ነው። *ሮሜ፡ ፱፡ ፴፪። ፩፡ ቆሮ፡ ፪፡ ፲፬።

፳፬፡ በተጸሩት፡ ዘንድ፡ ግን፡ ከአይሁድም፡ ከአሕዛብም፡ክርስቶስ፡ የእግዚአብሔር፡ *ኃይል፡ ነው፡ የእግዚአብሔርም፡ ተጥበብ፡ ነው። *ቍ፡ ፲፰። ተቀል፡ ፪፡ ፫።

፳፭፡ የእግዚአብሔር፡ ስንፍና፡ ከሰው፡ ጥበብ፡ ይበልጣልና፡ የእግዚአብሔርም፡ ድካም፡ ከሰው፡ ኃይል፡ ይበረታልና።

፳፮፡ አዩ፡እንዴት፡*ተጸራችሁ፡ወንድሞቼ፡ሆይ። ከላንት፡ እጅግ፡ጠቢባን፡የለባችሁምና፡እንደ፡ ሥጋ። እጅግም፡ ኃያላን፡ የለባችሁምና። እጅግም፡ የዘመድ፡ ታላቅነት፡ የላችሁምና። *ማቴ፡ ፲፩፡ ፳፭። ዮሐ፡ ፯፡ ፵፰። ያዕ፡ ፪፡ ፩፡ – ፭።

፳፯፡ ነገር፡ ግን፡ እግዚአብሔር፡ የዚህን፡ዓለም፡ ሰነፎች፡ መረጠ፡ጠቢባንን፡ያሳፍር፡ዘንድ። የዚህንም፡ ዓለም፡ ደካሞች፡ መረጠ፡ ኃያላንን፡ ያሳፍር፡ዘንድ።

፳፰፡ የዘመድ፡ ታላቅነት፡ የሌላቸውንም፡ በዚህ፡ ዓለም፡ የተናቁትንም፡እግዚአብሔር፡መረጣቸው። ያልሆኑንም፡ የሚሆኑን፡ ከንቱ፡ ያደርግ፡ ዘንድ።

፳፱፡ ማንም፡ ከሰው፡ በእግዚአብሔር፡ ፊት፡ *እንዳይመካ። *ሮሜ፡ ፫፡ ፳፯። ኤፌ፡ ፪፡ ፱።

፴፡ እላንት፡ ግን፡ ከርሱ፡ ናችሁ፡በየሱስ፡ክርስቶስ፡ ጥበብ፡የሆነልን፡ ከእግዚአብሔር፡ *ጽድቅም፡ ተቅድስናም፡ መድኃኒትም። *ኤር፡ ፳፫፡ ፭፡ ፮። ፪፡ ቆሮ፡ ፭፡ ፳፩። ተዮሐ፡ ፲፯፡ ፲፱።

፴፩፡ እንደ፡*ተጻፈ። የሚመካ፡በእግዚአብሔር፡ ይመካ። *ኢሳ፡ ፷፭፡ ፲፮። ኤር፡ ፱፡ ፳፫፡ ፳፬። ፪፡ ቆሮ፡ ፲፡ ፲፯።

## ምዕራፍ፡ ፪፡

፩፡ እኔም፡ ወደላንት፡ በመጣሁ፡ጊዜ፡ወንድሞቼ፡ ሆይ፡ ነገር፡ በማበርታት፡ አልመጣሁባችሁም፡ በጥበብም፡ *የእግዚአብሔርን፡ ምሥጢር፡ አላስተማርኋችሁም። *ም፡ ፩፡ ፲፯።

፪፡ በራሴም፡ አልፈረድሁም፡አንዳች፡አውቅ፡ ዘንድ፡በላንት፡ መካከል፡ *ከየሱስ፡ ክርስቶስ፡ በቀር፡ እርሱንም፡የተሰቀለውን። *ገላት፡ ፮፡ ፲፬።

፫፡ እኔም፡ *በድካም፡ በፍርሃትም፡ በጽኑም፡መንቀጥቀጥ፡ በላንት፡ ዘንድ፡ ነበርሁ። *የሐዋ፡ ፲፰፡ ፱። ፪፡ ቆሮ፡ ፲፡ ፩።

፬፡ *ነግሬም፡ ትምህርቴም፡ በሚወደድ፡ በሰው፡ ጥበብ፡ ነገር፡ አልነበረም። ነገር፡ ግን፡ መንፈስ፡ቅዱስ፡ በተገለጠበት፡ነበር፡እንጂ፡በኃይልም። *ም፡ ፩፡ ፲፯።

፭፡ ሃይማኖታችሁ፡ በሰው፡ ጥበብ፡ እንዳይሆን፡ ነገር፡ ግን፡ በእግዚአብሔር፡ *ኃይል። *ኤፌ፡ ፩፡ ፲፯፡ ፲፱። ፩፡ ተሰ፡ ፩፡ ፭።

፮፡ ለፍጹማን፡ ግን፡ በጥበብ፡ እንናገራለን። ነገር፡ ግን፡ በዚህ፡ዓለም፡ ጥበብ፡ ዓይደለም። በዚህም፡ ዓለም፡ አለቆች፡ ጥበብ፡ በሚጠፋ፡ አይደለም።

፯፡ ነገር፡ ግን፡ የእግዚአብሔርም፡ ጥበብ፡ በምሥጢር፡እንናገራለን፡ተሠውሮ፡በነበረው።እግዚአብሔር፡ አስቀድሞ፡ ያዘጋጀው፡ ዓለም፡ ሳይፈጠር፡ ለክብራችን። ሮሜ፡ ፲፮፡ ፳፭።

፰፡ ማንም፡ ያላወቀው፡ ከዚህ፡ዓለም፡ አለቆች። ቢያውቁስ፡ *የምስጋናን፡ ጌታ፡ ባልሰቀሉም። *ሉቃ፡ ፳፫፡ ፴፬። ያዕ፡ ፪፡ ፩። መዝ፡ ፳፬፡ ፰፡ ፱።

፱፡ ነገር፡ግን፡ እንደ፡ *ተጻፈ። ዓይን፡ያላየችው፡ ጆሮም፡ ያልሰማው፡ በሰው፡ ልብም፡ ያልታሰበ፡ እግዚአብሔር፡ ለሚወዱት፡ ያዘጋጀው፡ ነው። *ኢሳ፡ ፷፬፡ ፩።

፲፡ *ለኛ፡ ግን፡ እግዚአብሔር፡ ያነን፡ ገለጠልነ፡ በመንፈሱ። መንፈስ፡ ሁሉን፡ይመረምራልና፡ ደግሞም፡ እግዚአብሔር፡ ጠልቀ፡ የመከረውን። *ማቴ፡ ፲፫፡ ፲፩።

፲፩፡ ማነው፡ የሚያውቅ፡ ሰው፡ በሰው፡ ያለውን፡ ከሰው፡ መንፈስ፡ በቀር፡ በርሱ፡ያለው። እንደሁም፡ የእግዚአብሔርን፡ አሳብ፡ማንም፡ አያውቅም፡ ከእግዚአብሔር፡ መንፈስ፡ በቀር።

፲፪፡ እኛ፡ግን፡የዓለምን፡ መንፈስ፡ አልወሰድነም፡ ነገር፡ግን፡ ከእግዚአብሔር፡ዘንድ፡ያለውን፡መንፈስ፡ ነው ፡ እግዚአብሔር፡ የሰጠነን፡ ስጦታ፡ እናውቅ፡ ዘንድ።

፲፫፡ የምንናገርበትም፡እርሱ፡ ነው።ከሰው፡ ጥበብም፡ ነገር፡ትምህርት፡ አይደለም። ይህ፡ በመንፈስ፡ትምህርት፡ ነው፡እንጂ። የመንፈሳውያን፡ ነገር፡ ለመንፈሳውያን፡እናስተካክላለንና። ቍ፡ ፩፡ ፬። ም፡ ፩፡ ፲፯።

፲፬፡ ሥጋዊ፡ ሰው፡ ግን፡ የእግዚአብሔርን ፡ መንፈስ፡ ነገር፡አይቀበልም፡ በርሱ፡ ዘንድ፡ *ስንፍና፡ ነውና። ያስተውለውም ፡ ዘንድ ፡ አይቻለውም ፡ በመንፈስ፡ ይፈረድበታልና። *ም፡ ፩፡ ፳፫። ዮሐ፡ ፰፡ ፵፯።

፲፭፡ *መንፈሳዊ፡ሰው፡ግን፡ሁሉን፡ይፈርደል። እርሱ፡ግን፡ከማንም፡አይፈረድም። *፩፡ ዮሐ፡ ፪፡ ፳።

፲፮፡ ማነውስ፡ የእግዚአብሔርን፡ *አሳብ፡ ያወቀ፡ እርሱን ፡ ሊመክረው ። እኛ፡ ግን፡ የክርስቶስ፡ አሳብ፡ አለነ። *ሮሜ፡ ፲፩፡ ፴፬።

## ምዕራፍ፡ ፫፡

፩፡ እኔም፡ ወንድሞቼ፡ ሆይ፡ እንደ፡ መንፈሳውያን፡እነግራችሁ፡ ዘንድ፡አልቻልሁም፡ እንደ፡ ሥጋውያን፡ እንጂ ። *እንደ፡ ታናናሾች ፡ ሕፃናት፡ በክርስቶስ። *ዮሐ፡ ፲፯፡ ፲፪።

፪፡ ወተት፡ ጋትኋችሁ፡ መብልም፡ አይደለም። ያነን፡አልቻላችሁትምና፡ እስከ፡ ዛሬም፡ ድረስ፡ ደግሞ፡ አትችሉትም። ፩፡ ጴጥ፡ ፪፡ ፪። ዕብ፡ ፭፡ ፲፪፡ ፲፫።

፫፡ ገና፡ ሥጋውያን፡ ናችሁና ። ጸብ ፡ መለያየትም፡

ካለባችሁ፡ እላንት፡ ሥጋውያን፡ አይደላችሁምን፡ እ
ንደ፡ሰውም፡ ትሔዳላችሁ።    ም፡ ፲፤ ፲፩። ፲፩፡ ፲፰።
፬፥ ከላንት፡አንዱ፡ቢል። እኔ፡ የጳውሎስ፡ ነኝ። ሌላ
ውም፡እኔ፡የአጵሎስ፡ነኝ። ሥጋውያን፡መሆናችሁ፡አ
ይደለምን።    ም፡ ፩፤ ፲፪።
፭፥ ጳውሎስ፡ማነው። *አጵሎስስ፡ ማነው። ሎላል
ት፡ ናቸው ፡ እንጂ፡ በጀቸው፡ ያመናችሁ። ከርሳቸው
ም፡ ኢያንዳንዱ፡ እግዚአብሔር፡ እንደ፡ ሰጠው።
*የሐዋ፡ ፲፰፤ ፳፬።
፮፥ እኔ፡ተከልሁ። አጵሎስ፡አጠጣ፡ነገር፡ግን፡እግዚ
አብሔር፡ አሳደገ።    የሐዋ፡ ፲፰። ፬፤ ፲፩።
፯፥ እንደሁም፡ የሚተክል፡ አይጠቅምም ፡ የሚ
ያጠጣም ፡ አይጠቅምም ። የሚያሳድግ፡ እግዚአብ
ሔር፡ነው፡እንጂ።
፰፥ የሚተክልም፡የሚያጠጣም፡እርሳቸው፡ አን
ድ፡ናቸው።ሁሉም፡*ኢያንዳንዱ፡ ዋጋውን፡ ይወስ
ዳል፡እንደ፡ድካሙ።    *ም፡ ፬፤ ፭።
፱፥ እኛ ፡ የእግዚአብሔር ፡ *ሰራተኞች ፡ ነን ፡ ከርሱ
ም፡ጋራ፡ እንሰራለን። እላንት ፡ የእግዚአብሔር፡ እር
ሻ፡ናችሁ። †የእግዚአብሔር፡ ማነጽ፡ ናችሁ።
*ማቴ፡ ፲፫፤ ፫—፳፫። †ኤፌ፡ ፪፤ ፳።
፲፥ እንደ፡ተሰጠኝ፡እንደ፡እግዚአብሔር፡*ጸጋ፡መሠ
ረት፡አስቀመጥሁ፡ እንደ፡ ብልሃተኛ፡ አናጺ። ሌላው
ም፡ በላዩ፡ ይሠራል። ነገር፡ ግን፡ ሁሉ፡ ኢያንዳንዱ፡ ይ
መልከት፡እንዴት፡በላዩ፡ይሠራ፡ዘንድ። *ም፡ ፲፭፤፲።
፲፩፥ ማንም፡አይችልምና፡ሌላ፡ መሠረት፡ ይመሠ
ርት፡ዘንድ፡ከዚያ፡ከተመሠረተው፡ በቀር፡እርሱም፡
የሱስ፡ ክርስቶስ፡ ነው።    ፩፤ ጴጥ፡ ፪፤ ፬።
፲፪፥ ማንም፡ ቢሠራ፡ በዚህ፡ መሠረት፡ ላይ፡ወርቅ
ም፡ቢሆን፡ወይም፡ብር፡ወይም፡የከበረ፡ደንጊያ፡ወይ
ም፡እንጨት፡ወይም፡ሣር፡ አገዳም፡ ቢሆን።
፲፫፥ የሁሉ፡ስራ፡የተገለጠ፡ይሆናል። ያም፡ቀን፡ይገ
ልጠዋል። በሳት፡ ይታወቃልና ። *የዚያንም ፡ የዚያን
ም፡ ስራ፡እሳት፡ ይፈትነዋል።    *ኢሳ፡ ፵፰፤ ፲።
፲፬፥ የሠራው፡ስራ፡የጸናለት፡ ሰው፡ዋጋውን፡ ይወ
ስዳል።
፲፭፥ ስራው፡ግን፡ የተቃጠለበት፡ይጐዳበታል። እር
ሱ፡ ግን፡ ይድናል፡ ከሳት፡ ግን፡ እንደሚድን።
፲፮፥ አላወቃችሁምን ፡ እላንት ፡ የእግዚአብሔር፡
*መቅደስ፡እንደ፡ ሆናችሁ፡ የእግዚአብሔርም፡ መን
ፈስ፡ †አድሮባችኋል።    *ም፡ ፮፤ ፲፱።
ኤፌ፡ ፪፤ ፳፩፤ ፳፪። ዕብ፡ ፫፤ ፮። †ሮሜ፡ ፰፤ ፱።
፲፯፥ ማንም፡ የእግዚአብሔርን ፡ መቅደስ፡ ቢያጠ
ፋ፡ እርሱንም ፡ እግዚአብሔር ፡ ያጠፋዋል። የእግዚ
አብሔር ፡ ቤት፡ የተቀደሰ ፡ ነውና ፡ ያውም፡ እላንት፡
ናችሁ።
፲፰፥ ማንም፡ ራሱን፡ አያስት። የሚልም፡ሰው፡ ቢ
ኖር፡እኔ፡በዚህ፡ዓለም፡ጠቢብ፡ነኝ፡ ሰነፍ፡ይሁን፡ ጠቢ
ብ፡ ይሆን፡ ዘንድ።    ዮሐ፡ ራእ፡ ፫፤ ፲፯፤ ፲፰።

፲፱፥ የዚህ፡ዓለም፡ጥበብ፡በእግዚአበሔር፡ዘንድ፡
ስንፍና፡ነውና። ተጽፏልና። *ጠቢባንን፡ በምክራቸ
ው፡ ይይዛቸዋል።    *ኢዮ፡ ፭፤ ፲፪፤ ፲፫።
፳፥ ደግሞም ፡ *እግዚአብሔር ፡ የጠቢባንን ፡ አሳ
ብ፡ያውቃል፡ ከንቱ፡ እንደ፡ሆነ።    *መዝ፡ ፺፬፤ ፲፩።
፳፩፥ ስለዚህም፡ማንም፡ በሰው፡አይመካ። ሁሉ፡
ለላንት፡ ነውና።
፳፪፥ ጳውሎስም፡ ቢሆን፡አጵሎስም፡ቢሆን፡ኬፋ
ም፡ቢሆን፡ ዓለምም፡ ሕይወትም፡ ሞትም ፡ ያለው
ም፡የሚመጣውም፡ይህ፡ ሁሉ፡ የላንት፡ነው።
፳፫፥ *እላንትም፡ለክርስቶስ፡ናችሁ፡ ክርስቶስም፡
ለእግዚአብሔር፡ ነው።    *ም፡ ፲፩፤ ፫።

ምዕራፍ፡ ፬፥

፩፥ ስለዚህም፡ ሰዎች፡ እኛን፡ ይቍጠሩን፡ ለክርስ
ቶስ፡ እንደሚያገለግሉ፡ የእግዚአብሔርንም፡ ምሥ
ጢር፡ *እንደሚጠብቁ።    *ቲቶ፡ ፩፤ ፯።
፪፥ ከዚህም ፡ ጋራ ፡ ከመጋቦች ፡ ይፈለጋል ፡ ከርሳቸ
ው፡ሰው፡ሁሉ፡ *የታመነ፡ ሁኖ፡ ይገኝ፡ ዘንድ።
*ሉቃ፡ ፲፪፤ ፵፪።
፫፥ ይህም፡ነገር፡ለኔ፡ምናምን፡ነው፡በላንት፡ዘንድ፡
እንዲፈረድብኝ። ወይም፡ በሰው፡ቀን። እኔ፡ስንኳ፡በ
ራሴ፡ አልፈርድም።
፬፥ በራሴ ፡ ላይ ፡ አንዳችን፡ አላውቅምና ። በዚህ
ም፡ቅሉ፡አልጸደቅሁም። የሚፈርድብኝ፡ ግን፡ እግዚ
አብሔር፡ ነው።    መዝ፡ ፻፵፫፤ ፪።
፭፥ ስለዚህም፡ በምንምሥ፡ አትፈረዱ፡ከጊዜው፡አ
ስቀድማችሁ፡ ጌታ፡ እስኪመጣ፡ድረስ፡ በጨለማ፡ የ
ተሠወረውንም፡የሚያበራ፡ የልብንም፡አሳብ፡ የሚ
ገልጥ። የዚያን፡ጊዜም፡ለሁሉ፡ኢያንዳንዱ፡ ምስጋና፡
ይሆናል፡ከእግዚአብሔር፡ዘንድ።    ም፡ ፫፤ ፰።
፮፥ ይህነንም፡ ነገር፡ወንድሞቼ፡ ሆይ፡ ስለላንት፡በ
ራሴ፡መሰልሁት፡ በአጵሎስም። በኛ፡ትማሩ፡ ዘንድ፡
ከተጻፈው፡የሚበልጥ፡እንዳታስቡ። *አንዳችሁ፡ስለ
ንድ፡ሰው፡ በሌላው፡ ላይ፡ እንዳይጓደድ።
*ሮሜ፡ ፲፪፤ ፫።
፯፥ ማነው፡አንተን፡ ለየህ። ወደንተስ፡ ያለው፡ ም
ንድር፡ነው፡ያልወሰድህው። የወሰድህ፡ግን፡ ከሆንህ፡
ለምን፡ትጓደደለህ፡እንዳልወሰድህ።  ሮሜ፡ ፲፪፤ ፮።
፰፥ ዛሬ፡ እላንት፡ ጸገባችሁ። ዛሬ፡ እላንት፡ *ባለጸ
ጋ፡ ሁናችሁ። ያለኛም፡እንደ፡ ነገሥታት፡ገዛችሁ። ገዛ
ታችሁስ፡ እንደሆን፡መልካምሥ፡ነበረ፡ እኛ፡ ከላንት፡ ጋ
ራ፡ †እንገዛ፡ ዘንድ።    *ራእ፡ ፫፤ ፲፯። †ም፡ ፫፤ ፳፩።
፱፥ ለኔ፡ይመስለኛልና፡እግዚአብሔር፡እኛን፡ ሐዋ
ርያቱን፡የኋለኞችን፡የገለጠነ፡*ለሞት፡እንደሚነዱ።
ለዓለም፡ለመላእክትም፡ ለሰዎችም፡ †አተያይ፡ ሁነ
ናልና።    *ሮሜ፡ ፰፤ ፴፮። †ዕብ፡ ፲፤ ፴፫።
፲፥ እኛ፡ ስለ፡ ክርስቶስ፡*አብዶች፡ ነን፡ እላንት፡ግን፡
በክርስቶስ፡ጠቢባን፡ናችሁ። እኛ፡ደካሞች፡ ነን፡ እላን

ት፡ ግን፡ ኃይለኞች፡ ናችሁ። እላንት፡ ክቡራን፡ ናችሁ፡ እኛ፡ ግን፡ የተጠቃን። *ምዕ፡ ፫፡ ፲፰፡፡

፲፩፡ እስከዚህም፡ጊዜ፡ድረስ፡ *እንራባለን፡እንጠማማለን፡ዕራቁታችንነንም፡ ነን፡ በቡጢ፡ እንመታማለን፡የምናርፍበትም፡ስፍራ፡ የለንም።
*፪፡ ቆሮ፡ ፲፩፡ ፳፫፡—፳፯፡፡

፲፪፡ እንደክማለንም፡ *በጃችንም፡ ለነፍሳችን፡ እንሰራለን።እርሳቸው፡ †ይሰድቡናል፡እኛ፡ግን፡እንመርቃቸዋለን። **ያሳድዱናል፡ እንታገሥማለን።
*የሐዋ፡ ፲፰፡ ፫፡፡ ና፡ ፳፡ ፴፬፡፡ ፩፡ ተሰ፡ ፪፡ ፱፡፡ ፪፡ ተሰ፡ ፫፡ ፰፡፡ †ሮሜ፡ ፲፪፡ ፲፬፡፡ **መዝ፡ ፻፱፡ ፳፰፡፡

፲፫፡ ይሰድቡናል፡እንለምናቸውማለን። የዓለም፡ ጽርጊያ፡ ሆነ፡እስከ፡ዛሬ፡ለሁሉ፡እንደ፡ጕድፍም፡ነን።

፲፬፡ በዚህም፡ በጻፍሁላችሁ፡ ነገር፡ የምወቅሳችሁ፡አይደለሁም። ነገር፡ግን፡ እንደ፡ ተወደዱ፡ ልጆቼ፡ አስተምራችኋለሁ።

፲፭፡ በክርስቶስም፡ ብዙ፡ መምህራን፡ ቢኖርዋችሁ፡ነገር፡ግን፡አባቶች፡ እጅግ፡ ለላንት፡ አይደሉም። እኔ፡በክርስቶስ፡የሱስ፡ወልጀችኋለሁና፡ በወንጌሉ።
ገላት፡ ፬፡ ፲፱፡፡

፲፮፡ ስለዚህም፡እለምናችኋለሁ፡እኔን፡ እንድትመስሉ። ምዕ፡ ፲፩፡ ፩፡፡

፲፯፡ ስለዚህም፡ ጢሞቴዎስን፡ ሰደድሁላችሁ፡ የምወደውን፡ልጄን፡ በእግዚአብሔር፡ ዘንድ፡ የታመነውን።መንገዴን፡የሚገልጥላችሁ፡በክርስቶስ፡የሱስ፡ እንደስተምር፡በየስፍራው፡ በየቤተ፡ ክርስቲያኑም፡ ሁሉ።

፲፰፡ ከላንትም፡ ተከፍለው፡ ኰርትዋል፡ ወደላንት፡ እንደልመጣ፡ ሁሉ።

፲፱፡ ነገር፡ግን፡ፈጥኜ፡ወደላንት፡ እመጣለሁ፡ *እግዚአብሔር፡ቢፈቅደው፡ኵሮችንም፡አውቃቸዋለሁ፡ ነገራቸውንም፡ አይደለም፡ ኃይላቸውን፡ እንጂ።
*የሐዋ፡ ፲፰፡ ፳፩፡፡ ያዕ፡ ፬፡ ፲፭፡፡

፳፡ የእግዚአብሔር፡ መንግሥት፡ በነገር፡ አይደለምና፡ በኃይል፡ እንጂ። ምዕ፡ ፪፡ ፬፡፡ ሉቃ፡ ፲፯፡ ፳፡፡

፳፩፡ ምን፡ትሻላችሁ። በበትርን፡ ልምጣባችሁ፡ ወይስ፡በፍቅርና፡ በየውሃት፡ መንፈስ።

ምዕራፍ፡ ፭፡

፩፡ ፈጽሞ፡ ይሰማባችኋል፡ ዝሙት፡ እንደለባችሁ፡እንደርሱ፡ ያለም፡ ዝሙት፡ አልተሰማም፡ በአሕዛብ፡ስንኳ። ማንም፡*ያባቱን፡ ምሽት፡ ያገባ፡ ዘንድ።
*ዘሌዋ፡ ፲፰፡ ፯፡ ፰፡፡

፪፡ እላንትም፡ ከዚህ፡ ጋራ፡ ትጓደዳላችሁ፡ አላለቀሳችሁምም፡ እንዲገባችሁ፡ መጠን። ይህነን፡ ስራ፡ የሰራ፡ ከላንት፡ ይርቅ፡ ዘንድ።

፫፡ እኔ፡ግን፡ከላንት፡ብርቅ፡በሥጋ፡ በመንፈስ፡ ከላንት፡ጋራ፡ ነኝ፡ አሁንም፡ ፈርጀለሁ፡ ከላንት፡ ጋራ፡ እንደ፡ነበርሁ፡ይህነን፡እንደሁ፡በስራ፡ላይ። ቆላ፡ ፪፡ ፭፡፡

፬፡ በጌታችን፡በየሱስ፡ክርስቶስ፡ ስም። እላንት፡ በተሰበሰባችሁ፡ጊዜ፡ መንፈሴም፡ ከጌታችን፡ ከየሱስ፡ ክርስቶስ፡ *ኃይል፡ ጋራ። *ማቴ፡ ፲፮፡ ፲፱፡፡ ፲፰፡ ፲፰፡፡
፪፡ ቆሮ፡ ፲፫፡ ፲፡፡

፭፡ እንደህ፡ያለውን፡*ለሰይጣን፡አሳልፎ፡ ለመስጠት፡ሥጋው፡እንዲጠፋ፡ነፍሱ፡ትድን፡ ዘንድ፡በጌታ፡ በየሱስ፡ ቀን። *፩፡ ጢሞ፡ ፩፡ ፳፡፡

፮፡ መጓደዳችሁ፡ መልካም፡ አይደለም። አታውቁምን፡ *ጥቂት፡ እርሾ፡ ብሆውን፡ ሁሉ፡ እንዲያመጣው። *ገላት፡ ፭፡ ፱፡፡

፯፡ አሮጌውን፡እርሾ፡ አጽሩ፡ ከላንትም፡ አውጥታችሁ፡ጣሉት። አዲስ፡ ብሆ፡እንድትሆኑ፡ እርሾ፡ እንደሌለባችሁ።ክርስቶስ፡*ፋሲካችን፡ደግሞ፡ ስለኛ፡ ታርድዋልና። *ኢሳ፡ ፶፫፡ ፯፡፡ ፩፡ ጴጥ፡ ፩፡ ፲፱፡፡

፰፡ ስለዚህም፡ *በዓል፡ እናድርግ፡ ባሮጌ፡ እርሾ፡ አይደለም፡ በክፋትም፡ በኃጢአትም፡ እርሾ፡ አይደለም። ነገር፡ ግን፡ በየውሃትና፡ በጽድቅ፡ ቂጣ።
*ዘፀአ፡ ፲፪፡ ፫፡ ፲፭፡ ፲፱፡፡

፱፡ በመልእክት፡ ጻፍሁላችሁ፡ ከዘማዊ፡ ሰዎች፡ጋራ፡እንዳትገናኙ።

፲፡ ከዚህ፡ ዓለምስ፡ ዘማዊ፡ ሰዎች፡ አይደለውም። ከንቢተኞችም፡ ከተናጣቅያንም፡ ጣዖትንም፡ ከሚያመልኩ፡ ጋራ። ያለዚያስ፡ ይገባችኋል፡ ከዓለም፡ ትወጡ፡ ዘንድ። ገላት፡ ፭፡ ፲፱፡፡

፲፩፡ አሁን፡ግን፡ጻፍሁላችሁ፡ እንዳትገናኙ፡አንድ፡ ሰውም፡ቢኖር፡ለላንት፡ወንድም፡የሚባል፡እርሱም፡ ዝማዊ፡ ቢሆን፡ ዓመፀኛም፡ ጣዖትም፡ የሚያመልክ። ተሳዳቢም፡ቢሆን፡ ሰካርም፡ ቢሆን፡ ተናጣቂም፡ ቢሆን። እንደህ፡ያለውን፡ወዳጅ፡አታድርጉት፡ከርሱም፡ጋራ፡አትብሉ። ቲቶ፡ ፫፡ ፫፡፡

፲፪፡ ምን፡ አግደኝ፡ በሚደ፡ ሰዎች፡ ደግሞ፡ መፍረዴ። በውሥጡ፡ ሰዎች፡ እላንት፡የምትፈርዱ፡ አይደላችሁምን። ምዕ፡ ፲፡ ፳፫፡፡

፲፫፡ የሚደ፡ሰዎችን፡ግን፡ እግዚአብሔር፡ ይፈርድባቸዋል። *ክፉውንም፡ ከመካከላችሁ፡ አስነሥታችሁ፡ጣሉት። ዘዳግ፡ ፲፫፡ ፭፡፡

ምዕራፍ፡ ፮፡

፩፡ ደግሞስ፡ ይደፍራልን፡ ከላንት፡ አንዱ፡ ከባልንጀራው፡ጋራ፡ክርክር፡ቢኖረው፡ይፋረደው፡ዘንድ፡በኃጢአተኞች፡ፊት፡ በቅዱሳንም፡ፊት፡ አይደለም።

፪፡ አታውቁምን፡ *ቅዱሳን፡ በዓለም፡ እንዲፈርዱ።ዓለሙስ፡ በላንት፡ ከተፈረደ፡ እላንት፡ አይገባችሁምን፡ በዚህ፡ በታናሹ፡ ነገር፡ ትፈርዱ፡ ዘንድ።
*ራእ፡ ፫፡ ፳፩፡፡ ዳን፡ ፯፡ ፳፪፡፡

፫፡ ወይስ፡አታውቁምን፡እኛ፡በመላእክት፡ እንድንፈርድ። እንደትስ፡ ይገባ፡ በዚህ፡ ዓለም፡ ነገር፡መፍረድ።

፬፡ ነገር፡ ግን፡ ጽል፡ ቢኖርባችሁ፡ በላንት፡ መካከል፡

ስለዚህ፡ዓለም፡ነገር፡በቤተ፡ክርስቲያን፡የተዋረዱት
ን፡ ለፍርድ፡ አስቀምጥዋቸው።
፭፡ ይህነንም፡ማለቴ፡ስዘልፋችሁ፡ነኝ።እንዲህን፡
አዋቂ፡የለባችሁም፡አንድም፡ ስንኳ፡ በወንድሙና፡
በወንድሙ፡ መካከል፡ መፍረድ፡ የሚችል።
፮፡ ወንድም፡ወንድሙን፡ይፈረዳል፡ይህም፡ በማ
ያምኑት፡ ፊት።
፯፡ ይህም፡እንዲያው፡ በላንተ፡ፈጽሞ፡ ግድፈት፡
ነው፡ እርሱ፡ በርሳችሁ፡ መፈረዳችሁ። ምነውስ፡ አት
በደሉ። ምነውስ፡ አትጐሰቍሉ። ማቴ፡ ፭፡ ፴፱።
፩፡ ተሰ፡ ፭፡ ፲፭። ፩፡ ጴጥ፡ ፫፡ ፱።
፰፡ ነገር፡ ግን፡ እላንተ ፡ ትበድላላችሁ፡ ታጐሰቍሉ
ማላችሁ፡ ወንድሞቻችሁንም፡ ደግሞ።
፱፡ ወይስ፡ አታውቁምን፡ ግፈኞች፡ የእግዚአብሔ
ርን፡ መንግሥት፡ እንዲይወርሱ። አትሳቱ። ዘማዊ፡ሰ
ዎች፡ጣዖትም፡ የሚያመልኩ፡አመንዝሮችም፡ ቀላ
ጮችም፡ከወንድ፡ጋራ፡ የሚተኙም።
፲፡ ሌቦችም፡ ሰስታሞችም፡ ሰካሮችም፡ ተሳዳቦች
ም፡ ነጣቆችም፡ የእግዚአብሔርን፡ መንግሥት፡ አይ
ወርሰዋትም። ገላት፡ ፭፡ ፲፱፡—፳፩።
፲፩፡ እንዲህም፡*ያሉ፡ከላንተ፡ነበሩ። ግን፡ ተታጠባ
ችሁ፡ግን፡ ተቀደሳችሁ፡ ግን፡ ተጸደቃችሁ፡ በጌታችን፡
በየሱስ፡ክርስቶስ፡ስም፡ባምላካችንም፡መንፈስ።
*ቲጦ፡ ፫፡ ፫። †ዕብ፡ ፱፡ ፲፬።
፲፪፡ ነገር፡ሁሉ፡ ለኔ፡ተፈቶልኛል። ነገር፡ግን፡ ሁሉ፡ አ
ይረባም። ሁሉ፡ ተፈቶልኛል፡ነገር፡ ግን፡ ማንም፡ ይገዛ
ኝ፡ ዘንድ፡ አልተውም። ም፡ ፲፡ ፳፫።
፲፫፡ መብል፡ለሆድ፡ነው፡ሆድም፡ለመብል። እግዚ
አብሔር፡ ግን፡ ይህነን፡ ያነንም፡ያጠፋል። *ሥጋ፡ ግን፡
ለዝሙት፡አይደለም፡ለጌታ፡ እንጂ፡ጌታም፡ ለሥጋ።
*፩፡ ተሰ፡ ፬፡ ፫፡—፭።
፲፬፡ እግዚአብሔርም ፡ ጌታችነን ፡ አስነሣው ፡ እር
ሱም፡ እኛን፡ ደግሞ፡ ያስነሣናል፡ በችሎቱ።
ም፡ ፲፭፡ ፲፭፡ ፳።
፲፭፡ ወይስ፡ አታውቁምን ፡ ሥጋችሁ ፡ የክርስቶስ፡
ብልቶች፡ እንደሆነ። የክርስቶስንም፡ ብልቶች፡ ወስጄ
ን፡ለጋለሞታ፡ብልቶች፡ አደርገዋለሁ። አይገባም።
ም፡ ፲፪፡ ፳፯።
፲፮፡ አታውቁምን፡ከጋለሞታ፡ጋራ፡ የተገናኘ፡ ከር
ስዋ፡ጋራ፡ *አንድ፡ሥጋ፡እንዲሆን። ተብልዋልና፡ ሁለ
ቱ፡ አንድ፡ ሥጋ፡ ይሆኑ። *ዘፍ፡ ፪፡ ፳፬።
፲፯፡ ከእግዚአብሔር፡ ጋራ፡ ግን፡ የተገናኘ፡ አንድ፡
መንፈስ፡ይሆናል። ዮሐ፡ ፲፯፡ ፳፩፡ ፳፪። ኤፌ፡ ፭፡ ፴።
፲፰፡ ከዝሙት፡ሽሹ። ሰው፡የሚያደርገው፡ኀጢአ
ት፡ሁሉ፡ከሰውነቱ፡በሚደ፡ነው። የሚያዝም፡ግን፡እ
ርሱ፡ በሰውነቱ፡ ላይ፡ ኀጢአት፡ይሰራል።
፲፱፡ ወይስ፡አታውቁምን፡ሥጋችሁ፡ በላንተ፡ የሚ
ያድረው፡የመንፈስ፡ቅዱስ፡መቅደስ፡እንደ፡ሆነ፡ከእ
ግዚአብሔር፡ የተቀበላችሁት። ለራሳችሁም፡ አይደ
ላችሁም። ም፡ ፫፡ ፲፮።
፳፡ *በዋጋ፡ ተገዝታችኋልና። እንግዲህም፡ እግዚ
አብሔርን፡†አክብሩ፡በሥጋችሁና፡ በመንፈሳችሁ፡እ
ሌህም፡ ለእግዚአብሔር ፡ የሆኑት። *ም፡ ፯፡ ፳፫።
፩፡ ጴጥ፡ ፩፡ ፲፰፡ ፲፱። †ፊል፡ ፩፡ ፳።

ምዕራፍ፡ ፯፡

፩፡ ስለ፡ጻፋችሁልኝ፡ ግን፡ለሰው፡ሴት፡ ባይነካ፡ መ
ልካም፡ነው።
፪፡ ነገር፡ግን፡ስለ፡ዝሙት፡ሁሉ፡ኢያንዳንዱ፡ ምሽ
ቱ፡ትሁንለት። ለሴቲቱም፡ባልዋ፡ይሁንላት።
፫፡ ወንድ፡ለሴቲቱ፡ የሚገባትን፡ ፍቅር፡ ይፈጽም
ላት። እንደሁም፡ ሴቲቱ፡ ለወንዱ።
፬፡ ሴቲቱ፡ በሥጋዋ፡ ለራስዋ፡ ሥልጣን፡ ታጣለች፡
ወንዱ፡እንጂ። እንደሁም፡ደግሞ፡ወንዱ፡በሥጋው፡
ሥልጣን፡ ያጣል፡ ነገር፡ ግን፡ ምሽቱ።
፭፡ ይህነን፡ እርሱ፡ በርሳችሁ፡እምቢ፡ አትበሉ። ከ
ምትጸሙበትና፡ከምትጸልዩበት፡ ጊዜ፡ በቀር፡ባንድ፡
በተስማማችሁ፡ጊዜ። ደግሞም፡ ባንድነት፡ ተገናኙ።
ሰይጣን፡እንዲይፈታናችሁ፡ ስለ፡ ፍትወታችሁን፡አለ
መግዛት።
፮፡ ይህነንም፡ማለቴ፡ ምረዳችሁ፡ ነኝ፡ የማዛችሁ
ም፡አይደለም።
፯፡ እወዳለሁና ፡ ሰዎች፡ ሁሉ፡ እንደኔ፡ ይሆኑ፡ ዘን
ድ። ነገር፡ግን፡ለሁሉ፡ኢያንዳንዱ፡ እግዚአብሔር፡ እ
ንደ፡ከፈለው፡ጸጋው፡ነው። ላንዱ፡እንደህ፡ ለሌላው
ም፡እንዲያ። ማቴ፡ ፲፱፡ ፲፪።
፰፡ ላላገቡም፡እላለሁ፡ለባልቴቶችም፡ መልካም፡
እንደ፡ ሆነ፡ ይኖሩ፡ ዘንድ፡እንደኔ።
፱፡ ራሳቸውን፡ግን፡ መጠበቅ፡ባይችሉ፡ ያግቡ። ማ
ግባት፡ከመቃጠል፡ ይሻላልና። ፩፡ ጢሞ፡ ፭፡ ፲፬።
፲፡ የተጋቡትን፡ ግን፡ አዛቸዋለሁ ፡ እኔ ፡ አይደለሁ
ም፡ *ጌታ፡ እንጂ። †ሴት፡ ባልዋን፡ እንዳትፈታ።
*ቍ፡ ፳፭፡ ፵። †ማቴ፡ ፭፡ ፴፪።
፲፩፡ ብትፈታውም፡ሳታገባ፡ትቀመጥ፡ወይም፡ከባ
ልዋ፡ ጋራ፡ ትታረቅ። ወንዱም ፡ ምሽቱን፡ አይተው።
፲፪፡ ለቀሩትም፡ እኔ፡ እላለሁ፡ ጌታ ፡ አይደለም።
ማናቸውም ፡ ወንድም ፡ ምሽት፡ ብትኖረው፡ የማታ
ምን፡እርስዋም፡ ብትወድ፡ ከርሱ፡ጋራ፡ መቀመጥ፡ አ
ይስደዳት።
፲፫፡ ማናቸዪቱም ፡ ሴት፡ ባል ፡ ቢኖራት ፡ የማያም
ን ፡ እርሱም ፡ ቢሻ፡ ከርስዋ፡ ጋራ፡ መቀመጥ፡ አትስደ
ደው።
፲፬፡ የማያምን፡ ወንድ፡ በምታምን፡ ምሽት፡ ይቀ
ደሳልና፡ የማታምንም፡ ምሽት፡ በሚያምን ፡ ወንድ፡
ትቀደሳለችና። ያለዚያም፡ ልጆቻችሁ፡ ርኩሳን፡ ናቸ
ው፡ዛሬ፡ግን፡ *የተቀደሱ፡ናቸው። *ሮሚ፡ ፲፩፡ ፲፮።
፲፭፡ ያላመነው፡ግን፡ቢለይ፡ይለይ። ወንድም፡አት

ም፡ለንደዚህ፡ላለው፡አይገዙም። እግዚአብሔር፡ለሰላም፡ጸርቶናልና። ሮሜ፡ ፲፬፡ ፲፱።

፲፮፡ ምን፡ታውቂያለሽ፡ አንቺ፡ ሴት፡ ባልሽን፡ ታድኝ፡ እንደሆንሽ። አንተስ፡ ምን፡ ታውቃለህ፡ አንተ፡ ሰው፡ምሽትህን፡ታድን፡እንደ፡ሆንህ። ፩፡ ጴጥ፡ ፫፡ ፩።

፲፯፡ ነገር፡ ግን፡ እንዴህ፡ ነው፡ እግዚአብሔር፡ ለሁሉ፡*ኢያንዳንዱ፡እንደ፡ ከፈለው። ሁሉም፡ እግዚአብሔር፡እንደ፡ጸራው፡እንዴሁ፡ይሒድ።እንዴሁም፡ቤተ፡ክርስቲያኑን፡ሁሉ፡አሠራለሁ። *ቍ፡ ፳፡ ፳፬።

፲፰፡ ማንም፡ተገዝሮ፡ሳለ፡የተጸራ፡ ቢኖር፡ወደ፡ቍላፍነት፡ አይመለስ ። ማንም፡ ሳይገዝር፡ የተጸራ፡ ቢኖር፡ መገዘር፡ አይሻ።

፲፱፡ ግዝረት፡ ዝም፡ ብሎ፡ ነው፡ አለመገዘርም፡ ዝም፡ብሎ፡ነው፡ ነገር፡ግን፡ የእግዚአብሔርን፡ ትእዛዝ፡ መጠበቅ፡ ነው። ገላት፡ ፭፡ ፮። ፮፡ ፲፭።

፳፡ ሁሉ፡ኢያንዳንዱ፡በዚያው፡ በተጸራበቱ፡ነገር፡ ይቀመጥ። ቍ፡ ፲፯፡ ፳፬።

፳፩፡ አንተም፡ብትጸራ፡ባርያ፡ ሁነህ፡አትዘን። አርነት፡ መውጣት፡ ግን፡ ቢቻልህ፡ አርነት፡ብታደርግ፡ ይሻላል።

፳፪፡ ባርያ፡በእግዚአብሔር፡ ቢጸራ፡ እርሱ፡ ለእግዚአብሔር፡*ከባርነት፡ የወጣ፡ ነውና። እንዴሁም፡ ጌታ፡ የተጸራ፡ እንደሆን፡ እርሱ፡ †ባርያ ፡ ነው፡ ለክርስቶስ። *ዮሐ፡ ፰፡ ፴፮። †ኤፌ፡ ፮፡ ፮።

፳፫፡ *በዋጋ፡ ተገዝታችኋልና ። ለሰው፡ ባሮች፡ አትሁኑ። *ም፡ ፮፡ ፳። ፩፡ ጴጥ፡ ፩፡ ፲፰፡ ፲፱።

፳፬፡ ሁሉ፡ኢያንዳንዱ፡ወንድሞቼ፡ሆይ፡በተጸራበት፡ይቀመጥ፡በእግዚአብሔር፡ዘንድ። ቍ፡ ፲፯፡ ፳።

፳፭፡ ስለ፡ ደናግል፡ ግን፡ ከጌታ፡ አልታዘዝሁም፡ ነገር፡ ግን፡ እመክራችኋለሁ፡ *ይቅር ፡ ተብያለሁና፡ ከእግዚአብሔር፡ ዘንድ፡ የታመንሁ፡ እንድሆን። ቍ፡ ፲፡ ፵። *፩፡ ጢሞ፡ ፩፡ ፲፪፡ ፲፫።

፳፮፡ አሁንም፡ይህ፡መልካም፡ ይመስለኛል፡ ስለ፡ ዘመኑ፡ ጭንቀት። በሰውም፡ ያምርበት፡ እንዴህ፡ ቢሆን። ቍ፡ ፳፱። ም፡ ፲፡ ፲፩።

፳፯፡ በምሽት ፡ ታሥረህ፡ እንደ፡ ሆንህ፡ ከርስዋ፡ መለየት፡አትሻ። ያለ፡ምሽት፡ እንደ፡ ሆንህ፡ ምሽት፡ አትፈልግ።

፳፰፡ ደግሞም፡ማግባት።ብትሻ፡ኃጢአት፡አልሰራህም።ድንግልም፡ብታገባ፡ኃጢአት፡አይደለም።ነገር፡ግን፡ለሥጋ፡ መከራ፡ነው፡ እንዴህ፡ላሉት፡ እኔ፡ግን፡አዝንላችኋለሁ።

፳፱፡ ይህነንም ፡ እላችኋለሁ ፡ ወንድሞቼ፡ ሆይ። *ዘመኑ፡ያጠረ፡እንደሆነ። ምሽት፡ ያለችው፡ ምሽት፡ †እንደሌለው፡ ይሆን፡ዘንድ። *ሮሜ፡ ፲፫፡ ፲፩። †ሉቃ፡ ፲፬፡ ፳፮።

፴፡ የሚያለቅሱም፡እንደማያለቅሱ። ደስ፡የሚላቸውም፡ ደስ፡ እንደማይላቸው። የሚገዙም፡ እንደልገዙ።

፴፩፡ በዚህ፡ ዓለምም ፡ ተግባራቸውን ፡ የሚፈጽሙ፡ ለሥጋ፡ ፈቃድ፡ እንደማይፈጽሙት። *የዚህ፡ዓለም፡ መልክ፡ ያልፋልና። *፩፡ ዮሐ፡ ፪፡ ፲፭—፲፯።

፴፪፡ እኔም፡እወዳለሁ፡ያላሳብ፡ትኖሩ፡ዘንድ። ምሽት፡ የሌለው፡ የጌታውን፡ ነገር፡ያስባል፡ ጌታውን፡ ደስ፡ያሰኝ፡ዘንድ።

፴፫፡ ምሽት፡ያለችው፡ግን፡የዚህን፡*ዓለም፡ ነገር፡ ያስባል፡ምሽቱን፡ደስ፡ ያሰኝ፡ ዘንድ። *ሉቃ፡ ፲፬፡ ፳።

፴፬፡ በተጋባች፡ሴትና፡በድንግልና፡ ባለችው፡ መካከል፡ነገር፡ተለየ።ያላገባች፡ የእግዚአብሔርን፡ነገር፡ታስባለችና፡ ንጽሕት፡ ትሆን ፡ ዘንድ፡ በሥጋዋና፡ በነፍስዋ ። የተጋባች፡ ግን፡ የዓለምን፡ ነገር፡ ታስባለች፡ ባልዋን፡ደስ፡ታሰኝ፡ ዘንድ።

፴፭፡ ይህነንም ፡ ማለቴ፡ እንዲጠቅማችሁ፡ ነው፡ ላጸምደችሁም፡ ብዬ፡ አይደለም ። ነገር፡ግን፡ በመልካም፡ ትኖሩ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔርንም ፡ ጸንታችሁ፡ ያላሳብ፡ ታገለግሉ፡ ዘንድ፡ ነው።

፴፮፡ ማንም፡የሚሰደብ፡ ቢመስለው፡ በድንግሉ፡ የመጋባት፡ ዘመን፡ በደረሰ፡ ጊዜ። እንዴሁም፡ ይሆን፡ ዘንድ፡ቢገባ። የወደደውን፡ ያድርግ፡ ኃጢአትም፡ የለበትም። ያግቡ።

፴፯፡ የጸና፡ግን፡በልቡ፡ግድም፡ የሌለው፡ነገር፡ ግን፡ በገዛ፡ ፈቃድ፡ ችሎት፡ያለው፡ ያህነንም፡ በልቡ፡ የመረጠው፡ድንግሉን፡ከርሱ፡ ጋራ፡ ያለችውን፡ ይጠብቅ፡ ዘንድ፡ እርሱ፡ መልካም፡ አደረገ።

፴፰፡ እንጊዴህም፡ ድንግሉን ፡ ለመጋባት፡ የሰጠ፡ መልካም፡ አደረገ ። ድንግሉንም ፡ ለመጋባት ፡ ያልሰጠ፡ ከመልካም፡ የሚሻል፡ አደረገ።

፴፱፡ *ሴት፡በባልዋ፡ሕግ፡ የታሠረች፡ ናት፡ ባለበት፡ ዘመን፡ሁሉ። ባልዋ፡ ግን፡ ከሞተ፡ በኋላ፡ ተፈታች፡ የምትወደውንም ፡ ታግባ። ነገር፡ ግን፡ በጌታችን። *ሮሜ ፡ ፯፡ ፪።

፵፡ እንዴህ፡ግን፡ብትኖር፡ እርስዋ፡ እንደ፡ ምክሬ፡ አብዝቶ፡ ደስ፡ ይላታል ። የእግዚአብሔር፡ መንፈስ፡ ደግሞ፡በኔ፡ያለ፡ ይመስለኛል። ቍ፡ ፳፭።

## ምዕራፍ፡ ፰

፩፡ *ለጣዖታት፡ ስለ፡ ታረደው፡ ግን፡ ፈጽመን፡ እናውቃለን፡ እውቀትዋ፡ ከኛ፡ከሁላችን፡ ዘንድ፡ እንደ፡ሆነ፡ እውቀትም፡ ያኰራል፡ ፍቅር፡ ግን፡ ይሠራል። *የሐዋ፡ ፲፭፡ ፳።

፪፡ አውቃለሁም፡ የሚል፡ *እንደችም፡ገና፡ የሚገባውን፡አያውቅም። *ገላት፡ ፮፡ ፫። ፩፡ ጢሞ፡ ፮፡ ፬።

፫፡ እግዚአብሔርን፡ግን፡የሚወድ፡ እርሱ፡ *የታወቀ፡ ነው፡ በርሱ፡ዘንድ። *ገላት፡ ፬፡ ፱።

፬፡ ለጣዖታት፡ የታረዱትን፡ግና፡ስለ፡ መብላት፡ እናውቃለን፡ጣዖት፡ ምንምን፡ እንደይደለ፡ በዓለም። ሌላም፡አምላክ፡እንደሌለ፡ ካንዴ፡ በቀር። ም፡ ፲፡ ፲፱።

፭፡ ማንም፡ *አምላክ፡ተብሎ፡ ቢጸራ፡ በሰማይ፡በምድርም፡ያለው።ብዙ፡አማልክት፡እንደ፡ሆኑ፡ብዙም፡ ጌቶች። *ዮሐ፡ ፲፡ ፴፬፡፡

፮፡ ለኛ፡ግን፡ አንድ፡ አምላክ፡ አለን፡ እግዚአብሔር፡አብ። ሁሉ፡ ከርሱ፡ የሆነ፡ እኛም፡ለርሱ፡ አንድም፡ ነው፡ ጌታ፡ የሱስ፡ ክርስቶስ ። ሁሉ፡ በርሱ፡ የሆነ፡ እኛም፡ በርሱ። መልክ፡ ፪፡ ፲፡፡ ቆላ፡ ፩፡ ፲፮፡፡

፯፡ ነገር፡ግን፡ያነን፡ ማወቅ፡ ለሁሉ፡ አይደለም። ሰዎችም፡ ከላንት፡ለጣዖት፡ የታረደ፡ እንደ፡ሆነ፡ ቢያስቡ፡ለጣዖት፡እንደሚታረደው፡ይበላሉ፡እስከ፡ ዛሬ። ደካማውም፡ አኅባቸው፡ ይረክሳል። ም፡ ፲፡ ፳፰፡፡

፰፡ ነገር፡ግን፡መብል፡ወደ፡ እግዚአብሔር፡ አያደርሰነም። ብንበላ፡አንጨምርምና፡ ባንበላም፡ አንጐድልም። ሮሜ፡ ፲፬፡ ፲፯፡፡

፱፡ እላንት፡ግን፡እዩ፡ይህ፡ ችሎታችሁ፡የደካሞች፡ እንቅፋት፡ እንዳይሆን። ገላት፡ ፭፡ ፲፫፡፡

፲፡ ማንም ፡ አንተን፡ ቢያይህ ፡ አዋቂውን ፡ በጣዖት፡ ቤት፡ ለመብል፡ ተቀምጠህ። እርሱ፡ በደካማ፡ ልብ፡ ለጣዖት፡ የታረደውን ፡ ይበላ፡ ዘንድ፡ ይደፍራል።

፲፩፡ ያውም፡ ደካማው ፡ ወንድም ፡ *በውቀትህ፡ ይጠፋል። ክርስቶስ፡ ስለርሱ፡ የሞተለቱ። *ሮሜ፡ ፲፬፡ ፲፭፡፡

፲፪፡ እንደህስ ፡ ወንድሞችን ፡ ከበደላችሁ፡ የደከመውንም፡ ልባቸውን፡ ከሰበራችሁ ፡ ክርስቶስን፡ በደላችሁ።

፲፫፡ ስለዚህም፡*መብል ፡ ወንድሜን፡ ቢያሰናክለው፡ሥጋ፡ አልበላም፡ ለዘላለም፡ ወንድሜን፡ እንዳላሰናክለው። *ሮሜ፡ ፲፬፡ ፳፩፡፡

ምዕራፍ፡ ፱፡

፩፡ እኔ፡ሐዋርያ፡አይደለሁምን።ወይስ፡ጌታ፡ አይደለሁምን። የሱስ፡ ክርስቶስንስ፡ ጌታችነን፡ ያየሁ፡ አይደለሁምን። እላንትስ፡ በጌታ፡ ስራዬ፡ አይደላችሁምን። ም፡ ፲፭፡ ፰፡፡ የሐዋ፡ ፳፮፡ ፲፮፡፡ ፳፪፡ ፲፯፡፡

፪፡ ለሌሎችም፡ ሐዋርያ፡ ባልሆን፡ ነገር፡ ግን፡ ለላንት፡ሐዋርያ፡ነኝ። የመልእክቴ፡ማኅተም፡ በጌታ፡ እላንት፡ናችሁና። ፪፡ ቆሮ፡ ፫፡ ፪፡ ፫፡፡

፫፡ ለሚመረምሩኝ፡ ምላሼ፡ ይህ፡ ነው።

፬፡ አይገባነምን፡ እንበላ፡ እንጠጣም፡ ዘንድ። ሉቃ፡ ፲፡ ፰፡፡

፭፡ ወይስ፡አይገባነምን ፡ ምሽት ፡ እታችን፡ ከኛ፡ ጋራ፡ ትዞር፡ ዘንድ ። እንደ፡ ሌሎች፡ ሐዋርያት፡ እንደ፡ ጌታም፡ወንድሞች፡እንደ፡ኬፋም። ዮሐ፡ ፩፡ ፵፪፡፡

፮፡ ወይስ፡ እኔና፡ በርናባስ፡ ብቻን፡ አይገባነም፡ ማድረግ፡እንተው፡ ዘንድ።

፯፡ ማነው፡ ከተ፡ገንዘቡን፡ ኢየበላ፡ ወታደር፡ የሚሆን ። ማነው፡ ወይን፡ ተክሎ፡ ፍሬውን ፡ የማይበላ። ወይስ፡ ማነው፡ መንጋ፡ የሚጠብቅ፡ከመንጋውስ፡ ወተት፡ የማይጠጣ።

፰፡ ይህንም፡ነገር፡እንደ፡ሰውን፡እናገራለሁ። ወይስ፡ኦሪት፡ ደግሞ፡ ይህነን፡ አትልምን።

፱፡ በሙሴ፡ ኦሪት ፡ *ተጽፏዋልና ። የሚያሔድን፡ በሬ፡ አፏን፡ አትዝጋ ። ወይስ፡ እግዚአብሔር፡ ለበሬን፡ ያስባል። *ዘዳግ፡ ፳፭፡ ፬፡፡ ፩፡ ጢሞ፡ ፭፡ ፲፰፡፡

፲፡ ወይስ፡ስለኛ፡ ይህነን፡ ነገር፡ ፈጽሞ፡ ይላልን። ስለኛ፡ተጽፏዋልና። ገባሬ፡ በተስፋ፡ ያርስ፡ዘንድ፡ይገባዋልና፡ የሚያሔድም፡ እርሱ፡ ደግሞ፡ በተስፋ፡ያሔድ፡ዘንድ።

፲፩፡ መንፈሳዊ፡ ነገርስ፡ የዘራነባችሁ፡ ከሆነ፡ እጅግን፡ታላቅ፡ነው፡ከላንት፡ የሥጋዊን፡ ነገር፡ ብናጭድ። ሮሜ፡ ፲፭፡ ፳፯፡፡

፲፪፡ ሌሎች፡ሰዎችም፡ይህነን፡ ሥልጣን፡ ካደረጉባችሁ፡እንዴትስ፡ ይልቅ፡እኛ። *ነገር፡ግን፡ ይህነን፡ ሥልጣን፡ አላደረግነም። ሁሉን፡ እንታገሣለን ፡ እንጂ፡ የክርስቶስን፡ወንጌል፡ በማናቸውም፡ እንዳናሰናክል። *የሐዋ፡ ፳፡ ፴፫፡፡ ፪፡ ቆሮ፡ ፲፩፡ ፱፡፡

፲፫፡ አታውቁምን ፡ የመቅደስን ፡ ስራ ፡ የሚሰሩ፡ *ከመቅደስ፡ እንዲበሉ። ለመሠዊያም፡ የሚያገለግሉ፡መሥዋዕቱን፡ይካፈላሉ። *ዘኁል፡ ፲፰፡ ፰፡ ፴፩፡፡ ዘዳግ፡ ፲፰፡ ፩፡—፫፡፡

፲፬፡ እንዲሁም፡ ጌታችን፡ ሠራ፡ ወንጌልን፡ የሚያስተምሩ፡ በወንጌል፡እንዲመገቡ። ሉቃ፡ ፲፡ ፯፡፡

፲፭፡ እኔ፡*ግን፡ከዚህ፡ምንም፡አላደረግሁም፡ በዚህም፡ አልጸፍሁም፡ ይህ፡ ለኔ፡ ይሆንልኝ፡ ዘንድ ። ብሞትም፡ ይሻለኛል፡ ማንም፡ ትምክህቴን ፡ ኪያበላሸው። *የሐዋ፡ ፲፰፡ ፫፡፡

፲፮፡ ወንጌልን ፡ ከማስትማሬ ፡ ግን ፡ አልመካበትም፡ያው፡በግድ፡ ወድቀብኛልና። ባላስተምርም፡ *ወዮልኝ። *ኤር፡ ፳፡ ፱፡፡

፲፯፡ ይህነንስ፡ በፈቃዴ፡ አድርጌው ፡ እንደሆን፡ ዋጋ፡ አለኝ ። ያለ፡ ፈቃዴ፡ ግን፡ ከሆነ ፡ እኔ፡ ለማገልገል፡ ታምኛለሁ። ም፡ ፬፡ ፩፡፡

፲፰፡ እንጊዴህ፡ ዋጋዬ፡ ምንድር፡ ነው። የክርስቶስን፡ ወንጌል ፡ ባስተምር፡ እንደች ፡ ሳልቀበል። በወንጌል፡ የተሰጠችልኝን ፡ *ሥልጣን፡ ወደ፡ ክፋት፡ እንዳልመልስ። *ም፡ ፰፡ ፱፡

፲፱፡ ነገር፡ግን፡እኔ፡ ከሰው፡ ሁሉ፡ አርነት፡ የወጣሁ፡ ስሆን፡ራሴን፡ለሁሉ፡ አስገዛሁ፡ ሁሉን፡እረባ፡ ዘንድ። ማቴ፡ ፳፡ ፳፯፡—፳፰፡፡

፳፡ ከአይሁድም፡ ጋራ፡ እንደ፡ አይሁዳዊ፡ ሆንሁ፡ አይሁድን፡ እረባ፡ ዘንድ ። ከኦሪት፡ በታች፡ ካሉት፡ጋራ፡ከኦሪት፡በታች፡እንደ፡ሆንሁ፡ከኦሪት፡ በታች፡ ያሉትን፡ እረባ፡ ዘንድ። የሐዋ፡ ፲፮፡ ፫፡፡

፳፩፡ ሕግ፡ ከሌላቸው፡ ጋራ፡ ሕግ ፡ እንደሌላቸው፡ *ሆንሁ። በእግዚአብሔርም ፡ ዘንድ፡ ያለ፡ ሕግ፡ አይደለሁም፡ በክርስቶስ፡ ሕግ፡ አለሁ፡ እንጂ፡ ሕግ፡ የሌላቸውን፡ እረባ፡ ዘንድ። *ገላት፡ ፪፡ ፫፡፡

፳፪፡ ከደካሞች፡ ጋራ፡ እንደ፡ ደካማ፡ ሆንሁ፡ ደካ

ሞችን፡ እረባ፡ ዘንድ። ከሁሉ፡ ጋራ፡ እንደርሳቸው፡ ሆንሁ፡ ከርሳቸው፡ ሰዎች፡ ፈጽሚ፡ አድን፡ ዘንድ።
* ፪፡ ቆሮ፡ ፲፩፡ ፳፱። ሮሜ፡ ፲፩፡ ፲፬።

፳፫፡ ይህንም፡ ስለ፡ ወንጌል፡ አደርገዋለሁ፡ ከርሱ፡ ጋራ፡ አንድነት፡ ይሆንልኝ፡ ዘንድ።

፳፬፡ አታውቁምን፡ ሩጫ፡ ወደለበት፡ ስፍራ፡ የሚቀደደሙ፡ ሁሉ፡ እንዲሮጡ። ደመወዜን፡ ግን፡ አንዱ፡ ከርሳቸው፡ ያገኛል። እላንተም፡ እንዲሁ፡ ሩጡ፡ እንድታገኙት። ፪፡ ጢሞ፡ ፪፡ ፬፡ ፯።

፳፭፡ የሚጋደልም፡ ሁሉ፡ *ነገርን፡ ሁሉ፡ ይተዋል። እሌህም፡ የሚጠፋውን፡ አክሊል፡ ይወስዱ፡ ዘንድ፡ ነው፡ እኛ፡ ግን፡ †የማይጠፋውን።
*፪፡ ጢሞ፡ ፪፡ ፬፡ ፭። †፩፡ ጴጥ፡ ፭፡ ፬።

፳፮፡ እንግዲህ፡ እኔ፡ እንዲሁ፡ እሮጣለሁ፡ ላልታወቀ፡ ነገር፡ እንደሚሮጥ፡ እንደልሆን። እንዲሁም፡ እጋደላለሁ፡ ነፋስን፡ እንደሚጋደል፡ እንደልሆን።

፳፯፡ ነገር፡ ግን፡ ሥጋዬን፡ እጥብቄ፡ *እቀጣዋለሁ፡ አስገዛውማለሁ፡ ሌሎችን፡ አስተምሬ፡ እኔ፡ ለራሴ፡ የተጣልሁ፡ እንደልሆን። *ሮሜ፡ ፰፡ ፲፫። ፲፫፡ ፲፬።

## ምዕራፍ፡ ፲፤

፩፡ እኔም፡ እወዳለሁ፡ ታውቁ፡ ዘንድ፡ ወንድሞቼ፡ ሆይ፡ *አባቶቻችን፡ ሁሉ፡ †ከደመና፡ በታች፡ እንደ፡ ነበሩ፡ ሁሉም፡ ባሕርን፡ ተሻገሩ። *ዘፀአ፡ ፲፫፡ ፳፩።
†በፀአ፡ ፲፬፡ ፳፪።

፪፡ ሁሉም፡ ለሙሴ፡ ተጠመቁ፡ በደመናና፡ በባሕር።

፫፡ ያንንም፡ *መንፈሳዊ፡ አንድ፡ መብል፡ ሁሉ፡ በሉ።
*ዘፀአ፡ ፲፮፡ ፲፭።

፬፡ ያንንም፡ መንፈሳዊ፡ አንድ፡ *መጠጥ፡ ሁሉ፡ ጠጡ። ከርሳቸው፡ ጋራ፡ ይከተል፡ ከነበረው፡ ከመንፈሳዊ፡ ደንጊያ፡ ጠጥተዋልና። ያም፡ ደንጊያ፡ ክርስቶስ፡ ነበረ። *ዘፀአ፡ ፲፯፡ ፮።

፭፡ እግዚአብሔር፡ ግን፡ ከርሳቸው፡ በሚበዙት፡ አልወደደም፡ በምድረ፡ በደ፡ †ወድቀዋልና።
ዘኍል፡ ፲፬፡ ፳፫—፴። †ዮሐ፡ ፮፡ ፵፱።

፮፡ ይህም፡ ለኛ፡ ምሳሌ፡ ሆነልን፡ ክፉ፡ ነገር፡ እንዳንመኝ፡ እሊያ፡ እንደ፡ ተመኙ። ዘኍል፡ ፲፩፡ ፬፡ ፴፬።

፯፡ ጣዖትም፡ የምታመልኩ፡ አትሁኑ፡ ከርሳቸው፡ ተከፍለው፡ እንደመለኩ። *እንደ፡ ተጻፈ። ሕዝብ፡ ተቀመጡ፡ ሊበሉ፡ ሊጠጡም፡ ሊዘፍኑም፡ ተነሡ።
*ዘፀአ፡ ፴፪፡ ፮።

፰፡ አናመንዝርም፡ ከርሳቸው፡ ተከፍለው፡ እንደመነዘሩ፡ ከርሳቸውም፡ ወደቁ፡ ባንድ፡ ቀን፡ ሁለት፡ እልፍ፡ ከሦስት፡ ሺህ። ዘኍል፡ ፳፭፡ ፩፡ ፱።

፱፡ ክርስቶስንም፡ አንፈታተን፡ ከርሳቸው፡ ተከፍለው፡ እንደ፡ ተፈታተኑት፡ *በእርዌም፡ ጠፉ።
ዘኍል፡ ፳፩፡ ፭፡ ፮።

፲፡ አታንጐርጕሩም፡ ከርሳቸው፡ ተከፍለው፡ እንደንጐረጐሩ፡ የሚያጠፋውም፡ አጠፋቸው።
ዘኍል፡ ፲፬፡ ፪፡ ፴፯። ዕብ፡ ፫፡ ፲፩፡ ፲፯።

፲፩፡ ይህም፡ ሁሉ፡ በለዚያ፡ ደረሰባቸው፡ ምሳሌ፡ ሁና፡ ለኛም፡ ተጻፈልነ፡ እኛን፡ ሊገሥጽን፡ የዘመኑ፡ ፍጻሜዎች፡ የደረሱብነን።

፲፪፡ *ስለዚህም፡ ቁሚያለሁ፡ የሚመስለው፡ ይጠንቀቅ፡ እንዳይወድቅ። *ሮሜ፡ ፲፩፡ ፳።

፲፫፡ ሌላ፡ ፈተና፡ አላገኛችሁም፡ እንደ፡ ሰው፡ ያለ፡ ፈተና፡ እንጂ። እግዚአብሔር፡ ግን፡ እውነተኛ፡ ነው፡ አይተዋችሁም፡ ትፈተኑ፡ ዘንድ፡ በማትችሉት። ነገር፡ ግን፡ ከፈተናችሁ፡ ጋራ፡ መውጫውን፡ ያደርግላችኋል፡ ታገሡ፡ ዘንድ፡ እንድችሉ።

፲፬፡ ስለዚህም፡ ወንድሞቼ፡ ሆይ፡ ጣዖት፡ ከማምለክ፡ ሽሹ። ፩፡ ዮሐ፡ ፭፡ ፳፩።

፲፭፡ ለጠቢባን፡ እንዲባል፡ እላችኋለሁ። እላንት፡ በሚገባላችሁ፡ ፍረዱ።

፲፮፡ *የምንባርከው፡ የበረከቱ፡ ጽዋ፡ የክርስቶስ፡ የደሙ፡ እራት፡ አይደለምን። †የምንቈርሰውስ፡ እንጀራ፡ የክርስቶስ፡ የሥጋው፡ እራት፡ አይደለውምን። *ማቴ፡ ፳፮፡ ፳፯። †የሐዋ፡ ፪፡ ፵፪።

፲፯፡ እኛም፡ ሁላችን፡ አንድ፡ እንጀራ፡ አንድ፡ ሥጋም፡ ነነ። እኛ፡ ሁላችን፡ አንድ፡ እንጀራ፡ እንቀበላለንና። ሮሜ፡ ፲፪፡ ፭። ፩፡ ቆሮ፡ ፲፪፡ ፳፯።

፲፰፡ ወደ፡ እሥራኤል፡ ተመልከቱ፡ በሥጋ። *መሥዋዕቱን፡ የሚበሉ፡ ከመሠዊያው፡ ጋራ፡ አንድነት፡ ያደርጉ፡ የለምን። *ዘሌዋ፡ ፯፡ ፮፡ ፲፭።

፲፱፡ ምን፡ እላለሁ፡ እንግዲህ። ጣዖት፡ ምናምንን፡ ነው። ወይስ፡ ለጣዖት፡ የታረደው፡ አንዳችን፡ ነው።
፩፡ ቆሮ፡ ፰፡ ፬።

፳፡ ነገር፡ ግን፡ እላለሁ፡ *አሕዛብ፡ የሚያርዱት፡ ለሰይጣናት፡ የሚሠውት፡ ነው፡ ለእግዚአብሔርም፡ አይደለውም። የሰይጣናትም፡ ተካፋዮች፡ ትሆኑ፡ ዘንድ፡ አልወድም። *ዘሌዋ፡ ፲፯፡ ፯። ዘዳግ፡ ፴፪፡ ፲፯።
መዝ፡ ፻፮፡ ፴፯። ራእ፡ ፱፡ ፳።

፳፩፡ የጌታን፡ ጽዋና፡ የሰይጣናትን፡ ጽዋ፡ ትጠጡ፡ ዘንድ፡ አትችሉም። የጌታን፡ ማዕድና፡ የሰይጣናትን፡ ማዕድ፡ ትቀበሉ፡ ዘንድ፡ አትችሉም። ፪፡ ቆሮ፡ ፮፡ ፲፭።

፳፪፡ ወይስ፡ ጌታን፡ እናስቀናውን። ወይስ፡ እኛ፡ ከርሱን፡ እንበረታለን።

፳፫፡ ሁሉ፡ ተፈቶልኛል፡ ነገር፡ ግን፡ ሁሉ፡ አይስማማኝም። ሁሉ፡ ተፈቶኛል። ነገር፡ ግን፡ ሁሉ፡ የሚሠራ፡ አይደለም፡ ም፡ ፮፡ ፲፪።

፳፬፡ ማንም፡ ለራሱ፡ ብቻ፡ የሚረባውን፡ አይሻ፡ ያም፡ ለባልንጀራው፡ የሚረባውን፡ እንጂ።
ቍ፡ ፴፫። ሮሜ፡ ፲፭፡ ፪።

፳፭፡ በገቢያ፡ የሚሸጠውን፡ ሁሉ፡ ብሉ፡ ሳትመራመሩ፡ ስለ፡ ልባችሁ፡ አሳብ። ፩፡ ጢሞ፡ ፬፡ ፬።
ሮሜ፡ ፲፬፡ ፪—፮።

፳፮፡ ምድር፡ ለእግዚአብሔር፡ ናትና፡ በርስዋም፡ ያለ፡ሁሉ፥ መዝ፡ ፳፬፡ ፩፡፡

፳፯፡ ከማያምኑ፡ ሰዎች፡ አንድ፡ ለምሳ፡ ቢጠራች ሁ፡ልትሔዱም፡ ብትወዱ። ያቀረበላችሁን፡ ሁሉ፡ብ ሉ፡ ማናቸውንም፡ አትመርምሩ፡ ስለ፡ ልባችሁ፡ አ ሳብ።

፳፰፡ *የሚላችሁ፡ግን፡ቢኖር፡ይህ፡ለጣዖት፡የታረ ደ፡ ነው፡ አትብሉት፡ ስለዚያ፡ ስላስታወቃችሁ፡ ስለ፡ ልቡም፡ አሳብ። *ም፡ ፰፡ ፯፡፡

፳፱፡ ስለ፡አሳባችሁ፡የምል፡ አይደለሁም፡ ስለ፡ ባ ልንጀራችሁ፡አሳብ፡እንጂ። ስለ፡ምንስ፡አርነቴ፡ ከሌ ላው፡አሳብ፡ይፈረደል።

፴፡ የተቀበልሁትንስ፡ በምስጋና፡ ከተቀበልሁት፡ ስለ፡ ምን፡ ይሰድቡብኛል፡ እኔ፡ ባመሰገንሁበት። ፩፡ ጢሞ፡ ፬፡ ፬፡፡

፴፩፡ አሁንም፡ ብትበሉ፡ ወይም፡ ብትጠጡ፡ ወይ ስ፡ምንም፡ብታደርጉ፡ ሁሉን፡ ስለ፡ እግዚአብሔር፡ክ ብር፡ አድርጉት። ቆላ፡ ፫፡ ፲፯፡፡

፴፪፡ ያለ፡መሰናክል፡ ሁኑ፡ለአይሁድ፡ ለአረማው ያንም፡ ለእግዚአብሔርም፡ ቤተ፡ ክርስቲያን። ሮሜ፡ ፲፬፡ ፲፫፡፡

፴፫፡ እኔ፡በሁሉ፡እንደ፡ሆንሁ፡ ሁሉንም፡ ደስ፡አሰ ኛለሁ። እኔንም፡ደስ፡ የሚያሰኘኝን፡ሸቴ፡አይደለሁ ም፡ እጅግ፡ ሰዎችን፡ ደስ፡ የሚያሰኛቸውን፡ እንጂ፡ ይድኑ፡ ዘንድ። ም፡ ፱፡ ፳፡፡

ምዕራፍ፡ ፲፩፡

፩፡ እኔን፡ *ምሰሉ፡ እኔ፡ ክርስቶስን፡ እንደ፡ መሰል ሁ። *ም፡ ፬፡ ፲፮፡፡ ፊል፡ ፫፡ ፲፯፡፡

፪፡ እኔም፡ አመሰግናችኋለሁ፡ ወንድሞቼ፡ ሆይ፡ በኔ፡ ያለውን፡ ሁሉ፡ስለ፡ ማስባችሁ፡ ትእዛዚቱንም፡ ፈጽማችሁ፡ ይዛችኋልና፡እንደ፡ ሰጠኋችሁ።

፫፡ ታውቁም፡ዘንድ፡እወዳለሁ፡የሰው፡ሁሉ፡ራስ፡ ክርስቶስ፡እንደ፡ሆነ።የሴትም፡ ራስዋ፡ *ወንድ፡ነው፡ የክርስቶስም፡ራሱ፡ †እግዚአብሔር፡ ነው። *ኤፌ፡ ፭፡ ፳፫፡፡ †፩፡ ቆሮ፡ ፫፡ ፳፫፡፡

፬፡ ወንድ፡ ሁሉ፡ሲጸልይ፡ትንቢትም፡ሲናገር፡ ቢሆ ን፡ ራሱን፡ ተከናንቦ፡ራሱን፡ ያሰድባል። ም፡ ፲፪፡ ፲፡፡ ፲፬፡ ፩፡፡

፭፡ ሴት፡ ሁሉ፡ግን፡ ስጸልይ፡ ወይም፡ ትንቢት፡ስት ናገር፡ ራስዋን፡ ባትከናነብ፡ ራስዋን፡ ታሰድባለች። ይ ህ፡ አንድ፡ ነውና፡ የተላጨች፡ ከሆነች።

፮፡ ሴት፡ ራስዋን፡ ካልሸፈነች፡ ደግሞ፡ ጸጕርዋን፡ ትቈረጥ፡በሴትም፡ቢከፋባት፡ጸጕርዋን፡መቈረጥ፡ ወይም፡መላጨት፡ ራስዋን፡ ትከናነብ።

፯፡ ወንድ፡ይከናነብ፡ዘንድ፡አይገባምና፡ የእግዚአ ብሔር፡ ምሳሌ፡ ክብሩም፡ ነውና፡ሴት፡ ግን፡ የወንድ፡ ክብር፡ ናት። ዘፍ፡ ፩፡ ፳፯፡፡

፰፡ ወንድ፡ ከሴት፡ አልተገኘምና፡ ሴት፡ ከወንድ፡ እንጂ። ዘፍ፡ ፪፡ ፲፰፡ ፳፫፡፡

፱፡ ወንድም፡ ስለ፡ሴት፡አልተፈጠረም፡ሴት፡ስለ፡ ወንድ፡ ተፈጠረች፡እንጂ።

፲፡ ስለዚህም፡ ለሴት፡ ይገባል፡ በራስዋ፡ ሥልጣን፡ ይሆንላት፡ ዘንድ፡ ስለ፡ መላእክት።

፲፩፡ ነገር፡ግን፡ ሴት፡ ያለ፡ ወንድ፡ አትሆንም፡ ወን ድም፡ ያለ፡ ሴት፡ በእግዚአብሔር፡ ዘንድ።

፲፪፡ ሴት፡ከወንድ፡እንደ፡ ተገኘች፡ እንደሁም፡ወ ንድ፡ከሴት። ሁሉ፡ግን፡ ከእግዚአብሔር፡ ነው።

፲፫፡ እስኪ፡ ፍረዱ፡ እላንት፡ ለራሳችሁ፡ ለሴት፡ ያ ምርባታልን፡ በእግዚአብሔር፡ፊት፡ ትጸልይ፡ ዘንድ፡ ራስዋ፡ተገልጦ።

፲፬፡ ፍጥረትዋስ፡ አያስታውቃችሁምን፡ ወንድ፡ ጕተናውን፡ቢያስረዝም፡ በርሱ፡ ኀሰቍልና፡ እንዲሆ ንበት።

፲፭፡ሴት፡ግን፡ጸጕርዋን፡ብታስረዝም፡ለርስዋ፡ክብ ርዋ፡ ነው። ጸጕርዋ፡ ተሰጥዋታልና፡ ስለ፡ መሸፈኛ።

፲፮፡ ማንም፡ የሚከራከር፡ ቢሆን፡ ለኛ፡ እንደዚህ፡ ያለ፡ወግ፡ የለነም፡ ለእግዚአብሔርም፡ ቤተ፡ ክርስቲ ያናት።

፲፯፡ በዚህ፡በማዛችሁ፡ግን፡አመሰግኛችሁ፡ አይደ ለም፡ ትሰበሰባላችሁና፡ ወደሚያምር፡ አይደለም፡ ወደሚከፋ፡ እንጂ። ቍ፡ ፳፪፡፡

፲፰፡ አስቀድሞ፡በቤተ፡ክርስቲያን፡*በተሰበሰባች ሁ፡ጊዜ፡እርሱ፡በርሳችሁ፡ ክርክር፡ እንደለባችሁ፡ እሰ ማለሁና፡ በዚያውም፡ ከፊዬ፡ አምናለሁ።

፲፱፡ መለያየት፡*በላንት፡ መካከል፡ ይሆን፡ ዘንድ፡ አይቀርምና፡በላንት፡የተፈተኑት፡†ይገለጡ፡ዘንድ። *ም፡ ፩፡ ፲፡ ፲፩፡ ፲፪፡፡ ፫፡ ፫፡፡ ማቴ፡ ፲፡ ፴፬፡ ፴፭፡፡ ፩፡ ዮሐ፡ ፪፡ ፲፱፡፡ †ዘዳግ፡ ፲፫፡ ፫፡፡ ሉቃ፡ ፪፡ ፴፭፡፡

፳፡ እላንት፡ግን፡ ወደንድ፡ ስፍራ፡ በተሰበሰባችሁ፡ ጊዜ፡የጌታችንን፡ እራት፡ የምትበሉ፡ አይደላችሁም።

፳፩፡ ኢያንዳንዱ፡ ምሳውን፡ አስቀድሞ፡ ይበላል ና። አንዱ፡ ተርቦ፡ አንዱም፡ ሰክሮ።

፳፪፡ ቤት፡የላችሁምን፡የምትበሉበት፡የምጠጡ በትስ። ወይስ፡ የእግዚአብሔርን፡ ማኅበር፡ *ትንቃ ላችሁ፡ አንዳች፡ የሌላቸውንም፡ ታሳፍራላችሁ። ም ንስ፡ልበላችሁ። በዚህ፡ላመስግናችሁን። ከቶም፡ አላ መሰግናችሁም። *ያዕ፡ ፪፡ ፭፡ ፮፡፡

፳፫፡ እኔ፡ ከጌታ፡ ትእዛዝ፡ ወስጃለሁና፡ ለላንት፡ ደግሞ፡ የሰጠኋችሁን። *ጌታችን፡ የሱስ፡ በዚያች፡ በ ተያዘባት፡ ሌት፡ እንጀራ፡ እንደ፡ ወሰደ። *ማቴ፡ ፳፮፡ ፳፮፡፡ ማር፡ ፲፬፡ ፲፪፡፡ ሉቃ፡ ፳፪፡ ፲፱፡፡

፳፬፡ ባመሰገነም፡ጊዜ፡ቈረሰው፡ አለም። እንኩ፡ ብሉ። ይህ፡ነው፡ ሥጋዬ፡ ስለላንት፡ የሚሰበረው። ይ ህነን፡ አድርጉት፡ ለመታሰቤ።

፳፭፡ እንደሁም፡ጽዋውን፡ወሰደ፡ራታቸውን፡ከበ ሉ፡ በኋላ፡እንደህ፡ ቢል።ይህ፡ጽዋ፡ አዲስ፡ ሥርዓት፡ ነው፡በደሜ። ይህነን፡ አድርጉ፡ በጠጣችሁት፡ ጊዜ፡ ሁ ሉ፡ለመታሰቤ።

፳፮፤ ይህነንም፡ እንጀራ፡ በበላችሁ፡ ጊዜ፡ ሁሉ፡ ይህነንም፡ ጽዋ፡ በጠጣችሁ፡ ጊዜ፡ ሁሉ፡ የጌታን፡ ሞት፡ ታሳያላችሁ፡*እስኪመጣ፡ድረስ። *ማቴ፡ ፳፮፤ ፲፫። ና፡ ፳፯፤ ፳፱። ዮሐ፡ ፲፱፤ ፫።

፳፯፤ ስለዚህም፡ ይህነን፡ እንጀራ፡ የሚበላ፡ ሁሉ፡ የጌታንም፡ ጽዋ፡ የሚጠጣ፡ ሳይገባው፡ በጌታ፡ ሥጋ፡ ብደሙም፡ ዕዳ፡ ይገባል።

፳፰፤ ሰውም፡ራሱን፡ይፈትን፡እንደሁም፡ ይህን፡ እንጀራ፡ይብላ፡ ይህንመ፡ ጽዋ፡ ይጠጣ።

፳፱፤ ሳይገባው፡ ግን፡ ቢበላ፡ ቢጠጣም፡ ለራሱ፡ ኩነኔ፡ይበላል፡ይጠጣልም፡ የጌታን፡ሥጋ፡ባይለይ።

፴፤ ስለዚህም፡ ከላንት፡ብዙ፡ ድውያን፡ አሉ፡ደካሞችም፡ ብዙም፡ የተኙ፡ አሉ።

፴፩፤ በራሳችንም፡ *ብንፈርድ፡ባልተፈረደብነም። *መዝ፡ ፴፪፤ ፭።

፴፪፤ ቢፈረድብነም፡ እግዚአብሔር፡*የሚገሥጸን፡ነው፡ከዓለም፡ጋራ፡እንደንኰነን።*ዕብ፡ ፲፪፤ ፭፤ ፯።

፴፫፤ ስለዚህም፡ ወንድሞቼ፡ ለመብላት፡ በተሰበሰባችሁ፡ ጊዜ፡ እርሱ፡ በርሳችሁ፡ ይጠባበቅ።

፴፬፤ ማናቸው፡ ግን፡ ከላንት፡ ቢራብ፡ በቤቱ፡ ይብላ፡ለፍርድ፡ እንዳትሰበሰቡ። የቀረውንም፡ነገር፡ ወደ ላንት፡ በመጣሁ፡ ጊዜ፡ እሠራላችኋለሁ።

## ምዕራፍ፡ ፲፪፤

፩፤ ስለ፡ መንፈሳዊ፡ ስጥወታ፡ ግን፡ ወንድሞቼ፡ ሆይ፡ *እወዳለሁ፡ታውቁ፡ ዘንድ። *ም፡ ፲፤ ፩።

፪፤ *ታውቃላችሁና፡ አሕዛብ፡ እንደ፡ ነበራችሁ፡ድምጽ፡ የሌለውን፡ ጣዖት፡ የምታመልኩ፡ ሳታስተውሉ። *ም፡ ፮፤ ፲፩፤ ኤፌ፡ ፪፤ ፲፩፤ ፲፪።

፫፤ ስለዚህም፡ አስታውቃችኋለሁ፡ *ማንም፡ በእግዚአብሔር፡መንፈስ፡ የሚናገር፡እንደ፡ሌላ፡ የሱስ፡ የተረገመ፡ነው፡ የሚል። ማንም፡ አይችልም፡ ይል፡ዘንድ፡የሱስ፡ጌታ፡ነው፡ በመንፈስ፡ ቅዱስ፡ ካልሆነ። *ማር፡ ፱፤ ፴፱። ፩፤ ዮሐ፡ ፬፤ ፪፡ ፫።

፬፤ ስጥወታ፡ግን፡ *ልዩ፡ ልዩ፡ ነው፡ መንፈስ፡ አንድ፡ ሲሆን። *ሮሚ፡ ፲፪፤ ፮። ኤፌ፡ ፬፤ ፬። ዕብ፡ ፪፤ ፬።

፭፤ ለማገልገልም፡ *ልዩነት፡ አለው፡ እግዚአብሔር፡ ግን፡ እርሱ፡ አንድ፡ ነው። *ኤፌ፡ ፬፤ ፲፩።

፮፤ ኃይልም፡ ልዩ፡ ነው። ነገር፡ ግን፡*ሁሉን፡ በሁሉ፡ የሚያደርግ፡ እግዚአብሔር፡ አንድ፡ ነው። *ኤፌ፡ ፩፤ ፳፫።

፯፤ ለእያንዳንዱ፡ ግን፡ ከመንፈስ፡ ይገለጣል፡ የሚረባውን፡ ያህል። ም፡ ፲፬፤ ፳፮።

፰፤ ላንዱም፡ *የጥበብ፡ ነገር፡ በመንፈስ፡ ይሰጠዋል። ለሌላውም፡†የውቀት፡ነገር፡በዚያው፡ መንፈስ። *ም፡ ፪፤ ፮። †ም፡ ፩፤ ፭።

፱፤ ለሌላውም፡ሃይማኖት፡ ይሰጠዋል፡ በዚያው፡ መንፈስ። ለሌላውም፡ድውይ፡ የመፈወስ፡ ጸጋ፡ በዚያው፡ መንፈስ።

፲፤ ከርሳቸውም፡ ኃይል፡ የተሰጠው፡ አለ። ትንቢትም፡ የተሰጠው፡ አለ። ለሌላውም፡ መናፍስትን፡ መለየት። ለሌላውም፡*ቋንቋን፡ሁሉ፡ ማወቅ። ለሌላውም፡ ቋንቋን፡ መተርጐም። *ም፡ ፲፬፤ ፭። የሐዋ፡ ፪፤ ፬።

፲፩፤ ይህነንም፡ ነገር፡ ሁሉ፡እርሱ፡አንዱ፡ መንፈስ፡ ይሰራል፡ለሁሉም፡እያንዳንዱ፡ እንደ፡ ወደደ፡ *ይከፍለዋል። *ም፡ ፯፤ ፯። ሮሚ፡ ፲፪፤ ፫፤ ፮። ኤፌ፡ ፬፤ ፯።

፲፪፤ ሥጋም፡ አንድ፡ እንደ፡ ሆነ፡ ብዙም፡ ብልቶች፡ እንዳለው። *የሥጋም፡ ብልቶች፡ ምንም፡ ብዙ፡ ቢሆኑ፡ እርሱ፡ አንድ፡ ሥጋ፡ ነው፡ እንደሁም፡ ደግሞ፡ ክርስቶስ። *ም፡ ፲፤ ፲፯።

፲፫፤ እኛም፡ሁላችን፡ ባንድ፡ መንፈስ፡ ተጠመቅን፡ ወደንድ፡ ሥጋ፡ አይሁድም፡ ብንሆን፡ ወይም፡ አሕዛብ። ባሮችም፡የሰው፡ልጆችም፡ሁላችንም፡አንድ፡ መንፈስ፡ ሰጣነ፡ ገላት፡ ፫፤ ፳፰።

፲፬፤ እንዲሁም፡ሥጋ፡አንድ፡ብልት፡ አይደለምና፡ ነገር፡ ግን፡ ብዙ፡ ብልቶች፡ ናቸው። ቍ፡ ፳።

፲፭፤ እግርም፡ብትል፡እኔ፡ እጅ፡አይደለሁመና፡ ከሥጋ፡ወገን፡ አይደለሁም። ስለዚህን፡ ከሥጋ፡ መሆንዋ፡ ይቀራልን።

፲፮፤ ጆሮም፡ብትል፡ ዓይን፡ አይደለሁምና፡ እኔ፡ ከሥጋ፡ ወገን፡ አልሆንም። ስለዚህን፡ የሥጋ፡ ወገን፡ ከመሆን፡ይቀራልን።

፲፯፤ ሥጋ፡ ሁሉ፡ ዓይን፡ ቢሆን፡ መስማት፡ ወዴት፡ በተገኘ። ሁሉም፡ መስማት፡ ቢሆን፡ወዴት፡ በተገኘ፡ ማሽተት።

፲፰፤ አሁን፡ ግን፡ እግዚአብሔር፡ *ብልቶችን፡ እያንዳንዱ፡ በሥጋ፡ አስቀመጠ፡ እርሱ፡ እንደ፡ ወደደ። *ቀለ፡ ፪፤ ፲፱።

፲፱፤ ሁሉስ፡አንድ፡ብልት፡ቢሆን፡ ሥጋ፡ወዴት፡ በደረሰ።

፳፤ አሁንም፡ እጅግ፡ብልቶች፡ ነው፡ ሥጋ፡ ግን፡ አንድ፡ነው። ቍ፡ ፲፬።

፳፩፤ ዓይንም፡ አይቻላትም፡ እጅን፡ ትላት፡ ዘንድ፡ አልሻሽም። ራስም፡ ደግሞ፡ አይችልም፡ እግሮችን፡ ይላቸው፡ ዘንድ፡ አልሻችሁም።

፳፪፤ ነገር፡ ግን፡ ታናሽ፡ የምትመስልህ፡ ብልት፡ እርስዋን፡ ይልቅ፡ ትሻታለህ።

፳፫፤ ከሥጋ፡ ብልት፡ ሁሉም፡ የተናቀች፡ የምትመስልህ፡ ለርስዋ፡ ክብር፡ ትጨምርላታለህ፡ የምናፍርባትም፡ብልታችን፡ ለርስዋ፡ እጅግ፡ ክብር፡ ይጨመርላታል።

፳፬፤ ለከበረችው፡ ብልታችን፡ ግን፡ ክብር፡ አንሻላትም። ነገር፡ ግን፡ እግዚአብሔር፡ ሥጋን፡ አሰማማ፡ ለተናቀውም፡ የበለጠ፡ ክብር፡ ሰጠው።

፳፭፤ በሥጋ፡ መለያየት፡ እንዳይሆን። ብልት፡ እርሱ፡ በርሱ፡ ባንድ፡ ያስባል፡ እንጂ።

፳፮፤ አንድ፡ ብልትም፡ ቢታመም፡ ብልት፡ሁሉ፡ ከ

ርሱ፡ ጋራ፡ ይታመማል። አንድ፡ ብልትም፡ ደስ፡ ቢለው፡ ብልት፡ ሁሉ፡ ከርሱ፡ ጋራ፡ ደስ፡ ይለዋል።

፳፯፡ እላንትም፡ ዛሬ፡ የክርስቶስ፡ ሥጋ፡ ናችሁ፡ ባላችሁብትም፡ ብልቶች፡ ናችሁ። ሮሜ፡ ፲፪፡ ፭። ኤፌ፡ ፭፡ ፴።

፳፰፡ እግዚአብሔርም፡ በቤተ፡ ክርስቲያን፡ ሰዎችን፡ ሠራ። አስቀድሞ፡ ሐዋርያትን፡ሁለተኛም፡ነቢያትን። ሶስተኛም፡መምህራንን። ከርሳቸው፡በኋላ፡ ተአምራት፡ የሚያደርጉትን። ደግሞም፡ ድውይ፡ የመፈወስ፡ ጸጋ። የሚራዱ፤ን። ሠርቾንም። ልዩ፡ ልዩ፡ ቋንቋ፡የሚያውቁንም። ኤፌ፡ ፬፡ ፲፩፡ ፲፪።

፳፱፡ ሁሉን፡ ሐዋርያት፡ ናቸው። ወይስ፡ ሁሉን፡ ነቢያት፡ ናቸው። እንጀ፡ ሁሉን፡ መምህራን፡ናቸው። ወይም፡ ሁሉን፡ ተአምራት፡ ያደርጋለ።

፴፡ ወይስ፡ ለሁሉን፡ ተሰጥትዋቸዋል፡ ድውይ፡ የመፈወስ፡ ጸጋ። ሁሉስ፡ በቋንቋን፡ ይናገሩ። ወይስ፡ ሁሉን፡ ይተረጕማሉ።

፴፩፡ ነገር፡ ግን፡ *ለምትበልጥ፡ ጸጋ፡ ቅኑ። ደግሞም፡ሌላ፡መንገድ፡እጅግ፡ የሚበልጥ፡አሳያችኋለሁ። *ም፡ ፲፬፡ ፩።

ምዕራፍ፡ ፲፫፡

፩፡ በሰዎችና፡ በመላእክት፡ ቋንቋ፡ ብናገር፡ ፍቅርም፡ባትኖርብኝ፡እንደሚጮህ፡ ናስ፡ ሆንሁ። ወይም፡ እንደሚጮህ፡ ጸናጽል።

፪፡ ትንቢትም፡ ብትኖርልኝ፡ ምሥጢርንም፡ ሁሉ፡ ባውቅ፡ ዕውቀትንም፡ ሁሉ። *ሃይማኖትም፡ ሁሉ፡ ብትኖርልኝ፡ ተራራ፡ እስካፈልስ፡ ድረስ። ፍቅርም፡ ከሌለኝ፡ አንዳችም፡ አይደለሁም። *ማቴ፡ ፯፡ ፳፪። †ማቴ፡ ፲፯፡ ፳።

፫፡ ለድኆችም፡ *ገንዘቤን፡ሁሉ፡ባበላ፡ሥጋዬንም፡ ብሳት፡ ለመቃጠል፡ ብሰጥ፡ ፍቅርም፡ ከሌለኝ። ያ፡ ምንም፡አይረባኝም። *ማቴ፡ ፮፡ ፩። ዮሐ፡ ፲፭፡ ፲፫። ሮሜ፡ ፲፪፡ ፳፡ ፳። ፩፡ዮሐ፡ ፫፡ ፲፯።

፬፡ ፍቅር፡ *ታጋሽ፡ ናት፡ በጎም፡ ናት። ፍቅር፡ አትቀናም። ፍቅር፡ አትመካም፡ አትነፋም። *ምሳ፡ ፲፡ ፲፪።

፭፡ ፊትዋን፡ አታጠቍርም፡ *ገንዘብዋን፡ አትሻም። ተሎ፡ አትቈጣም። በክፉ፡ አታስብም። *ፊል፡ ፪፡ ፬፡ ፳፩።

፮፡ በኃጢአት፡ደስ፡አይላትም፡በውነት፡ደስ፡ይላታል፡ እንጂ።

፯፡ ሁሉን፡ *ትችላለች። ሁሉን፡ ታምናለች። ሁሉን፡ ተስፋ፡ ታደርጋለች። በሁሉ፡ትታገሣለች። *ም፡ ፱፡ ፲፪። ምሳ፡ ፲፡ ፲፪። ሮሜ፡ ፲፭፡ ፩።

፰፡ ፍቅር፡ ከቶ፡ አትወድቅም። ትንቢት፡ ታልፋለች ና። ቋንቋም፡ ትቀራለች። ዕውቀትም፡ ትጠፋለች።

፱፡ ከውቀት፡ ከፊለን፡ እናውቃለንና። ከትንቢቱም፡ ከፊለን፡ እንናገራለን።

፲፡ *ፍጹም፡ ግን፡ የሚሆን፡ በደረሰ፡ ጊዜ፡ ሁሉ፡ ያልፋል፡ ከፊለን፡ ያወቅነው። *ኤፌ፡ ፬፡ ፲፫።

፲፩፡ ሕፃን፡ በነበርሁ፡ ጊዜ፡ እንደ፡ ሕፃን፡ እናገር፡ ነበርሁ፡ እንደ፡ ሕፃን፡ አውቅ፡ ነበርሁ፡ እንደ፡ ሕፃንም፡ አስብ፡ ነበርሁ። ጕልማሳ፡ ግን፡ በሆንሁ፡ ጊዜ፡ የሕፃኑን፡ ጠባይ፡ ተውሁ።

፲፪፡ ዛሬ፡ እኛ፡ እናያለንና፡ ምሳሌ፡ በመስተዋት፡ እንድናይ። የዚያን፡ ጊዜ፡ ግን፡ ፊት፡ ለፊት፡ እናያለን። ዛሬ፡ ከውቀቱ፡ ከፊዩ፡ አውቃለሁ። የዚያን፡ ጊዜም፡ አውቃለሁ፡ እኔ፡ ደግሞ፡ እንደታወቅሁ። ፪፡ ቆሮ፡ ፭፡ ፯።

፲፫፡ አሁንም፡ ትኖራለች፡ ሃይማኖት፡ ተስፋም፡ ፍቅርም፡ እሌህ፡ ሶስቱ። ከሌህ፡ ግን፡ የምትበልጠው፡ *ፍቅር፡ ናት። *፩፡ ተሰ፡ ፩፡ ፫። ፩፡ ዮሐ፡ ፬፡ ፲፮።

ምዕራፍ፡ ፲፬፡

፩፡ ተቀደደሙ፡ ፍቅርን፡ ለመሻት፡ *መንፈስ፡ ቅዱስም፡ ለሚሰጠው፡ ጸጋ፡ ቅኑ። የሚበልጠውም፡ †ትንቢት፡ ትናገሩ፡ ዘንድ። *ም፡ ፲፪፡ ፴፩። †ም፡ ፲፪፡ ፲።

፪፡ በቋንቋ፡ የሚናገር፡ ለሰው፡ አይናገርምና፡ ለእግዚአብሔር፡ እንጅ። ነገሩን፡የሚያስተውል፡የለምና፡ በመንፈስ፡ግን፡ ምሥጢር፡ ይናገራል።

፫፡ ትንቢት፡ የሚናገር፡ ግን፡ ለሰዎች፡ ይናገራል፡ ለማነጽ፡ ለመገሠፅም፡ ለማጽናትም።

፬፡ በቋንቋ፡የሚናገር፡ራሱን፡ ይሠራል። ትንቢት፡ የሚናገር፡ ግን፡ ቤተ፡ክርስቲያንን፡ ይሠራል።

፭፡ ሁላችሁ፡ በቋንቋ፡ ትናገሩ፡ዘንድ፡ *እወደለሁ፡ ከዚያ፡ የሚበልጥ፡ግን፡ ትንቢት፡ትናገሩ፡ዘንድ። ትንቢት፡የሚናገር፡ በቋንቋ፡ከሚናገር፡ ይበልጣልና፡ የተረጕመው፡ካልሆነ፡ቤተ፡ክርስቲያንን፡ይሠራ፡ዘንድ። *ዘኍል፡ ፲፩፡ ፳፱።

፮፡ አሁንም፡ወንድሞቼ፡ሆይ፡ወደላንት፡ብመጣ፡ በብዙ፡ ቋንቋስ፡ በማታስተውሉት፡ ብነግራችሁ፡ ምንድር፡ነው፡ የምረባችሁ፡ በራእይ፡ ካልተናገርኋችሁ፡ ወይም፡ *በውቀት፡ ወይም፡ በትንቢት፡ወይም፡በማስተማር። *ም፡ ፲፪፡ ፰።

፯፡ አዋን፡ ደግሞ፡ ነፍስ፡የሌለበት፡ፍጥረት፡ ድምጽ፡ይሰጣል፡ በገና፡ሁነ፡መሰንቆም፡ሁነ፡ዜማውንም፡ ካለየ፡ እንዴት፡ የሚመታውን፡ በገና፡ የሚመታውንስ፡ መሰንቆ፡ ሰው፡ ያውቃል።

፰፡ መለከትስ፡ ቢነፋ፡በማይታወቅ፡ድምጽ፡ማን፡ ይዘጋጃል፡ ለሰልፍ።

፱፡ እንደሁም፡ እላንት፡ በቋንቋ፡ ብትናገሩ፡ ያነንም፡ ባትተረጕሙት፡ እንዴት፡ ይታወቃል፡ የምትሉት። የዚየን፡ ጊዜም፡ ከነፋስ፡ ጋራ፡ እንድትናገሩ፡ ናችሁ።

፲፡ በዚህ፡ ዓለም፡ እጅግ፡ ልዩ፡ ልዩ፡ ቋንቋ፡ አለ። ከርሱም፡ አንድ፡ አይገኝም፡ ድምፅ፡ የሌለው።

፲፩፡ እኔም፡የድምፁን፡ ኃይል፡ ባላውቅ፡በሚናገረው፡ ዘንድ፡ ደንቆር፡ ሆንሁ። የሚናገረኝም፡ ደግሞ፡ ደንቆሮ፡ ሆነ፡ በኔ፡ ዘንድ።

፲፪፡ እንደሁም፡ እላንተ፡ ደግሞ፡ለመንፈስ፡ ቅዱስ፡ ስጦታ፡ ትቀናላችሁና፡ እኹ፡ትበዙ፡ ዘንድ፡ቤተ፡ክርስቲያንን፡እንድትሠሩ። ቆ፡ ፩፡—፬፡፡

፲፫፡ ከላንትም፡ በማያስተውለው፡ *ቋንቋ፡ የሚናገር፡ ይጸልይ፡ነገሩን፡ መተርጐም፡ እንዲችል። *ም፡ ፲፪፡ ፲፡፡

፲፬፡ እነሆ፡ እኔ፡ በሌላ፡ ቋንቋ፡ ብጸልይ፡ ሰውነቴ፡ ይጸልያል፡ ለአእምሮዬ፡ግን፡ ፍሬ፡ የለውም።

፲፭፡ እንግዲህስ፡ ምን፡ይደረግ። በመንፈስ፡እጸልያለሁ። ነገር፡ግን፡ በአእምሮዬ፡እጸልያለሁ፡ ደግሞ። በመንፈስ፡ *አመሰግናለሁ፡ በአእምሮዬም፡ አመሰግናለሁ፡ ደግሞ። *ኤፌ፡ ፭፡ ፲፱፡፡

፲፮፡ እንዲያማ፡ካልሆነ፡አንተ፡በመንፈስ፡ብትመርቅ፡ያ፡በማያውቀው፡ ስፍራ፡ የቆመው፡ እንዴት፡ ይላል፡ አሜን፡ ባንተ፡ ምስጋና፡ አንተ፡ የምትለውን፡ አያውቅምና።

፲፯፡ አንተስ፡እጅግ፡መልካም፡መረቅህ፡ ነገር፡ግን፡ ባልንጀራህ፡ በዚያ፡ አይረባም።

፲፰፡ እኔ፡እግዚአብሔርን፡አመሰግናለሁ፡ በልሳን፡ እናገራለሁና፡ ከሁላችሁ፡ ይበልጥ።

፲፱፡ ነገር፡ ግን፡ እወዳለሁ፡ በቤተ፡ክርስቲያን፡አምስት፡ ቃል፡ በአእምሮዬ፡እናገር፡ ዘንድ፡ ሌሎችን፡ ደግሞ፡ አስተምር፡ ዘንድ፡አሥር፡ ሺህ፡ቃላት፡ በልሳን፡ ከመናገር፡ ይልቅ።

፳፡ ወንድሞቼ፡ ሆይ፡በአእምሮ፡ *ሕፃናት፡አትሁኑ፡ ነገር፡ ግን፡ *በክፋት፡ ሕፃናት፡ ሁኑ። በአእምሮ፡ ግን፡ ፍጹማን፡ ሁኑ። *ኤፌ፡ ፬፡ ፲፬፡፡ †ማቴ፡ ፲፰፡ ፫፡፡

፳፩፡ *በኦሪት፡ ተጽፏልና፡ በልዩ፡ ቋንቋ፡ በሌላም፡ ነገር፡ እሌህን፡ ሕዝብ፡ እናገራቸዋለሁ፡ እንደሁም፡ ደግሞ፡ አይሰሙኝም፡ ይላል፡ እግዚአብሔር። *ዘዳግ፡ ፳፰፡ ፵፱፡፡ ኢሳ፡ ፳፰፡ ፲፩፡ ፲፪፡፡

፳፪፡ ፈጽሞ፡ ልዩ፡ ቋንቋ፡ ለምልክት፡ ተቀመጠ፡ ላመኑት፡ አይደለም፡ ላላመኑት፡ እንጂ፡ ትንቢት፡ ግን፡ ለማያምኑ፡ አይደለም፡ ለሚያምኑ፡ እንጂ።

፳፫፡ ጉባኤም፡ ሁሉ፡ ቢከማች፡ሁሉም፡በልዩ፡ልዩ፡ ቋንቋ፡ ቢናገሩ፡ የማያውቁም፡ ቢገቡባችሁ፡ የማያምኑም። አይሉምን፡ እሌህ፡ ፈጽመው፡ አእምሮዋቸው፡ ጠፋ፡ አበዱም።

፳፬፡ ሁሉ፡ ግን፡ ትንቢት፡ ቢናገሩ፡ የማያውቅም፡ ቢገባባቸው፡ወይም፡ የማያምን፡ ከሁሉ፡ ይገሠጻል፡ ከሁሉም፡ ይፈረደል።

፳፭፡ እንደሁም፡ የልቡ፡ ምሥጢር፡ ትገለጣለች፡ በዚያን፡ጊዜም፡ በግምባሩ፡ ይወድቃል፡ ለእግዚአብሔርም፡ ይሰግዳል፡ ይላልም፡ እግዚአብሔር፡ በውነት፡ ከላንት፡ ጋራ፡ ነው።

፳፮፡ እንግዲህ፡ ምንድር፡ ነው፡ ወንድሞቼ፡ ሆይ። *በተሰበሰባችሁ፡ ጊዜ፡መዝሙር፡ ያለው፡ ነው። ሌላም፡ †ትምህርት፡ ያለው። ቋንቋም፡ ያለው፡ ራእይም፡ ያለው። ትርጓሚም፡ ያለው። ያም፡ ሁሉ፡ **ለመንጸት፡ ይሁን። *ም፡ ፲፩፡ ፲፰፡ ፳፡፡ †ም፡ ፲፪፡ ፰፡—፲፡፡ **ኤፌ፡ ፬፡ ፲፪፡፡

፳፯፡ ማንም፡ በቋንቋ፡ ቢናገር፡ ሁለት፡ ይናገሩ፡ ወይም፡ ከዚያ፡ የበለጠ፡ ሶስት። ኢያንዳንዲም፡ይናገር፡ ሌላውም፡ ይተርጉምለት።

፳፰፡ አስተርጓሚም፡ ባይኖር፡ በቤተ፡ክርስቲያን፡ ዝም፡ ይበል፡ ያ፡ በሌላ፡ ቋንቋ፡ የሚናገረው፡ ለራሱና፡ ለእግዚአብሔር፡ ይናገር።

፳፱፡ ከነቢያትም፡ ደግሞ፡ይናገሩ፡ሁለት፡ወይም፡ ሶስት፡ ሌሎችም፡ ያስተውሉ።

፴፡ ለሌላውም፡ ራእይ፡ ቢገለጥለት፡ እርሱ፡ ተቀምጦ፡ የፊተኛው፡ ዘንድ፡ ይበል።

፴፩፡ ትንቢት፡ ትናገሩ፡ ዘንድ፡ ትችላላችሁና፡ ሁላችሁ፡ ኢያንዳንዳችሁ። ሁሉ፡ እንዲማር፡ሁሉም፡ ደስ፡ ይለው፡ ዘንድ።

፴፪፡ የነቢያት፡ መንፈስ፡ ለነቢያት፡ ይገዛልና። ም፡ ፲፪፡ ፱፡—፲፩፡፡

፴፫፡ እግዚአብሔር፡ የመለየት፡ አምላክ፡ አይደለምና፡ የዕርቅ፡ እንጂ፡ በቅዱሳን፡ ቤተ፡ ክርስቲያን፡ ሁሉ፡እንዲያደርግ።

፴፬፡ *ሴቶቻችሁ፡ በቤተ፡ ክርስቲያን፡ ዝም፡ ይበሉ፡ አልታዘዙምና፡ ይናገሩ፡ ዘንድ፡ †ይገዙ፡ ዘንድ፡ እንጂ፡ በኦሪት፡ ደግሞ፡ እንደ፡ተጻፈ። *፩፡ ጢሞ፡ ፪፡ ፲፪፡፡ †ም፡ ፲፩፡ ፫፡፡ ኤፌ፡ ፭፡ ፳፪፡፡ ቆል፡ ፫፡ ፲፰፡፡ ቲቶ፡ ፪፡ ፭፡፡ ዘፍ፡ ፫፡ ፲፮፡፡

፴፭፡ ምንም፡ ይማሩ፡ዘንድ፡ ቢወዱ፡ ባሎቻቸውን፡ ይጠይቁ፡ በቤታቸው፡ በሴቶች፡ ነውር፡ነውና፡ በቤተ፡ ክርስቲያን፡ ይናገሩ፡ ዘንድ።

፴፮፡ የእግዚአብሔር፡ ነገር፡ ከላንትን፡ወጣ፡ ወይስ፡ ወደላንት፡ ብቻን፡ ደረሰ።

፴፯፡ ከላንት፡ አንዱ፡ ነቢይ፡ እንደ፡ ሁነ፡ ቢመስለው፡ ወይም፡ መንፈሳዊ፡ ይህነን፡ የጻፍሁላችሁን፡ ትእዛዝ፡ ይወቅ፡ የጌታችን፡ ትእዛዝ፡ ነውና። ፩፡ ዮሐ፡ ፬፡ ፮፡፡

፴፰፡ የማያውቅም፡ ቢኖር፡ አይወቅ።

፴፱፡ እንግዲህ፡ ወንድሞቼ፡ ሆይ፡ ቅኑ፡ ትንቢት፡ እንድትናገሩ፡ በልሳንም፡ መናገር፡ አትከልክሉ።

፵፡ የምታደርጉት፡ ሁሉ፡ ባገባብ፡ *በሥርዓትም፡ ይሁን። *ቆል፡ ፪፡ ፭፡፡

## ምዕራፍ፡ ፲፭፡

፩፡ እነግራችሁማለሁ፡ወንድሞቼ፡ሆይ፡*ያስተማርኋችሁ፡ ወንጌል፡ የተቀበላችሁት፡በርሱም፡ የጸናችሁበት። *ገላት፡ ፩፡ ፲፩፡ ፲፪፡፡

፪፡ በርሱም፡ ትድናላችሁ፡ በምን፡ ነገር፡ *አስተማርኋችሁ፡ ታስቡት፡ እንደ፡ ሆነ፡ በከንቱ፡ ያመናችሁ፡ ባትሆኑ። *ም፡ ፩፡ ፳፩፡፡

፫፡ አስቀድሞ፡ ሰጥቻችኋለሁና፡ እኔ፡ ደግሞ፡ የተቀበልሁትን። ክርስቶስ፡ ስለ፡ ኃጢአታችን፡ እንደ፡ ሞተ፡ እንደ፡ *ተጻፈ። *ኢሳ፡ ፶፫፡ ፰፡ ፱፡፡

፬፡ እንደ፡ ተቀበረም፡ በሦስተኛም፡ቀን፡ እንደ፡ ተነሣ፡ እንደ፡ *ተጻፈ። *መዝ፡ ፲፮፡ ፲፡፡

፭፡ እርሱም፡ *ለጴጥሮስ፡ እንደ፡ ታየ። በኋላም፡ †ላሥራ፡ ሁለቱ፡ ሐዋርያት። *ሉቃ፡ ፳፬፡ ፴፬፡፡ †ማር፡ ፲፮፡ ፲፬፡፡

፮፡ ከዚያም፡ በኋላ፡ ካምስት፡ መቶ፡ለሚበልጡ፡ ወንድሞች፡ ባንድ፡ ጊዜ፡ ተገለጠ። ከለዚህም፡የሚበልጡት፡ እስከ፡ ዛሬ፡ አሉ፡ ከርሳቸውም፡ደግሞ፡ ሰዎች፡ ተኝተዋል።

፯፡ ከዚያም፡ በኋላ፡ ለያዕቆብ፡ተገለጠ፡በኋላም፡ *ለሐዋርያት፡ ሁሉ። *ሉቃ፡ ፳፬፡ ፶፡፡

፰፡ ከርሳቸውም፡ ሁሉ፡ በኋላ፡ ለኔ፡ ደግሞ፡ ታየ፡ ለኔ፡ ጭንጋፍ፡ ለምመሰል። የሐዋ፡ ፱፡ ፭፡፡

፱፡ እኔ፡ከሐዋርያት፡ *አንሳለሁና፡የማይገባኝ፡ ሐዋርያ፡ እባል፡ ዘንድ፡ የእግዚአብሔርን፡ ቤተ፡ ክርስቲያን፡ ስላሳደድሁ። *ኤፌ፡ ፫፡ ፰፡፡

፲፡ በእግዚአብሔር፡ ጸጋ፡ ግን፡ የሆንሁት፡ ነኝ። ጸጋውም፡ በኔ፡ ያለችው፡ ከንቱ፡ አልነበረችም፡ነገር፡ግን፡ እኔ፡ ደከምሁ፡ ከሁሉ፡ይልቅ። እኔም፡አይደለሁም፡ ከኔ፡ ጋራ፡ ያለችው፡ የእግዚአብሔር፡ ጸጋ፡ እንጂ። ፪፡ቆሮ፡ ፲፩፡ ፳፫፡፡

፲፩፡ እኔም፡ብሆን፡እርሳቸውም፡ቢሆኑ። እንዲሁ፡ እናስተምራለን፡ እንዲሁም፡ እላንተ፡ አመናችሁ።

፲፪፡ ክርስቶስ፡ ግን፡ ከሙታን፡ ተነሣ፡ ብለን፡ ካስተማርን። እንደ፡ ምን፡ ከላንተ፡ ወገን፡ሰዎች፡ይላሉ፡ ትንሣኤ፡ ሙታን፡ የለም።

፲፫፡ ትንሣኤ፡ ሙታንስ፡ ከሌለ፡ ክርስቶስም፡ አልተነሣም።

፲፬፡ ክርስቶስም፡ ካልተነሣ፡ ማስተማራችን፡ እንኪያስ፡ ዝምብሎ፡ ነው፡ ማመናችሁም፡ ደግሞ፡ምናምምን፡ ነው።

፲፭፡ እኛም፡ ደግሞ፡ በእግዚአብሔር፡ ያሰት፡ ምስክሮች፡ ሁነን፡ ተገኘን። በእግዚአብሔር፡ መስክረናልና፡ ክርስቶስን፡ እንደሰነሣ። ያላስነሣውን፡ ሙታን፡ ባይነሡ። የሐዋ፡ ፫፡ ፲፭፡፡

፲፮፡ *ሙታን፡ ባይነሡ፡ ክርስቶስ፡ ደግሞ፡ አልተነሣምና። *ሮሜ፡ ፰፡ ፲፩፡፡

፲፯፡ ክርስቶስም፡ ካልተነሣ፡ ሃይማኖታችሁ፡ ከንቱ፡ ነው፡ እስከ፡ዛሬ፡ድረስ፡በኃጢአታችሁ፡አላችሁ።

፲፰፡ እንግዲህም፡ በክርስቶስ፡ የተኙ፡ ደግሞ፡ ፈጽመው፡ ጠፉ።

፲፱፡ በዚህ፡ ዓለም፡ ሕይወት፡ ብቻ፡ ክርስቶስን፡ ተስፋ፡ ብናደርገው፡ ከሰው፡ ሁሉ፡ ይልቅ፡ የተጠቃን፡ ሆን።

፳፡ አሁን፡ ግን፡ ክርስቶስ፡ ከሙታን፡ ተነሣ፡ ላንቀላፉትም፡ *መጀመርያ፡ ሆነ። *የሐዋ፡ ፳፮፡ ፳፫፡፡

፳፩፡ ሞትም፡ *በሰው፡ እንደ፡ ሆነች፡ እንዲሁም፡ ከሰው፡ የሙታን፡ ትንሣኤ፡ ሆነች። *ዘፍ፡ ፫፡ ፲፱፡፡ ሮሜ፡ ፭፡ ፲፪፡ ፲፰፡፡

፳፪፡ ሁሉ፡ በአዳም፡ እንደ፡ ሞቱ፡ እንዲሁም፡ በክርስቶስ፡ ሁሉ፡ *ሕያዋን፡ ይሆናሉና። *ሮሜ፡ ፭፡ ፳፩፡፡

፳፫፡ ነገር፡ ግን፡ ሰው፡ ሁሉ፡ በሥርዓቱ። ክርስቶስ፡ *አስቀድሞ፡ ነው። ከዚያም፡ በኋላ፡ †ለክርስቶስ፡ የሚሆኑ፡ እርሱ፡ በመጣ፡ ጊዜ። *፩፡ ተሰ፡ ፬፡ ፲፬፡፡ †ገላት፡ ፭፡ ፳፬፡፡

፳፬፡ በዚያን፡ ጊዜም፡ ፍጻሜ፡ ይሆናል፡ መንግሥቱን፡ ለእግዚአብሔር፡ አብ፡ አሳልፎ፡ በሰጠ፡ ጊዜ፡ አለቅነትን፡ ሁሉ፡ በሻረ፡ ጊዜ፡ መንግሥትንም፡ ሁሉ፡ ኃይልንም፡ ሁሉ።

፳፭፡ ይነግሥ፡ ዘንድ፡ *አለውና፡ ጸላቶቹን፡ ሁሉ፡ ከግሩ፡ በታች፡ እስኪጥል፡ ድረስ። *ማቴ፡ ፳፪፡ ፵፬፡፡

፳፮፡ የኋለኛው፡ ጸላት፡ የሚሻረው፡ ሞት፡ ነው። ራእ፡ ፳፡ ፲፬፡፡ ፳፩፡ ፬፡፡

፳፯፡ ሁሉን፡ *ከግሩ፡ በታች፡ አስገዝቶታልና። ባለም፡ ጊዜ፡ †ሁሉ፡ እንደ፡ ተገዛለት፡ የተገለጠ፡ ነው፡ ሁሉን፡ ለርሱ፡ ካስገዛለት፡ በቀር፡ እንደለ። *መዝ፡ ፰፡ ፯፡፡ †ማቴ፡ ፲፩፡ ፳፯፡፡

፳፰፡ ሁሉም፡ በተገዛለት፡ ጊዜ፡ የዚያን፡ ጊዜም፡ ልጁ፡ ይገዛል፡ እርሱ፡ ደግሞ፡ ሁሉን፡ ላስገዛለት። እግዚአብሔር፡ ይሆን፡ ዘንድ፡ ሁሉን፡ በሁሉ።

፳፱፡ እንኪያ፡ ምን፡ ያደርጋሉ፡ በጥምቀት፡ የሚጠመቁ፡ ስለ፡ ሙታን። ሙታን፡ ባይነሡ፡ ስለ፡ ምን፡ ነው፡ መጠመቃቸው፡ ስለ፡ ሙታን።

፴፡ ለምንስ፡ ሁልጊዜ፡ መከራ፡ እንቀበላለን። ሮሜ፡ ፰፡ ፴፮፡፡

፴፩፡ በየሱስ፡ ክርስቶስ፡ በጌታችን፡ ካለኝ፡ *ትምክህታችን፡ ወንድሞቼ፡ ሆይ፡ ዕለት፡ ዕለት፡ እሞታለሁ። *፩፡ ተሰ፡ ፪፡ ፲፱፡፡ ፪፡ ቆሮ፡ ፬፡ ፲፡ ፲፩፡፡

፴፪፡ እንደ፡ ሰው፡ ካራዊት፡ ጋራ፡ በኤፌሶን፡ ከተጋደልሁ፡ በዚያ፡ ምን፡ እጠቀማለሁ፡ ሙታን፡ *ባይነሡ። እንብላና፡ እንጠጣ፡ ነገ፡እንሞታለንና። *ኢሳ፡ ፳፪፡ ፲፫፡፡ ፶፮፡ ፲፪፡፡

፴፫፡ *አትሳቱ፡ክፉ፡ ጨወታ፡ መልካሙን፡ አካሔድ፡ ያጠፋልና። *ኤፌ፡ ፭፡ ፮፡፡

፴፬፡ ልባችሁ፡ *ለጽድቅ፡ አስነሡ፡ አትበድሉም፡ ከላንት፡ እግዚአብሔርን፡ የማያውቁ፡አሉና። ይህነንም፡ ማለቴ፡ †ስገሠጻችሁ፡ ነኝ። *ሮሜ፡ ፲፫፡ ፲፩፡፡ †ም፡ ፮፡ ፭፡፡

፴፭፡ ነገር፡ ግን፡ ከላንት፡ ሰው፡ይላል፡ ሙታን፡ እንዴት፡ ይነሣሉ፡ በምንስ፡ ሥጋ፡ ይመጣሉ። ሕዝ፡ ፴፯፡ ፫፡፡

፴፮፡ አንተ፡ ሰነፍ። አንተ፡ የምትዘራው፡ሕያው፡ አይሆንም፡ *ካልሞተ። *ዮሐ፡ ፲፪፡ ፳፬፡፡

፴፯፡ ያም፡ የምትዘራው፡ ዘር፡ የሚሆነው፡ ሥጋ፡

አይደለም፡ነገር፡ግን፡ ዘር፡ብቻ፡ነው፡ የስንዴ፡ ወይም፡ የገብስ፡ ወይም፡ የማናቸውም፡ ዘር፡ ቢሆን።

፴፰፤ እግዚአብሔር፡ ግን፡ ሥጋ፡ ያደርግለታል፡ እን ደ፡ ወደደ፡ለሁሉም፡ኢያንዳንዱ፡ *ሥጋውን፡ ይሰጠ ዋል። *ዘፍ፡ ፩፡ ፲፩።

፴፱፤ ሥጋም፡ ሁሉ፡ አንድ፡አይደለም፡የሰው። ሥ ጋ፡ ሌላ፡ ነውና። የእንስሳም፡ ሥጋ፡ሌላ፡ነው፡ያሣም፡ ሥጋ፡ ሌላ፡ ነው፡ የወፎም፡ ሥጋ፡ ልዩ፡ ነው።

፵፤ የሰማይም፡ ወገን፡ ሥጋ፡ አለ፡ የምድርም፡ ወ ገን፡ ሥጋ። ነገር፡ ግን፡ የሰማይ፡ ወገን፡ ክብራቸው፡ ሌ ላ፡ ነው፡ የምድርም፡ ወገን፡ ክብር፡ ሌላ።

፵፩፤ የጸሐይ፡ ክብር፡ ሌላ፡ነው። የጨረቃም፡ ክብ ር፡ ሌላ። የከዋክብትም፡ ክብራቸው፡ ሌላ፡ ነው። ኮ ከብም፡ ከኮከብ፡ በክብር፡ ይበልጣል።

፵፪፤ እንዲሁም፡የሙታን፡ ትንሣኤ፡ናት። በጥፋ ት፡ ይዘራል፡ ባለ፡ ጥፋት፡ ይነሣል።

፵፫፤ባለመክበር፡ይዘራል፡በክብርም፡ይነሣል። በድ ካም፡ይዘራል።በኃይልም፡ይነሣል። ፊል፡፫፡፳፡፳፩።

፵፬፤ መሬታዊ፡ ሥጋ፡ ይዘራል፡ መንፈሳዊ፡ ሥጋ፡ ይነሣል። መሬታዊ፡ ሥጋ፡ አለ፡ መንፈሳዊም፡ ሥጋ፡ አለ።

፵፭፤ እንዲሁም፡ደግሞ፡ *ተጽፎዋል። አደም፡ የ ፊተኛው፡ ሰው፡ በነፍስ፡ ሕያው፡ ሆነ። ሁለተኛው፡ አደም፡ የሚያድን፡ †መንፈስ፡ ነው።

*ዘፍ፡ ፪፡ ፯። †፪፡ ቆሮ፡ ፫፡ ፲፯።

፵፮፤ የፊተኛው፡ ግን፡ መንፈሳዊ፡ አይደለም፡ነፍ ሳዊ፡ ነበረ፡ እንጂ። ከዚያም፡ በኋላ፡ መንፈሳዊ።

፵፯፤ የፊተኛው፡ ሰው፡ መሬታዊ፡ነው፡ከምድር። ሁለተኛው፡ ሰው፡ ጌታ፡ ከሰማይ።

፵፰፤ እንደ፡ መሬታዊም፡ እንዲሁም፡ መሬታው ያን፡ ናቸው። እንደ፡ ሰማያዊም፡ እንዲሁ፡ ደግሞ፡ ሰማያውያን፡ ናቸው።

፵፱፤ የዚያነንም፡ የመሬታዊ፡ መልክ፡ እንደ፡ ለበ ስነ። እንዲሁም፡ የዚያን፡ የሰማያዊ፡ መልክ፡ እንለ ብሳለን።

፶፤ ይህነንም፡ እላለሁ፡ ወንድሞቼ፡ሆይ። *ሥጋና፡ ደም፡ የሰማይን፡ መንግሥት፡ ይወርሰ፡ ዘንድ፡ አንዳ ይችል።የሚጠፋም፡የማይጠፋውን፡አይወርስም።

*ማቴ፡ ፲፮፡ ፲፯። ዮሐ፡ ፩፡ ፲፫።

፶፩፤ እነሆ፡ በምሥጢር፡ እነግራችኋለሁ። እኛ፡ ሁ ላችን፡ *እንደንትኛ፡ ነገር፡ ግን፡ ሁላችን፡ እንለወጣ ለን። *፩፡ ተሰ፡ ፬፡ ፲፭።

፶፪፤ ድንገት፡ እንደ፡ ቅጽበት፡ ዓይን፡ የኋለኛው፡ *መለከት፡ በተነፋ፡ ጊዜ። መለከት፡ ይነፋልና፡ ሙታ ንም፡ ያለ፡ ጥፋት፡ ይነሣሉ፡ እኛም፡ እንለወጣለን።

*ማቴ፡ ፳፬፡ ፴፩። ፩፡ ተሰ፡ ፬፡ ፲፮።

፶፫፤ ይህ፡ የሚጠፋው፡ የማይጠፋውን፡ይለብስ፡ ዘንድ፡ አለውና፡ ይህም፡ የሚሞተው፡ የማይሞተ ውን፡ ይለብስ፡ ዘንድ፡ አለው። ፪፡ ቆሮ፡ ፭፡ ፬።

፶፬፤ ይህም፡ የሚጠፋው፡ የማይጠፋውን፡ በለበ ሰ፡ ጊዜ፡ ይህም፡ የሚሞተው፡የማይሞተውን፡ በለ በሰ፡ ጊዜ፡ የዚያን፡ ጊዜ፡ ይፈጸማል፡ *የተጻፈው፡ ነገ ር። ሞት፡ በማሸነፍ፡ ተዋጠ። *ኢሳ፡ ፳፭፡ ፰።

፶፭፤ የታለ፡ ሞት፡ መውጊያህ፡ ሆይ። ማሸነፍህስ፡ የታለ፡ ሲኦል፡ ሆይ። ሆሴ፡ ፲፫፡ ፲፬።

፶፮፤ የሞት፡ መውጊያ፡ ኃጢአት፡ ነው፡ የኃጢአትም፡ ኃ ይል፡ ኦሪት፡ ናት። ሮሜ፡ ፯፡ ፲፫። ፮፡ ፲፬።

፶፯፤ ነገር፡ ግን፡ እግዚአብሔር፡ ምስጋና፡ ይድረሰ ው፡ ማሸነፍ፡ የሰጠነ፡ በጌታችን፡ በየሱስ፡ ክርስቶስ።

፶፰፤ ስለዚህም፡ወንድሞቼ፡ሆይ፡የተወደዳችሁ፡ የጸናችሁ፡ ሁኑ፡ ሳትናወጡ። የተረፋችሁም፡ ሁኑ፡ የ ጌታን፡ ስራ፡ በመስራት፡ ሁለግዜ። አውቃችሁ፡ ድካ ማችሁ፡ *በከንቱ፡ እንዲይደለ፡ በጌታ፡ ዘንድ።

*፪፡ ዜና፡ ፲፭፡ ፯።

## ምዕራፍ፡ ፲፮፡

፩፤ ለቅዱሳን፡ ስለሚሰበሰበው፡ *መቀራመጥ፡ ግ ን፡ ለገላትያ፡ አብያተ፡ ክርስቲያናት፡እንደ፡ ሠራሁ፡ እላንትም፡ እንዲሁ፡ አድርጉ። *የሐዋ፡ ፲፩፡ ፳፱።

፪፡ ቆሮ፡ ም፡ ፰፡ ና፡ ፱፡ ገላት፡ ፪፡ ፲።

፪፤ በሳምንት፡ በሳምንት፡ *በመጀመርያው፡ ቀን፡ ሁሉ፡ እላንት፡ ሁላችሁ፡ አከማቹ፡ ኢያንዳንዱም፡ ከርሱ፡ ዘንድ፡ ያኑር፡ እንደ፡ ተቻለው። ገና፡ እንዳያ ከማቹ፡ እኔ፡ ወደላንት፡ ስመጣ። *የሐዋ፡ ፳፡ ፯።

፫፤ በመጣሁም፡ ጊዜ፡ የመረጣችኋቸውን፡ እርሳ ቸውን፡ በጽፈት፡ እስደቸዋለሁ፡ ምጽዋታችሁን፡ ወ ደ፡ የሩሳሌም፡ ያደርሱ፡ ዘንድ።

፬፤ እኔም፡ ደግሞ፡ እሔድ፡ ዘንድ፡ ነገሩ፡ ቢቀናኝ፡ ከኔ፡ ጋራ፡ ይሔዳሉ።

፭፤ ወደላንት፡ ግን፡ እመጣለሁ፡ ወደ፡ መቄደንያ፡ ባለፍሁ፡ ጊዜ፡ በመቄደንያ፡ እዘራለሁና።

የሐዋ፡ ፲፱፡ ፳፩።

፮፤ በላንትም፡ ዘንድ፡ እቆይ፡ ወይም፡ እከርም፡ እንደሆን። እላንት፡ ወደ፡ ወደድሁት፡ ስፍራ፡ ትሸኙ ኝ፡ ዘንድ። ሮሜ፡ ፲፭፡ ፳፬።

፯፤ አሁን፡ ሳልፍ፡ ብቻ፡ አያችሁ፡ ዘንድ፡ አልወድ ምና፡ ከላንት፡ ዘንድ፡ ለመቀመጥ፡ ተስፋ፡ አደርጋለ ሁ፡ እንጂ፡ የሆነን፡ ያህል። ያነን፡እግዚአብሔር፡ቢወ ደው። የሐዋ፡ ፲፰፡ ፳፩።

፰፤ *በኤፌሶን፡ ግን፡ እቀመጣለሁ፡ እስከ፡ ጰንጠ ቆስጤ፡ ድረስ። *የሐዋ፡ ፲፱፡ ፩፡ ፲።

፱፤ ታላቅ፡ ደጅ፡ ተከፍቶልኛልና፡ስራ፡ *የመላበት፡ ቦደረኞችም፡ እጅግ፡ ናቸው። *፪፡ ቆሮ፡ ፪፡ ፲፪።

ቆላ፡ ፬፡ ፫። ራእ፡ ፫፡ ፰።

፲፤ ጢሞቴዎስ፡ ግን፡ ቢመጣ፡ተመልከቱ፡በላንት፡ ዘንድ፡ እንዲሆን፡ ያለ፡ ፍርሃት። *እርሱም፡ ደግሞ፡ የጌታን፡ ስራ፡ እንደኔ፡ ያደርጋልና። *ፊል፡ ፪፡ ፳።

፲፩፤ እንጊዲህ፡ ማንም፡ አያቃለው፡ በደህና፡ ስደ

ዴት፡ እንጂ፡ ወደኔ፡ ይመጣ፡ ዘንድ፡ ከወንድሞች፡ ጋራ፡ እጠብቀዋለሁና።
ቍ፡ ፮ ፤

፲፪፡ አጵሎስን፡ ወንድሜን፡ ግን፡ እጅግ፡ ለመንሁት፡ ወደላንት፡ ይሔድ፡ ዘንድ፡ ከወንድሞች፡ ጋራ። ከቶ፡ ፈቃዲ፡ አልነበረም፡ አሁን፡ ሊመጣ፡ ነገር፡ ግን፡ ይመጣል፡ በተቻለው፡ ጊዜ።

፲፫፡ *ንቁ፡ በሃይማኖት፡ ቁሙ፡ ጐልምሱ፡ ጠንክሩም። *ም፡ ፲፭፡ ፶፰፡፡ ማቴ፡ ፳፬፡ ፵፪፡፡ ና፡ ፳፭፡ ፲፫፡፡

፲፬፡ ነገራችሁ፡ ሁሉ፡ በፍቅር፡ ይሁን።

፲፭፡ እለምናችሁማለሁ፡ ወንድሞቼ፡ ሆይ። *የስጢፋናን፡ ቤት፡ አውቃችኋል፡ የአካይያ፡ *መጀመርያ፡ እንደሆነ፡ ራሳቸውንም፡ እንደሠሩ፡ ቅዱሳንን፡ ለማገልገል።
*ም፡ ፩፡ ፲፮፡፡ †ሮሜ፡ ፲፮፡ ፭፡፡

፲፮፡ እላንተ፡ ትታዘዙ፡ ዘንድ፡ እንደለዚህ፡ላሉት፡ ከኛ፡ ጋራም፡ ለሚረዳ፡ለሚደክምም፡ ሁሉ።
ፊል፡ ፪፡ ፳፱፡፡

፲፯፡ እኔም፡ደስ፡ይለኛል፡በእስጢፋና፡መምጣት፡ በፈርጡናጦስም፡በአካይቆስም። ከላንት፡ የጐደለውን፡እርሳቸው፡ ጨርሰዋልና።

፲፰፡ መንፈሴንና፡ መንፈሳችሁን፡ አሳርፈዋልና። እንግዴህም፡ *እንደለዚህ፡ ያሉትን፡ የምታውቁ፡ ሁኑ።
*፩፡ ተሰ፡ ፭፡ ፲፪፡፡

፲፱፡ የእስያ፡ ቤተ፡ክርስቲያናት፡ እንዴት፡ ናችሁ፡ ይልዋችኋል። *አኪላስና፡ ጵርስኪላ፡ እጅግ፡ እንዴት፡ ናችሁ፡ ይልዋችኋል፡ በእግዚአብሔር፡ በቤታቸው፡ ካለችው፡ ቤተ፡ ክርስቲያን፡ ጋራ።
*የሐዋ፡ ፲፰፡ ፪፡ ፲፰፡ ፳፮፡፡ ሮሜ፡ ፲፮፡ ፫፡፡

፳፡ ወንድሞች፡ ሁሉ፡ እንዴት፡ ናችሁ፡ ይልዋችኋል። እርሱ፡ በርሳችሁ፡ተገናኙ፡ በተቀደሰች፡መሳም።
ሮሜ፡ ፲፮፡ ፲፮፡፡ ፪፡ ቆሮ፡ ፲፫፡ ፲፪፡፡ ፩፡ ጴጥ፡ ፭፡ ፲፬፡፡

፳፩፡ ይህነን፡ሰላም፡ እኔ፡ በጄ፡ ጻፍሁት፡ እኔ፡ጳውሎስ።
ቀለ፡ ፬፡ ፲፰፡፡ ፪፡ ተሰ፡ ፫፡ ፲፯፡፡

፳፪፡ ጌታችነን፡ የሱስ፡ክርስቶስን፡ የማይወድ፡የተረገመ፡ ይሁን፡ ማራን፡ አታ፡(ጌታ፡ ይመጣል)።
ገላት፡ ፩፡ ፰፡፡

፳፫፡ የጌታችን፡ የየሱስ፡ ክርስቶስ፡ ጸጋ፡ ከላንት፡ ጋራ፡ ይሁን።
ሮሜ፡ ፲፮፡ ፳፬፡፡

፳፬፡ ፍቅሬ፡ ከላንት፡ ጋራ፡ ከሁላችሁ፡ ይሁን፡በክርስቶስ፡ የሱስ። አሜን።

ተፈጸመች፡ መጀመርያይቱ፡ መልእክት፡ ወደ፡ ቆሮንቶስ፡ ሰዎች። ተጻፈች፡ በፊልጵሰዩስ፡ አገር፡ ተላከችም፡ ከጢሞቴዎስ፡ ጋራ፡ ከፈርጡናጦስም፡ ከስጢፋናም፡ ከአካይቆስም፡ ጋራ።

# የሐዋርያው ፡ የጳውሎስ ፡ መልእክት ፡ ሁለተኛይቱ ፡ ወደ ፡ ቆሮንቶስ ፡ ሰዎች ።

ምዕራፍ፡ ፩፡

፩፡ ከጳውሎስ፡ ከየሱስ፡ ክርስቶስ፡ ሐዋርያ፡በእግዚአብሔር፡*ፈቃድ። ከወንድምም፡ከጢሞቴዎስ። በቆሮንቶስ፡ ወደለች፡ ወደ፡እግዚአብሔር፡ ቤተ፡ክርስቲያን፡በአካይያ፡አገር፡ ሁሉ፡ ከሚኖሩ፡ከቅዱሳን፡ ሁሉ፡ ጋራ።
*፩፡ ቆሮ፡ ፩፡ ፩፡፡

፪፡ ጸጋ፡ ይሁንላችሁ፡ ሰላምም፡ ካባታችን፡ ካምላክ፡ ከጌታም፡ ከየሱስ፡ ክርስቶስ።
ሮሜ፡ ፩፡ ፯፡፡

፫፡ እግዚአብሔር፡ ይመስገን፡ የጌታችን፡ የየሱስ፡ ክርስቶስ፡ አባት፡ የምህረት፡ አባት፡ *የደስታም፡ ሁሉ፡ አምላክ።
*ሮሜ፡ ፲፭፡ ፭፡፡

፬፡ ደስ፡የሚያሰኘን፡በመከራችን፡ሁሉ። ባዘን፡ ሁሉ፡ ያሉትን፡ ደስ፡ ልናሰኝ፡ እንችል፡ ዘንድ፡ እኛ፡ ደስ፡ በሚለን፡ ደስታ፡ ከእግዚአብሔር፡ ዘንድ።

፭፡ የክርስቶስም፡ ሕማም፡ እንደ፡ በዛብን፡ መጠን፡ እንደሁ፡ ደግሞ፡ ደስታችን፡ በክርስቶስ፡ ይበዛል።
መዝ፡ ፴፬፡ ፳፡፡ ፺፬፡ ፲፱፡፡

፮፡ ብንሳደድም፡ ስለ፡ ደስታችሁ፡ ስለ፡ *ደህንነታችሁም፡ እንሳደደለንና። ደስ፡ ቢለነም፡ ያም፡ እላንትን፡ ደስ፡ ይላችሁ፡ ዘንድ፡ነው። ትዕግሥት፡በላንት፡ ይሆን፡ ዘንድ፡ መከራ፡ ለመቀበል፡ እኛም፡ ደግሞ፡ የምንቀበላት።
*ም፡ ፬፡ ፲፭፡ ፲፯፡፡

፯፡ ስለላንትም፡ ተስፋችን፡ጽኑ፡ነው፡ እናውቃለንና፡ የመከራና፡ የሐዘን፡ ተካፋዮች፡እንደ፡ሆናችሁ፡ እንደሁም፡ የደስታ፡ ተካፋዮች፡ ናችሁ።

፰፡ እወደለሁም፡ ወንድሞቼ፡ ሆይ፡ በእስያ፡ ያገኘነን፡ *መከራ፡ ታውቁ፡ ዘንድ። ያለ፡ ልክ፡ እንደተጨነቅነ፡ ከምንችለው፡የሚበዛ። ሕይወታችን፡ ለመጥፋት፡ እስክትደርስ፡ ድረስ።
*የሐዋ፡ ፲፱፡ ፳፫፡፡

፱፡ ለሞትም፡ ፈረድነብነ፡ በሰውነታችን፡ ላይ፡ በራሳችን፡ እንዳንታመን፡በእግዚአብሔር፡እንጂ፡ ሙታን፡ የሚያስነሣ።

፲፡ እንዲህ፡ ካለው፡ ሞት፡ ያደነ የሚያድነንም፡ እኛም፡ ተስፋ፡ እናደርጋለን፡ ደግሞ፡ *እንዲያድነነ፡ እላንትም፡ በጸሎት፡ አብራችሁ፡ ስትረዱነ።
*፪፡ ጢሞ፡ ፬፡ ፲፰፡፡

፲፩፡ ስጥወታው፡ ለኛ፡የተሰጠ፡ለብዙ፡ ሰዎች፡ጸጋ፡ ትሆን፡ ዘንድ፡ በኛ፡ ምክንያትም፡ብዙ፡ሰዎች፡ ያመሰግኑ፡ ዘንድ።

፲፪፡ ይህ፡ትምክሕታችን፡ነውና፡ያሳባችን፡*ምስክር። በልባችን፡ †የውሃት፡ በእግዚአብሔርም፡ ንጽሕና፡እንደ፡ሔድነ፡በዓለም፡ከዚያም፡የሚበልጥ፡በላንት፡ዘንድ። በሥጋዊ፡ጥበብም፡ አይደለም፡ በእግዚአብሔር፡ጸጋ፡እንጂ።
*ዕብ፡ ፲፫፡ ፲፰፡፡ †ማቴ፡ ፲፡ ፲፮፡፡

፲፫፤ በሌላም፡ ነገር፡ የምንጽፋላችሁ፡አይደለነም፡
እላነት፡ ካነበባችሁት፡ በቀር፡ ከኛ፡በምታውቁት፡ እ
ንጂ። እኔም፡ ተስፋ፡ አደርጋለሁ፡ ያነን፡ እስከ፡ ፍጻ
ሜ፡ እንድታውቁ።
፲፬፤ ዛሬ፡እንደወቃችሁኅ፡ከፋላችሁ። እኛ፡ *ትም
ክሕታችሁ፡ እንደሆነ፡ እላንትም፡ ደግሞ፡ ትምክሕ
ታችን፡ እንደ፡ ሆናችሁ፡ በየሱስ፡ በጌታችን፡ ቀን።
*ም፡ ፭፤ ፲፪፡፡
፲፭፤ በዚህም፡ ተስፋ፡እወድ፡ ነበርሁ፡አስቀድሜ፡
ወደላንት፡ እመጣ፡ ዘንድ፡ ዕጽፍ፡ ጸጋ፡ ትወስዱ፡ ዘ
ንድ።
፲፮፤ ወደ፡ መቄደንያም፡ በላንት፡መካከል፡አልፍ፡
ዘንድ። ደግሞም፡ከመቄደንያ፡ወደላንት፡እመለስ፡
ዘንድ፡ ወደ፡ ይሁዳ፡ ምድርም፡ ትሸኙኝ፡ ዘንድ።
፲፯፤ ይህችም፡ነገር፡በቅሌት፡ያሰብኋት፡ናትን። ወ
ይስ፡ይህ፡የማስበው፡የሥጋን፡ምክር፡ ነው፡ ከኔ፡ ይሆ
ን፡ ዘንድ፡ አዎን፡ አዎን። አይደለም፡ አይደለም።
፲፰፤ እግዚአብሔር፡ *እውነተኛ፡ ነው፡ ለላንት፡ የነ
ገርናችሁ፡ ነገር፡ እንደልሆነ፡ አዎን፡ አይደለምም።
*፩፤ ቆሮ፡ ፩፤ ፱፡፡
፲፱፤ የእግዚአብሔር፡ ልጅ፡ የሱስ፡ክርስቶስ፡ ከኛ፡
የተሰበከላችሁ። ከኔ፡ ከጳውሎስ፡ ከስልዋኖስም፡ ከ
ጢሞቴዎስም። አዎን፡ አይደለምም፡አልሆነም፡ነገ
ር፡ ግን፡ አዎን፡ ተደረገበት።
፳፤ የእግዚአብሔር፡ ተስፋ፡ ሁሉ፡ በርሱ፡ እውነተ
ኛ፡ ሁኖለችና፡ በርሱም፡ አዎን፡ አሜንም፡ ተብላለች
ና፡ ለእግዚአብሔር፡ ምስጋና፡ በኛ። ራእ፡ ፫፤ ፲፬፡፡
፳፩፤ እግዚአብሔር፡ የሚያጸናን፡ ከላንት፡ ጋራ፡ በ
ክርስቶስ፡ ሃይማኖት፡ *የቀባነም፡ እርሱ፡ ነው።
*፩፤ ዮሐ፡ ፪፤ ፳፯፡፡
፳፪፤ እርሱም፡ ደግሞ፡ አተመነ፡ የመንፈሱንም፡
መያዣ፡ በልባችን፡ ሰጠነ። ም፡ ፭፤ ፭፡፡
ሮሜ፡ ፰፤ ፲፮፡፡ ኤፌ፡ ፩፤ ፲፬፡፡
፳፫፤ እኔ፡ ግን፡ እግዚአብሔርን፡ *ምስክር፡ በሰው
ነቴ፡ ላይ፡ እጸራለሁ፡ አዝኜላችሁ፡ ወደ፡ ቆሮንቶስ፡
ግና፡እንደልመጣሁ። *ም፡ ፲፩፤ ፴፩፡፡ ሮሜ፡ ፩፤ ፱፡፡
፳፬፤ ሃይማኖታችሁን፡ *የምንገዛው፡ ሁነን፡አይደ
ለነምና፡ ነገር፡ ግን፡ ደስታችሁን፡ እንራደላን፡በሃይማ
ኖት፡ ጸንታችኋልና። *፩፤ ጴጥ፡ ፭፤ ፫፡፡

## ምዕራፍ፡ ፪፤

፩፡ ይህነንም፡ በራሴ፡ ፈረድሁ፡ ደግሞ፡ወደላንት፡
እንደልመጣ፡ በኀዘን።
፪፤ እኔም፡ አሳዝኛችሁ፡ እንደ፡ ሆንሁ፡ ማነው፡ ደ
ስ፡ የሚያሰኘኝ፡ ከዚያ፡ እኔ፡ ካሳዘንሁቱ፡ በቀር።
፫፤ እኔም፡ ይህነን፡ *ጻፍሁላችሁ። በመጣሁ፡ ጊዜ፡
አዘን፡ እንደያገኘኝ። ከርሳቸው፡ ደስ፡ ያሰኙኝ፡ዘን
ድ፡ ከሚገባኝ፡ ሰዎች። እኔም፡ በላንት፡ ለሁላችሁ፡
ደስታ፡ እንደ፡ሆን። *ም፡ ፲፪፤ ፳፩፡፡

፬፤ ከብዙ፡ ኀዘን፡ ከልብ፡ ጭንቀት፡ የተነሣም፡ ጽ
ፈላችኋለሁና፡ በንብ፡ ብዛት። ልታዝኑ፡ አይደለው
ም። ልታውቁ፡ነው፡እንጂ፡ እኔ፡ የምወዳችሁን፡ መ
ውደድ፡ ብዙ፡ እንደ፡ ሆነ።
፭፤ አንድ፡ሰውም፡ ቢያሳዝነኝ፡ እኔን፡ ያሳዘነ፡ አይ
ደለም፡ ከጥቂቱ፡ በቀር፡ ሁላችሁን፡ እንደልከብደ
ችሁ። ፩፤ ቆሮ፡ ፭፤ ፩፡፡
፮፤ እንደዚህ፡ ላለው፡ ይህች፡ ተግሣጽ፡ ትበቃዋለ
ች፡ ብዙ፡ ሰዎች፡ የገሠጹባት።
፯፡ አሁንም፡ሌላ፡ ነገር፡ደገባችኋል፡ ይቅር፡ትሉት፡
ዘንድ፡ታጽናኑትም፡ ዘንድ፡ ምናልባት፡በዚህ፡ ነገር፡ ያ
ለው፡ ሰው፡ እንደ፡ይጠፋ፡ ከብዙ፡ ኀዘን፡ የተነሣ።
፰፤ ስለዚህም፡ እለምናችኋለሁ፡ ፍቅራችሁን፡
ታጸኑለት፡ ዘንድ።
፱፤ ስለዚህ፡ደግሞ፡ጽፈላችኋለሁና፡እፈትናችሁ፡
ዘንድ፡ በነገሩ፡ ሁሉ፡ *ትታዘዙኝ፡ እንደሆን።
*ም፡ ፯፤ ፲፮፡፡
፲፤ ኀጢአቱንም፡እላንት፡ይቅር፡ያላችሁትን፡ እኔ፡
ደግሞ፡ ይቅር፡ እላለሁ። እኔም፡ ይቅር፡ ያልሁትን፡ስ
ላላንት፡ ይቅር፡ አልሁ፡ *በክርስቶስ፡ ፊት።
*ሉቃ፡ ፲፤ ፲፮፡፡
፲፩፤ *ሰይጣን፡ እንዳይገለጠን፡ ማገበሉን፡ እናው
ቃለንና። *ሉቃ፡ ፳፪፡ ፴፩፡፡
፲፪፤ ወደ፡*አጥራዋስም፡በመጣሁ፡ጊዜ፡ ለክርስቶ
ስ፡ ወንጌል፡ †ደጁም፡ በተከፈተልኝ፡ ጊዜ፡ በጌታ።
*የሐዋ፡ ፳፤ ፮፡፡ †የሐዋ፡ ፲፬፤ ፳፯፡፡ ፩፤ ቆሮ፡ ፲፮፤ ፱፡፡
፲፫፤ ለነፍሴ፡ዕረፍት፡አላገኘሁም፡ ቲቶስን፡ ወንድ
ሜን፡ ባላገኘው፡ ነገር፡ ግን፡ ትቻቸው፡ ወደ፡ መቄደን
ያ፡ወጣሁ።
፲፬፤ ለእግዚአብሔርም፡ምስጋና፡ይሁን፡ሁለግዜ፡
ድል፡ የሚያስነሣነ፡ በክርስቶስ። የውቀትንም፡ ሽታ፡
በየስፍራው፡ የሚገልጥብነ።
፲፭፤ እኛ፡ የክርስቶስ፡ ሽቱ፡ ነንና፡ ለእግዚአብሔር፡
*በሚድኑት፡ በሚጠፉትም። *፩፤ ቆሮ፡ ፩፤ ፲፰፡፡
፲፮፤ ለሚጠፉት፡የሞት፡ሽታ፡ለሞት።ለሚድኑት
ም፡ የሕይወት፡ ሽታ፡ ለሕይወት። ይህነንስ፡ ነገር፡ መ
ፈጸም፡ የሚችል፡ *ማነው። *ም፡ ፫፤ ፭፤ ፮፡፡
ሉቃ፡ ፪፤ ፴፬፡፡
፲፯፤ የእግዚአብሔርን፡ ነገር፡ በሌላ፡ እንደሚቀላ
ቅሉ፡ እንደ፡ ብዙ፡ ሰዎች፡ አይደለነምና። ነገር፡ግን፡ በ
የውሃት፡ ከእግዚአብሔርም፡ ዘንድ፡ እንደ፡ መጣ፡
በእግዚአብሔር፡ ፊት፡ በክርስቶስ፡ እንናገራለን።
ም፡ ፩፤ ፲፪፡፡

## ምዕራፍ፡ ፫፤

፩፤ አሁንስ፡ ደግሞ፡ ራሳችነን፡ *እናመሰግንን፡ወይ
ስ፡እንደ፡ ሌሎች፡ እንሻዋለን፡ ሰዎች፡ስለኛ፡ ጽፈት፡
ይጽፉላችሁ፡ዘንድ። ወይስ፡ እላንት፡ ትጽፉልነ፡ ዘ
ንድ። *ም፡ ፭፤ ፲፪፡፡

፪፡ የኛ፡ጽፈት፡ግን፡ እላንት፡ ናችሁ፡ በልባችን፡ የተ
ጻፋችሁ። እርሱም፡ የታወቀ፡ነው፡ ከሁሉም፡ ይነበባ
ል። ፩፡ ቆሮ፡ ፱፡ ፪።

፫፡ እላንትም፡የታወቃችሁ፡ ናችሁ፡የክርስቶስ፡መ
ልእክት፡ እንደ፡ ሆናችሁ፡እኛ፡ልናወጣት፡ የተሾምነ፡
ያለ፡ ቀለም፡ የተጻፋች፡ በሕያው፡ በእግዚአብሔር፡
መንፈስ፡ እንጂ። *በደንጊያ፡ ጽላም፡ አይደለም፡ በ
ሥጋዊ፡ ጽላ፡ እንጂ፡ በልባችሁ። *ዘፀአ፡ ፳፬፡ ፲፪።

፬፡ እንደህም፡ ያለውን፡ ማመን፡ አለን፡ *በክርስ
ቶስ፡ ወደ፡ እግዚአብሔር። *ዮሐ፡ ፲፬፡ ፮።

፭፡ እንደችን፡ከራሳችን፡ እንደ፡ በግዛጀችን፡ እናስ
ብ፡ ዘንድ፡ የምንችል፡ አይደለነም። ኃይላችን፡ ከእግ
ዚአብሔር፡ነው፡እንጂ። ም፡ ፪፡ ፲፮።

፮፡ ላደ ሱ፡ ኪደን፡ እናገለግል፡ ዘንድ፡ ያስቻለነ፡ *በ
ፊደልም፡ ላለች፡ አይደለም፡ በመንፈስ፡ ላለች፡ እን
ጂ። ፊደል፡ ይገላልና፡ †መንፈስ፡ ግን፡ ሕያው፡ ያደር
ጋል። *ሮሜ፡ ፯፡ ፮። †ዮሐ፡ ፮፡ ፷፫።

፯፡ የሞትም፡መልእክት፡ በፊደላት፡ በደንጊያ፡ የ
ተቀረጸች፡የተመሰገነች፡ ከሆነች። የእሥራኤል፡ ልጆ
ች፡ *የሙሴን፡ ፊት፡ ማየት፡ እስኪሳናቸው፡ ድረስ፡
ስለዚያ፡ ስላለፈው፡ ስለ፡ፊቱ፡ ብርሃን።
*ዘፀአ፡ ፴፬፡ ፴።

፰፡ እንደ፡ ምን፡ የመንፈስ፡ መልእክት፡ ከርስዋ፡
በምስጋና፡ አትበልጥምን። ገላት፡ ፫፡ ፪፡ ፭።

፱፡ ለኩነኔ፡ መልእክት፡ ክብር፡ ከሆነች። እንዴት፡
እጅግ፡ *የጽድቅ፡ መልእክት፡ በክብር፡ ትመላለች።
*ሮሜ፡ ፩፡ ፲፯። ፫፡ ፳፩።

፲፡ የተመሰገነችው፡እንደልተመሰገነች፡ እስክትሆ
ን፡ድረስ። በዚያ፡ በብዙ፡ክብር፡ በመጠንዋት፡ ጊዜ።

፲፩፡ ያም፡ የጠፋው፡ የከበረ፡ ከሆነ፡ እንዴት፡ ጸን
ቶ፡ የሚኖረው፡ እጅግ፡ የከበረ፡ ይሆን።

፲፪፡ ይህም፡ተስፋ፡ ካለነ፡ በፊታችን፡ በታላቅ፡ ደስ
ታ፡ተገልጠን፡ እንናገራለን።

፲፫፡ እንደ፡ ሙሴም፡ አይደለም፡ ፊቱን፡ ይሸፍን፡
እንደ፡ነበረ። የእሥራኤል፡ልጆች፡ የዚያን፡የተሻረው
ን፡ፍጻሜ፡እንዳያዩ። ዘፀአ፡ ፴፬፡ ፴፫፡ ፴፭።

፲፬፡ ነገር፡ግን፡ልባቸው፡ታወረ። እስከ፡ ዛሬ፡ድረስ፡
ያ፡ያረጀው፡ ሥርዓት፡ በተነበበ፡ ጊዜ፡ መጋረጃው፡ ይ
ሠውራቸዋልና፡ አይገለጥላቸውምም፡ በክርስቶስ፡
እንዲሻር። ሮሜ፡ ፲፩፡ ፳፭።

፲፭፡ ነገር፡ግን፡እስከ፡ ዛሬ፡ የሙሴ፡መጽሐፍ፡ ሲየ
ተነበበ፡መጋረጃው፡ በልባቸው፡አለ።

፲፮፡ ወደ፡ጌታ፡ ግን፡ *በተመለሰ፡ጊዜ፡ መጋረጃው፡
ፈቀቅ፡ ይላል። ሮሜ፡ ፲፩፡ ፳፫፡ ፳፮።

፲፯፡ ነገር፡ግን፡ *ጌታ፡ መንፈስ፡ ነው፡ የጌታም፡መን
ፈስ፡ ካለበት፡ ዘንድ፡ ወደዚያ፡ አርነት፡ አለ።
*ዮሐ፡ ፬፡ ፳፬።

፲፰፡ እኛም፡ሁላችን፡ በተገለጠ፡ ፊት፡ የጌታችንን፡
ክብር፡ እናያለን፡ በማስተዋት፡ እንድናይ፡ ወደዚያ
ም፡ምሳሌ፡እንለወጣለን፡ ከክብር፡ወደ፡ ክብር፡ በጌ
ታ፡ መንፈስ።

## ምዕራፍ፡ ፬፡

፩፡ ስለዚህም፡ ይህች፡ *መልእክት፡ ተሰጥታናለች
ና፡ምህረትን፡ እንደ፡ †ተቀበልነ፡ አንደክምም።
*ም፡ ፫፡ ፮። †፩፡ ቆሮ፡ ፯፡ ፳፭።

፪፡ ነገር፡ግን፡ የተሰወረውን፡ ነውር፡ ከደነ፡ በተንኰ
ልም፡ አንሔድም፡ የእግዚአብሔርንም፡ነገር፡ *አንሸ
ነግልነም። ነገር፡ ግን፡ እውነቱን፡ በመግለጽ፡ ራሳችነን፡
ለሰው፡ ሁሉ፡ ሕሊና፡ በእግዚአብሔር፡ ፊት፡ እንገል
ጻለን። ፩፡ ተሰ፡ ፪፡ ፭።

፫፡ ወንጌላችን፡ግን፡ የተከደነች፡ብትሆን፡ ከሚጠ
ፉት፡ ሰዎች፡ *የተከደነች፡ ናት። *፩፡ ቆሮ፡ ፩፡ ፲፰።

፬፡ በርሳቸውም፡ ዘንድ፡ የዚህ፡ ዓለም፡ አምላክ፡
የማያምኑትን፡ ልብ፡ አሳወረ። የክርስቶስ፡ የክብሩ፡
ወንጌል፡ ብርሃን፡ እንዳያበራላቸው፡ እርሱም፡* የእ
ግዚአብሔር፡ ምሳሌ። *ዕብ፡ ፩፡ ፫።

፭፡ እኛ፡ በራሳችን፡ *የምንሰብክ፡ አይደለነምና፡
በየሱስ፡ ክርስቶስ፡ በጌታችን፡ እንጂ። ራሳችነን፡ ግን፡
ለላንት፡ ባሮች፡ እናደርጋለን፡ስለ፡ የሱስ።
*ም፡ ፩፡ ፳፬።

፮፡ *እግዚአብሔር፡ ከጨለማ፡ ብርሃን፡ ይወጣ፡ ዘ
ንድ፡ ያዘዘ፡ እርሱ፡ በልባችን፡ †ብርሃን፡ ሰጥቶልናልና፡
የእግዚአብሔርን፡ የክብሩን፡ ዕውቀት፡ ለማብራት፡
በየሱስ፡ክርስቶስ፡ ፊት። *ዘፍጥ፡ ፩፡ ፫።
†፪፡ ጴጥ፡ ፩፡ ፲፱።

፯፡ ይህም፡ *መዝገብ፡ በሸክላ፡ እቃ፡ አለን፡ የኃይ
ል፡ ታላቅነት፡ ከእግዚአብሔር፡ ይሆን፡ ዘንድ፡ †ከኛ
ም፡ አይደለም። *ም፡ ፭፡ ፩። †፩፡ ቆሮ፡ ፪፡ ፭።

፰፡ እኛ፡ በሁሉ፡ *ይከፋናል፡ ነገር፡ ግን፡ አንጨነቅ
ም። መከራ፡እንቀበላለን፡ነገር፡ ግን፡ ተስፋ፡ አንቈር
ጥም። *ም፡ ፩፡ ፰። ና፡ ፯፡ ፭።

፱፡ እንሰደዳለን፡ ነገር፡ ግን፡ *አንጣልም። እንወድ
ቃለን፡ነገር፡ግን፡አንጠፋም። *መዝ፡ ፴፯፡ ፳፬፡ ፴፫።

፲፡ ሁልግዜም፡ በሥጋችን፡ የክርስቶስን፡ ሞት፡ *እ
ንሸከማለን፡የክርስቶስ፡ሕይወት፡ደግሞ፡በሥጋችን፡
ይገለጥ፡ ዘንድ። *ሮሜ፡ ፰፡ ፲፯።

፲፩፡ እኛም፡ሕያዋን፡ሁነን፡ሁልግዜ፡ *ለሞት፡ የተ
ሰጠነ፡ ሆነ፡ስለ፡ የሱስ። የየሱስ፡ሕይወት፡ደግሞ፡ይገ
ለጥ፡ ዘንድ፡ በዚህ፡ በሚሞተው፡ ሥጋችን።
*መዝ፡ ፵፬፡ ፳፫።

፲፪፡ እንግዴህ፡ *ሞት፡ በላያችን፡ ብርቱ፡ ሆነ፡ ሕይ
ወት፡ ግን፡ በላንት። *፩፡ ቆሮ፡ ፬፡ ፱።

፲፫፡ እኛም፡ደግሞ፡አንድ፡መንፈስ፡ያለነ፡የሃይማ
ኖት፡ መንፈስ፡ የሚሆን፡ እንደ፡ *ተጻፈ። አመንሁ፡
ስለዚህም፡ ተናገርሁ። እኛም፡ ደግሞ፡ እናምናለን፡
ስለዚህም፡ እንናገራለን። *መዝ፡ ፻፲፮፡ ፲።

፲፬፡ እናውቃለንም፡ያ፡ *ጌታችነን፡ የሱስ፡(ክርስቶ

ስን፡) ከሙታን፡ ያስነሣው፡ እኛንም፡ ደግሞ፡ ያስነሣ
ናል፡ በጌታችን፡ በየሱስ፡ ክርስቶስ፡እጅ፡ ከላንተ፡ ጋራ
ም፡ ያቀመናል። *የሐዋ፡ ፫፤ ፲፭፡፡
፲፭፤ ነገርም፡ሁሉ፡ስለላንተ፡ነው፡ *ጸጋ፡ በበዛ፡ጊዜ፡
ከብዙ፡ሰዎች፡ምስጋና፡ ይበዛ፡ ዘንድ፡ ለእግዚአብሔ
ር፡ክብር። *ሮሜ፡ ፭፤ ፲፭፡፡
፲፮፤ ስለዚህም፡እንደክምም፡ *ሚደዊውም፡ ሥ
ጋችን፡ቢጠፋ፡ †የውስጡ፡ ሰውነታችን፡ ግን፡ዕለት፡ዕ
ታደሳል። *፩፤ ጴጥ፡ ፬፤ ፩፡፡ †ኤፌ፡ ፫፤ ፲፮፡፡
፲፯፤ የዚህ፡ ዘመን፡ *መከራ፡ ምንም፡ቀሎ፡ አላፊ
ና፡ቃላል፡ቢሆን፡እጅግ፡ ታላቅ፡ ክብር፡ ያደርግልናልና፡
ፍጻሜ፡ የሌለው፡ ለዘላለሙ። *ሮሜ፡ ፰፤ ፲፰፡፡
፲፰፤ ይህንንም፡ *የሚታየውን፡ ነገር፡ አንመለከት
ም፡ ነገር፡ ግን፡ የማይታየውን። የሚታየው፡ የዛሬ፡
ነውና፡ ያልፈ.ማል። የማይታየው፡ ግን፡ የዘላለም፡
ነው። *ሮሜ፡ ፰፤ ፳፬፤ ፳፭፡፡

ምዕራፍ፡ ፭፤

፩፤ እናውቃለንና፡ የዚህ፡ የምድራዊው፡ የቤታች
ን፡ *ድንኳን፡ቢፈርስ፡ ከእግዚአብሔር፡ †ቤት፡እንደ
ለን፡እጅ፡ያልሰራው፡ እርሱም፡ የዘላለም፡ በሰማይ።
*ኢዮብ፡ ፬፤ ፲፱፡፡ ፪፤ ጴጥ፡ ፩፤ ፲፫፤ ፲፬፡፡ †ዮሐ፡ ፲፬፤ ፪፡፡
፪፤ ስለዚህም፡ *እንቈዝማለን፡ እንናፍቅማለን፡
የሰማዩን፡ ቤታችንን፡ እስክንለብስ፡ ድረስ።
*ሮሜ፡ ፰፤ ፳፫፡፡
፫፤ በለበስነውም፡ ጊዜ፡ ደግሞ፡ ራቁታችንን፡ አንገ
ኝም።
፬፤ አሁንም፡እኛ፡ በዚህ፡ ማደርያ፡ሳለን፡ እንቈዝ
ማለን፡ ከመክበዷ፡ የተነሣ። ልናወጣስ፡ግንወድ፡ *በ
ሕይወት፡ ይዋጥ፡ ዘንድ። *፩፤ ቆሮ፡ ፲፭፤ ፶፫፡፡
፭፤ ለዚህም፡ የሚያዘጋጀን፡ እግዚአብሔር፡ ነው፡
የመንፈሱን፡ መያዣም፡ ደግሞ፡ የሰጠን።
ም፡ ፩፤ ፳፪፡፡ ሮሜ፡ ፰፤ ፲፮፤ ፳፫፡፡ ኤፌ፡ ፩፤ ፲፫፤ ፲፬፡፡
፮፤ ሁለግዜም፡ አምነናል፡ አውቀናልም፡ እኛ፡በ
ሥጋ፡ሳለን፡ ከጌታችን፡ እንድንርቅ። *ዕብ፡ ፲፩፤ ፲፫፡፡
፯፤ በሃይማኖት፡ እንሔዳለንና፡ በማየት፡ አይደ
ለም። ፩፤ ቆሮ፡ ፲፫፤ ፲፪፡፡
፰፤ ነገር፡ ግን፡ እናምናለን፡ አብዝተንም፡ እንመኛ
ለን፡ከዚህ፡ሥጋ፡እንርቅ፡ዘንድ፡ከጌታም፡ጋራ፡እንሆ
ን፡ዘንድ። ፊል፡ ፩፤ ፳፫፡፡
፱፤ ስለዚህም፡እንጠጣር፡ከርሱ፡ጋራ፡ያለን፡ብንሆ
ን፡ወይም፡ *የራቅን፡ ብንሆን፡ እርሱን፡ ደስ፡ እናሰኝ
ዘንድ። መዝ፡ ፵፱፤ ፲፫፡፡
፲፤ ሁላችን፡ይገባናልና፡በክርስቶስ፡ወንበር፡ *ፊት፡
እንገለጥ፡ ዘንድ፡ ሁሉ፡ ኢያንዳንዱ፡ የሰራውን፡ ብድ
ራት፡ ይወስድ፡ ዘንድ፡ በሥጋው፡ እንደ፡ ስራ፡ መልካ
ምም፡ ቢሆን፡ ክፉም፡ ቢሆን። *የሐዋ፡ ፲፯፤ ፴፩፡፡
ሮሜ፡ ፪፤ ፮፡፡ ፲፬፤ ፲፡፡
፲፩፤ የእግዚአብሔርንም፡ግርማ፡ *ስላወቅን፡ ሰዎ
ችን፡እናግባለን፡ ለእግዚአብሔር፡ ግን፡ የተገለጥን፡
ነን። ተስፋም፡ እናደርጋለን፡ ደግሞ፡ በሕሊናችሁ፡ የተ
ገለጥን፡ እንደ፡ ሆነ። *ኢዮብ፡ ፴፩፤ ፳፫፡፡
፲፪፤ ራሳችንን፡ *በላንተ፡ ዘንድ፡ ደግሞ፡ የምናመሰ
ግን፡ አይደለንምና። ነገር፡ ግን፡ ምክንያት፡ እናደርግላ
ችኋለን፡ ትመኩብን፡ ዘንድ፡ በለዚያ፡ ፊት፡ በፊት፡የ
ሚመኩ፡ በልብም፡ አይደለውም። *ም፡ ፫፤ ፩፡፡
፲፫፤ ሰነፎችም፡ብንሆን፡ ለእግዚአብሔር፡ ሰነፍን።
አዋቆችም፡ ብንሆን፡ስለላንተ፡አወቅን።
፲፬፤ የክርስቶስ፡ ፍቅር፡ይዞናልና፡ እንደዚህም፡ እ
ንፈርዳለን። *አንድ፡ሰው፡ ስለ፡ ሁሉ፡ ቢሞት፡ ሁሉ፡
ሙተዋል። *ዕብ፡ ፪፤ ፱፡፡
፲፭፤ እርሱም፡ ሞተ፡ስለ፡ሁሉ፡ *የሚድኑ፡ለራሳቸ
ው፡ እንዳይኖሩ፡ ነገር፡ግን፡ †ስለርሳቸው፡ ለሞተው፡
ለተነሣውም። *፩፤ ጢሞ፡ ፪፤ ፮፡፡ †ሮሜ፡ ፲፬፤ ፯፤ ፰፡፡
፲፮፤ ዛሬም፡ ማንንም፡ በሥጋ፡የምናውቅ፡አይደለ
ንም። ክርስቶስንም፡ በሥጋ፡ያወቅነው፡ ብንሆን፡ ዛ
ሬ፡ግን፡ የምናውቀው፡ አይደለንም፡
፲፯፤ በክርስቶስም፡ *የሆነው፡ ሁሉ፡ እርሱ፡ አዲስ፡
ፍጥረት፡ነው። †አሮጌው፡ ስራ፡ ፈጽሞ፡ሔደ፡ እነሆ፡
ሁሉ፡ ታደሰ። *ሮሜ፡ ፰፤ ፩፤ ፲፡፡ †ኢሳ፡ ፵፫፤ ፲፱፡፡
ራእ፡ ፳፩፤ ፭፡፡
፲፰፤ ሁሉም፡ *ከእግዚአብሔር፡ ነው፡ ከራሱ፡ ጋራ፡
ያስታረቀን፡ በየሱስ፡ ክርስቶስ፡ የመታረቅም፡ መልእ
ክት፡ የሰጠን። *ሮሜ፡ ፭፤ ፲፡፡
፲፱፤ *እግዚአብሔር፡ በክርስቶስ፡ ሁንዋልና፡ ዓለ
ሙንም፡ለርሱ፡ ታርቀታልና፡ ኃጢአታቸውን፡ ሳይቈ
ጥርባቸው። በኛም፡ የመታረቅ፡ ነገር፡ አኖረብን።
*ሮሜ፡ ፫፤ ፳፬፤ ፳፭፡፡ ቆል፡ ፩፤ ፲፱፤ ፳፡፡
፳፤ እኛም፡በክርስቶስ፡ *ፈንታ፡ እንለምናለን። እ
ግዚአብሔርም፡ ደግሞ፡ በጃችን፡ ይለምናችኋል። በ
ክርስቶስ፡ ፈንታ፡ እንለምናችኋለን፡ ለእግዚአብሔ
ር፡ ትታረቁ፡ ዘንድ። *ኢሳ፡ ፶፪፤ ፯፡፡
፳፩፤ ኃጢአት፡ *የማያውቀውን፡ †ስለኛ፡ ኃጢአ
ት፡አድርጎታልና። እኛ፡ **በርሱ፡ የእግዚአብሔር፡ ጽ
ድቅ፡እንሆን፡ዘንድ፡ *፩፤ ጴጥ፡ ፪፤ ፳፪፡፡ ዕብ፡ ፬፤ ፲፭፡፡
†ገላት፡ ፫፤ ፲፫፡፡ **፩፤ ቆሮ፡ ፩፤ ፴፡፡ ፊል፡ ፫፤ ፱፡፡

ምዕራፍ፡ ፮፤

፩፤ እኛ፡ ከርሱ፡ጋራ፡ የምንሰራ፡ ግን፡ *እንለምናች
ኋለን፡ የእግዚአብሔርን፡ ጸጋ፡ በከንቱ፡ እንዳትቀበ
ሉ። *ም፡ ፩፤ ፳፬፡፡ ፭፤ ፳፡፡
፪፤ ይላልና። *በምቀበልበት፡ ጊዜ፡ ሰማሁህ፡ በመ
ድኃኒትም፡ቀን፡ ረዳሁህ። እነሆ፡ †ዛሬ፡ ነው፡ የሚቀ
በልበት፡ ጊዜ። እነሆ፡ዛሬ፡ ነው፡ የመድኃኒቱ፡ ቀን።
*ኢሳ፡ ፵፱፤ ፰፡፡ †ሉቃ፡ ፬፤ ፲፱፤ ፳፡፡
፫፤ በማንም፡ማሰናከልን፡አናደርግ፡ግንደች፡ከተ።
መልእክታችን፡ እንዳትነወር።
፬፤ ራሳችንን፡እንገለጽ፡እንጂ፡*በነገሩ፡ሁሉ፡እንደ፡

እግዚአብሔር፡ ሎሌት፡ በብዙ፡ ትዕግሥት፡ በኀዘን
ም፡ በመከራም፡ በመጨነቅም። *ም፡ ፬፡ ፪።

፭፡ በመመታትም፡ በግዞትም፡ በሁከትም፡ በድካ
ምም፡ በትጋትም፡ በጾምም። ም፡ ፲፩፡ ፳፫—፳፯።

፮፡ *በንጽሕናም፡ በውቀትም፡ በርኅራኄም፡ በቸ
ርነትም፡ በመንፈስ፡ ቅዱስም፡ በመውደድ፡ ያለ፡ ተን
ኰል። *፩፡ ጢሞ፡ ፬፡ ፲፪።

፯፡ በውነት፡ ነገርም፡ በእግዚአብሔር፡ *ኀይልም፡
የጽድቅን፡ እቃ፡ ጦር፡ ለብሰን፡ በቀኝና፡ በግራ።
*፩፡ ቆሮ፡ ፪፡ ፬።

፰፡ በክብርም፡ በአፍረትም። በኀቅም፡ ተብለን፡
ክፉቅም፡ ተብለን። እንደ፡ አሳቾች፡ እኛ፡ እውነተኞች፡
ስንሆን።

፱፡ እንደማንታወቅ፡ እኛ፡ በጣም፡ ስንታወቅ። እን
ደ፡ *ምዋቾችም፡ እነሆም፡ ሕያዋን፡ ነን። እንደምንሣ
ቀይም፡ ያልሞትነ። *ም፡ ፬፡ ፲፡ ፲፩። መዝ፡ ፻፲፰፡ ፲፰።

፲፡ እንደምናዝን፡ ሁለግዜም፡ ደስ፡ ይለናል። እን
ደ፡ ድኆችም፡ ብዙ፡ ሰዎችን፡ ባለጠጎች፡ ስናደርግ። እ
ንደቾም፡ እንደ፡ ሌለነ፡ እኛ፡ ሁሉን፡ ስንገዛ።

፲፩፡ አፋችን፡ ለላንት፡ ተከፍቷል፡ እላንት፡ የቆ
ሮንቶስ፡ ሰዎች። ልባችን፡ ሰፍቷል።

፲፪፡ በኛ፡ አልጠበባችሁም፡ በልባችሁ፡ ጠባችኋል፡
እንጂ።

፲፫፡ እላችሁማለሁ፡ *ልጆቼ፡ ስለ፡ ሆናችሁ። እርስ
ዋን፡ ይህችን፡ ብድራት፡ ስጡኝ፡ ውደቻችሁንም፡ አስ
ፋልኝ። *፩፡ ቆሮ፡ ፬፡ ፲፬።

፲፬፡ *ከማያምኑ፡ ሰዎች፡ ጋራ፡ የምትስማሙ፡ አ
ትሁኑ። ምን፡ †አንድነት፡ አለ፡ በጽድቅና፡ በኃጢአ
ት፡ መካከል። ወይስ፡ ምን፡ መገናኘት፡ አለው፡ ለብር
ሃን፡ ከጨለማ፡ ጋራ። *ዘዳግ፡ ፯፡ ፪። †ኤፌ፡ ፭፡ ፲፩።

፲፭፡ ወይስ፡ ምን፡ ባልንጀርነት፡ አለው፡ ለክርስቶስ፡
ከሰይጣን፡ ጋራ፡ ወይስ፡ ምን፡ ፈንታ፡ ለሚያምን፡ ከ
ማያምን፡ ጋራ።

፲፮፡ ወይስ፡ ምን፡ መዋደድ፡ አለው፡ ለእግዚአብ
ሔር፡ መቅደስ፡ ከጣዖታት፡ ጋራ። እላንት፡ የሕያው፡
እግዚአብሔር፡ *መቅደስ፡ ናችሁና፡ እግዚአብሔር፡
እንደለ። †እኔ፡ አድርባቸዋለሁ፡ ከርሳቸውም፡ ጋራ፡
እሔዳለሁ። እኔም፡ አምላካቸው፡ እሆናለሁ፡ እርሳ
ቸውም፡ ወገኖቼ፡ ይሆናሉ። *፩፡ ቆሮ፡ ፫፡ ፲፮።
†ዘሌዋ፡ ፳፮፡ ፲፪።

፲፯፡ ስለዚህም፡ *ከመካከላቸው፡ ውጡ፡ ከርሳቸ
ውም፡ ተለዩ፡ እግዚአብሔር፡ ይላል። ወደ፡ ርኩስም፡
ሁሉ፡ አትቅረቡ፡ እኔም፡ እቀበላችኋለሁ።
*ኢሳ፡ ፵፰፡ ፳። ና፡ ፶፪፡ ፲፩። ራእ፡ ፲፰፡ ፬።

፲፰፡ እኔም፡ *አባት፡ እሆናችኋለሁ፡ እላንትም፡ ል
ጆች፡ ትሆኑልኛላችሁ። ይላል፡ እግዚአብሔር፡ ሁሉን፡
የሚችል። *ኤር፡ ፴፩፡ ፩፡ ፱፡ ፴፫። ና፡ ፴፪፡ ፴፰።

ምዕራፍ፡ ፯፡

፩፡ እንደዚህ፡ ያለ፡ ተስፋ፡ ሳለነ፡ ወዳጆቼ፡ ሆይ፡ ሰው
ነታችንን፡ እናጽራ፡ ከሥጋና፡ ከነፍስ፡ ርኩሰት፡ ሁሉ፡ ቅ
ድስናን፡ በመፈጸም፡ እግዚአብሔርን፡ እየፈራን።

፪፡ ተቀበሉነ። እኛ፡ ማንንም፡ አልበደልነምና፡ ማንን
ም፡ አልማረክነም። ም፡ ፲፪፡ ፲፯። የሐዋ፡ ፳፡ ፴፫።

፫፡ ይህነንም፡ የምል፡ ለመኰነን፡ አይደለም። አስ
ቀድሜ፡ ብያለሁና፡ *በልባችን፡ እንዳላችሁ፡ ከላንት፡
ጋራ፡ እንሞትና፡ እንኖር፡ ዘንድ። *ም፡ ፮፡ ፲፩—፲፫።

፬፡ ለኔ፡ ታላቅ፡ ድፍረት፡ አለኝ፡ በላንት፡ አኰል።
ለኔ፡ ታላቅ፡ ትምክሕት፡ ነው፡ ስለላንት። ደስታ፡ መላ
ብኝ፡ እጅግም፡ በዛ፡ ደስታዬ፡ በመከራችን፡ ሁሉ።

፭፡ ወደ፡ መቄዶንያ፡ በመጣነ፡ ጊዜ፡ ለሰውነታችን፡
አንዲት፡ ስንኳ፡ ዕረፍት፡ አላገኘነምና፡ በሁሉ፡ አዘ
ንነ፡ እንጂ። በሜዳ፡ ሰልፍ፡ በውሥጥም፡ ፍርሃት።

፮፡ ነገር፡ ግን፡ አዘንተኞችን፡ ደስ፡ የሚያሰኝ፡ እግዚ
አብሔር፡ ደስ፡ አሰኘነ፡ በቲቶስ፡ መምጣት።
ም፡ ፩፡ ፫፡ ፬። ፪፡ ፲፫።

፯፡ በመምጣቱም፡ ብቻ፡ አይደለም፡ ደስ፡ ባሰኘች
ሁትም፡ ደስታ፡ እንጂ፡ ደግሞ። እንደ፡ ናፈቃችሁኝ፡
በነገረነ፡ ጊዜ፡ በልቅሶዋችሁም፡ በቅንዓታችሁም፡ ስለ
ኔ። እኔንም፡ በዚህ፡ እጅግ፡ ደሳለኝ።

፰፡ በመልእክትም፡ አሳዝኛችሁ፡ እንደ፡ ሆንሁ፡ አ
ሁን፡ አላዝንም፡ አዝኜም፡ እንደሆንሁ። ያች፡ መል
እክት፡ በጥቂት፡ ጊዜ፡ አሳዝናችሁ፡ እንደ፡ ሆነች፡ አያለ
ሁና። ም፡ ፪፡ ፬።

፱፡ አሁን፡ ግን፡ ደስ፡ ይለኛል፡ ስላዘናችሁ፡ አይደለ
ም። ለንስሐ፡ አዝናችኋልና፡ እንጂ። ለእግዚአብሔ
ር፡ ደስ፡ የሚያሰኝ፡ አዘን፡ አዝናችኋልና፡ ከኛ፡ እንደት
ጐዱ፡ ባንድ፡ ነገር፡ ስንኳ።

፲፡ እግዚአብሔርን፡ ደስ፡ የሚያሰኝ፡ አዘን፡ ወደ፡
ደህንነት፡ የሚያደርስ፡ ንስሐ፡ ያደርጋልና፡ አዘን፡ የሌ
ለበት። የዚህ፡ *ዓለም፡ አዘን፡ ግን፡ ሞት፡ ያደርጋል።
*ማ፡ ፳፯፡ ፫—፲።

፲፩፡ አሁንም፡ እነሆ፡ የልብ፡ አዘን፡ እንደ፡ እግዚአ
ብሔር፡ ፈቃድ፡ የሚሆን፡ ስንት፡ ጥረት፡ አሻችሁ። ል
መናም፡ ቍጣም፡ ፍርሃትም፡ ንፍቀትም፡ ቅናትም፡
መበቀልም፡ ሰውነታችሁን፡ አቀማችሁ፡ በሁሉ፡ ንጹ
ሓን፡ ሁናችሁ፡ በዚህ፡ ነገር።

፲፪፡ ይህም፡ ወደላንት፡ የጻፍሁላችሁ፡ ስለርሱ፡ ስ
ለ፡ በደደ፡ አይደለም፡ ስለ፡ ተበደደም። ነገር፡ ግን፡ በኛ፡
ምክንያት፡ ስለላንት፡ የምናደርገው፡ መጋደል፡ በእግ
ዚአብሔር፡ ፊት፡ ይገለጥ፡ ዘንድ፡ ነው።

፲፫፡ ስለዚህም፡ ደስ፡ አለነ፡ በደስታችሁ። የሚበል
ጥም፡ ደስታ፡ ደሳለነ፡ በቲቶስ፡ ደስታ። ሰውነቱ፡ አርፏ
ለችና፡ በላንት፡ በሁላችሁ፡ ዘንድ።

፲፬፡ በርሱ፡ ዘንድም፡ ስለላንት፡ የተመካሁበት፡ ቢ
ሆን፡ አላፈርሁበትም፡ ነገር፡ ግን፡ እንደ፡ ነገርናችሁ፡ በ

ውነት፡በነገራችን፡ሁሉ፡እንደዚሁም፡ በላንት፡ መመ
ካታችን፡በቲቶስ፡ዘንድ፡እውነት፡ ሆነ።

፲፭፤ ወደላንትም፡ውደ፡እጅግ፡ነው።የሁላችሁን፡
*መታዘዝ፡ ኢያሰበ ፡ በፍርሃትና ፡ በመንቀጥቀጥም፡
እንደ፡ ተቀበላችሁት።

*ም፡ ፪፤ ፱።

፲፮፤ ደስም፡ ደለኛል፡ በሁሉ፡ ታምኛችኋለሁና።

ምዕራፍ፡ ፰፤

፩፤ እናስታውቃችሁማለን፡ ወንድሞቼ፡ ሆይ፡ የእ
ግዚአብሔርን፡ጸጋ፡ለመቄዶንያ፡ቤተ፡ ክርስቲያን፡ የ
ተሰጠችውን። ሮሜ፡ ፲፭፤ ፳፮። ፩፤ ቆሮ፡ ፲፮፤ ፩።

፪፤ በብዙ፡ባዘናቸው፡ መፈተን፡ደስታቸው፡ ተረፈ
ለችና፡እጅግ፡ የጠለቀች፡ችጋራቸውም፡ በዝታለችና፡
ወደ፡ልግሥነታቸው፡ ባለጸግነት።

፫፤ እመሰክራለሁና ፡ በችሎታቸው ፡ መጠን ፡ ከች
ሎታቸውም፡ በሚበልጥ፡ በፈቃዳቸው፡ እንደ፡ በዙ።

፬፤ በብዙ፡ልመናም፡ፈለጉነ፡ጸጋ፡እንቀበል፡ዘንድ፡
ለቅዱሳንም፡የምትሆነውን፡ የማገልገል፡ አንድነት።

ም፡ ፱፤ ፩። የሐዋ፡ ፲፩፤ ፳፱።

፭፤ እኛም፡ተስፋ፡እንደደረግነው፡አይደለውም።
ራሳቸውን፡ ለእግዚአብሔር፡ አስቀድሞ ፡ ሰጡ፡ እን
ጅ፡ለኛም፡በእግዚአብሔር፡ ፈቃድ።

፮፤ ቲቶስን፡ እስክንለምን፡ድረስ፡ አስቀድሞ፡እን
ደ፡ጀመረ፡ እንደሁ፡ ደግሞ፡ ይህችን፡ጸጋ ፡ በላንት፡ደ
ጨርስ፡ ዘንድ።

፯፤ ነገር፡ግን፡ በሁሉ፡ እንደ፡ በዛችሁ፡ በሃይማኖት፡
በቃልም፡በውቀትም፡በመጠበቅም፡ ሁሉ፡እኛንም፡
በመውደዳችሁ ። እንደሁም ፡ በዚህ ፡ ጸጋ፡ ደግሞ፡
ብዙ።

፰፤ በማዘዝም፡የምላችሁ፡ አይደለም፡ነገር፡ ግን፡
ስለ፡ ሌሎች፡ ጥረት፡ የፍቅራችሁንም ፡ ቅንነት ፡ ለመ
መርመር።

፱፤ የጌታችነን፡ የየሱስ፡ ክርስቶስን ፡ ጸጋ፡ አውቃች
ኋልና። ስለላንት፡ *ድኃ፡ ሁንዋልና፡ ባለጠጋ፡ ሳለ። እ
ላንት፡ በድህነቱ፡ ባለጠጎች፡ ትሆኑ፡ ዘንድ።

*ማቴ፡ ፰፤ ፳።

፲፤ አሁንም፡ በዚህ፡ እመክራችኋለሁ፡ በሚረባች
ሁ፡ ነገር ። የምታደርጉ፡ ብቻ፡ አልሆናችሁምና፡ በፈቃ
ዳችሁ፡ የምትወዱም ፡ እንጅ ፡ ካምና፡ ጀምራችሁ፡
አስባችኋልና።

፲፩፤ አሁንም፡ በማድረግ፡ ፈጽሙ ። እንደ፡ ወደዳ
ችሁ፡ ታደርጉ፡ ዘንድ፡ እንደሁ ፡ በማድረግ፡ ፈጽሙ፡
ኢያንዳንዳችሁ፡ ከከብታችሁ።

፲፪፤ ፈቃድ፡ ካለች፡ሰው፡ እንደለችው፡ መጠን፡ ደ
ቀበላል፡ በሌለውም፡ መጠን፡ አይደለም።

ምሳ፡ ፫፤ ፳፰። ማር፡ ፲፪፤ ፵፫።

፲፫፤ ለሌሎችም፡ዕረፍት፡ይሆን፡ዘንድ፡አይገባም፡
በላንትም፡ ጭንቀት፡ ነገር፡ ግን ፡ የተካከላችሁ፡ ሁኑ።

፲፬፤ በዚህ፡ዘመን፡ከላንት፡ የተረፈው፡ የለዚያን፡
ጉደሉ፡የሚመላ፡ይሆን፡ዘንድ። ከለዚያም፡ደግሞ፡
የተረፈው፡ የላንትን፡ ጉደሉ ፡ እንደ፡ዘጋ ፡ የተካከለ፡
ይሆን፡ ዘንድ። ም፡ ፱፤ ፲፪።

፲፭፤ እንደ፡ *ተጻፈ። እጅግ፡ የወሰደ፡አንዳች፡ አል
ተረፈውም ፡ ጥቂትም ፡ የወሰደ ፡ አልጐደለበትም።

*ዘፀአ፡ ፲፮፤ ፲፰።

፲፮፤ ለእግዚአብሔርም፡ *ምስጋና፡ ይሁነው፡ይህነ
ን፡ጥረት፡በቲቶስ፡ልብ፡የሰጠ፡ስለላንት። *ም፡ ፱፤ ፲፭።

፲፯፤ ልመናችነን፡እሺ፡ብልዋልና። ነገር፡ ግን፡እጅግ፡
ደጥር፡ስለ፡ ነበረ፡ ወደላንት፡ ወጣ፡ በፈቃዱ።

፲፰፤ ደግሞም ፡ ከርሱ፡ ጋራ፡ ወንድማችነን፡ ላክነ፡
ምስጋናው፡ በወንጌል፡ የሚሆን፡ በቤተ፡ ክርስቲያን፡
ሁሉ።

፲፱፤ ደህ፡ብቻም፡አይደለም። ቤተ፡ ክርስቲያናት፡
መረጡት፡እንጅ፡ ከኛ፡ጋራ፡ ደሔድ፡ ዘንድ፡ ስለዚህ፡
ጸጋ፡እኛ፡ስለምናገለግለው፡ ለእግዚአብሔር፡ ምስጋ
ና፡ለበጎውም፡ ፈቃዳችሁ፡ ምስክር።

፳፤ በዚህም፡ነገር፡ተጠበቅነ፡ማንም፡ እንዳያነው
ረነ፡በዚህ፡ በምናገለግለው፡ ባለጠግነት።

፳፩፤ እንጠነቅቃለንና ፡ ደህ፡ ነገር፡ መልካም፡ ደሆ
ን፡ ዘንድ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ብቻ ፡ አይደለም፡
በሰው፡ ፊትም፡ እንጅ።

፳፪፤ ከርሳቸውም፡ጋራ፡ ወንድማችነን፡ ላክነ፡ በብ
ዙ፡ነገር፡ የፈተነውን፡ እርሱም፡ብዙ፡ጊዜ፡ እንዲጥር፡
አገኘነው ። አሁንም፡ አጥብቆ ፡ ደጥራል፡ እላንትን፡
በብዙ፡ መታመኑ።

፳፫፤ *ቲቶስም ፡ ቢሆን ፡ እርሱ፡ ባልንጀራዬ፡ ነው፡
አብሮኝም፡የሚሰራ፡በላንት፡ዘንድ። ወንድሞቻችን
ም፡ቢሆኑ፡እርሳቸውም፡የቤተ፡ክርስቲያን፡ †መለክ
ተኞች፡ ናቸው፡ የክርስቶስ፡ ክብር።

*ም፡ ፯፤ ፲፫። ፲፪፤ ፲፰። †ሮሜ፡ ፲፮፤ ፯።

፳፬፤ ማናቸውም ፡ ቢሆን ፡ የፍቅራችሁን፡ ጽናት፡
ግለጡ። በላንትም፡ የሆነውን፡ *ትምክሕታችን፡ ለር
ሳቸው፡ ግለጡት፡ በቤተ፡ ክርስቲያን፡ ፊት።

ም፡ ፯፤ ፲፬።

ምዕራፍ፡ ፱፤

፩፤ ለቅዱሳን፡ስለ፡ማገልገል፡ ግን፡ ልጽፍላችሁ፡ አ
ያሻኝም። ም፡ ፰፤ ፬፤ ፳።

፪፤ የምክራችሁን፡ *መልካምነት ፡ አውቃለሁና።
ስለዚህም፡ ተመካሁባችሁ ፡ በመቄዶንያ፡ ሰዎች፡ ዘ
ንድ፡ አልሁም፡ የአካይያ፡ ሰዎች፡ ተዘጋጅተዋል፡ ካ
ምና፡ጀምሮ፡ ቅናታችሁም፡ ብዙ፡ ሰዎች፡ አስቀናች።

*ም፡ ፰፤ ፲፱።

፫፤ ወንድሞችንም፡ የላክነባችሁ፡ በዚህ፡ነገር፡ የተ
መካነው፡ትምክሕት፡ከንቱ፡ እንዳይሆን፡ ነው። የተ
ዘጋጃችሁም፡ ትሆኑ፡ ዘንድ፡ እኔ፡ እንዳልሁ።

ም፡ ፰፤ ፳፬።

፬፡ ምን፡አልባት፡ የመቄዶንያ፡ ሰዎች፡ ከኔ፡ጋራ፡ የመጡ፡እንደሆን፡ሳትዘጋጁ፡ም፡ ያገኙዋችሁ፡ እንደሆን፡እኛ፡እናፍራለን፡ በላንት፡ ስላልነው፡ የተነሣ። እላንትም፡ታፍራላችሁ፡አንልም።

፭፡ ስለዚህም፡ የግድ፡ አሰብሁ፡ የወንድሞችን፡ ልብ፡ አባብል፡ ዘንድ፡ ወደላንት፡ እንዲቀድሙኝ፡ ከጥንትም፡ የነገራችኋትን፡ በረከት፡ እንዲያዘጋጁ። ይህች፡ እንደሁ፡ የተዘጋጀች፡ ልትሆን፡ እንደ፡ በረከት፡ እንደ፡ንፉገትም፡ አይደለም።

፮፡ በንፉገት፡ የዘራ፡ በንፉገትም፡ ያጭዳልና፡በበረከትም፡ የዘራ፡ በበረከትም፡ ያጭዳል።

ምሳ፡ ፲፩፡ ፳፬። ፲፱፡ ፲፯።

፯፡ ኢያንዳንዱ፡ በልቡ፡ እንደ፡ ተዘጋጀ፡ ያድርግ። በልብ፡ችጋርም፡ በግድም፡ እንደሚሆን፡ አይደለም። እግዚአብሔር፡ *ወደ፡ የሚሰጠውን፡ ይወዳልና።

*ሮሜ፡ ፲፪፡ ፰።

፰፡ እግዚአብሔርም፡ከሃሊ፡ነው፡ ጸጋን፡ሁሉ፡ ያበዛላችሁ፡ ዘንድ፡ሁሉ፡ የተሰጣችሁ፡ እስክትሆኑ፡ ድረስ፡ ትተርፉም፡ አላችሁ፡ በመልካም፡ ስራ፡ ሁሉ።

፱፡ እንደ፡*ተጻፈ። በተነ፡ለድኆች፡ ሰጠ፡ጽድቁ፡ለዘላለም፡ ይኖራል። *መዝ፡ ፻፲፪፡ ፱።

፲፡ ዘርንም፡ ለሚዘራ፡ የሚሰጥ፡ እንጀራንም፡ ለመብል። ይስጣችሁ፡ ዘራችሁንም፡ ያብዛ፡ የጽድቃችሁንም፡ፍሬ፡ያሳድገው። ኢሳ፡ ፶፭፡ ፲። ሆሴ፡ ፲፡ ፲፪።

፲፩፡ በሁሉ፡ባለጠጎች፡ትሆኑ፡ ዘንድ፡ በልግሥና፡ ሁሉ። ምስጋና፡ በኛ፡ የምታስነሣ፡ ለእግዚአብሔር፡

ም፡ ፩፡ ፲፩። ፬፡ ፲፭።

፲፪፡ የዚህ፡ የማገልገል፡ ስራ፡ የቅዱሳንን፡ ጕድሎ፡ ብቻ፡የሚመላ፡አይደለምና፡ በብዙ፡ ሰዎች፡ ለእግዚአብሔር፡ ምስጋና፡ ያበዛል፡ እንጂ። *ም፡ ፰፡ ፲፬።

፲፫፡ ስለዚህ፡ ማገልገል፡ ብዛት፡ እግዚአብሔርን፡ ያመሰግናሉና። ለክርስቶስ፡ ወንጌል፡ ስለ፡ ተገዛችሁ፡ በሃይማኖት። በየውሃታችሁም፡ አንድ፡ሁናችኋልና፡ ከርሳቸው፡ ጋራ፡ ከሰዎችም፡ ሁሉ፡ ጋራ።

፲፬፡ እርሳቸውም፡ ይጸልዩላችኋል፡እላንትን፡ ቢናፍቁ፡ ስለ፡ በዛች፡ ስለ፡ እግዚአብሔር፡ ጸጋ።

፲፭፡ ለእግዚአብሔርም፡ምስጋና፡ይሁነው፡ስለማትነገረው፡ ጸጋው።

ምዕራፍ፡ ፲፡

፩፡ እኔ፡ ጳውሎስም፡ ራሴ፡ እለምናችኋለሁ፡ በክርስቶስ፡ ትሕትና፡ በገርነትም፡ ምንም፡ እኔ፡ በፊታችሁ፡የተዋረድሁ፡ ብሆን፡ ከላንት፡ በራቅሁ፡ጊዜ፡ ልቤ፡ ነቅተላችኋልና። ፩፡ ቆሮ፡ ፪፡ ፫።

፪፡ እለምናችኋለሁም፡ ወደላንት፡ በመጣሁ፡ ጊዜ፡በልቤ፡እጅግ፡ያመንሁ፡እንዳልሆን፡በሰዎች፡ላይ፡ በሚመስላቸው፡ አካሔዳችን፡ በሥጋ፡ መንገድ፡ እንደ፡ሆነ። ቍ፡ ፲፩።

፫፡ ምንስ፡አካሔዳችን፡ በሥጋ፡ ቢሆን፡ በሥጋን፡አንዋጋም።

፬፡ የመጋደላችንም፡ *ጋሻና፡ ጦር፡ በሥጋ፡ አይደለም፡ በእግዚአብሔር፡ ኃይል፡ ነው፡ እንጂ። በርሱ፡ጽኑ፡ አምባ፡ የምናፈርስባት። *ኤፌ፡ ፮፡ ፲፫—፲፯።

፭፡ አሳብን፡ ሁሉ፡ የሚኰራንም፡ ሁሉ፡ በእግዚአብሔር፡እውቀት፡ ላይ፡ የምናፈርስባት። ጥበብንም፡ ሁሉ፡ የምንማርክባት፡ ወደ፡ ክርስቶስ፡ መታዘዝ።

፮፡ መዘጋጀትም፡ አለነ፡ አለመታዘዝን፡ ሁሉ፡ እንበቀል፡ ዘንድ፡ መታዘዛችሁ፡ በተፈጸመች፡ ጊዜ።

፯፡ በፊታችሁ፡ ወደለው፡ ታያላችሁን። ማንም፡ በራሱ፡ ቢያምን፡ የክርስቶስ፡ እንደ፡ ሆነ፡ ይህነን፡ደግሞ፡በራሱ፡ ያስብ። እርሱ፡ ለክርስቶስ፡ እንደ፡ ሆነ፡እኛም፡ ደግሞ፡ እንደሁ፡ ለክርስቶስ፡ ነነ።

፰፡ ይልቁንም፡በዚህ፡*ብመካ፡ጌታ፡በሰጠኝ፡ ተሥልጣን፡ ለመሠራታችሁ፡ ለመፍረሳችሁም፡ አይደለም፡ የማፍር፡ አይደለሁም። *ም፡ ፲፪፡ ፮።

*፩፡ ቆሮ፡ ፭፡ ፪፡ ፬፡ ፭።

፱፡ ማንም፡ እንዲይመስለው፡ በመልእክቴ፡ የማስፈራችሁ።

፲፡ ከላንት፡ የሚል፡ አለና፡ መልእክቱ፡ የከበደ፡ ነው፡ጽኑም፡ነው።የሰውነቱ፡መምጣት፡ግን፡ ደካማ፡ ነው፡ነገሩም፡የሚናቅ፡ ነው። ቍ፡ ፩።

፲፩፡ እንዲህ፡ ያለው፡ ይህነን፡ አሳብ፡ ያስብ። እኛ፡ በመልእክታችን፡ነገር፡ርቀን፡ እንደ፡ ሆነ፡ እንደሁም፡ እኛ፡ደግሞ፡መጥተን፡ ነነ፡ በማድረግ። ም፡ ፲፫፡ ፪፡ ፲።

፲፪፡ ሰውነታችነን፡ ለማኰራት፡ አንደፍርም፡ ራሳችነንም፡ ለማስተካከል፡ ከለዚያ፡ ጋራ፡ ሰውነታቸውን፡ ከሚያኰሩ። እርሳቸውም፡ ሰውነታቸውን፡ እርሱ፡በርሳቸው፡ ቢመጥኑ፡ እርሱ፡ በርሳቸውም፡ ቢያስተካክሉ፡ አያስተውሉም። ም፡ ፫፡ ፩፡ ፭፡ ፲፪።

፲፫፡ እኛ፡ ግን፡ አንመካም፡ በማንችለው፡ ነገር። እግዚአብሔር፡እንደ፡ ሰጠነ፡እንደ፡ ወጉ፡ መጠን፡ ነው፡ እንጂ።ወደላንት፡ ደግሞ፡ እንመጣ፡ ዘንድ።

ሮሜ፡ ፲፪፡ ፫።

፲፬፡ ራሳችነንም፡ የምናኰብር፡ አይደለነም፡ ወደላንት፡ እንደንመጣ። ወደላንትም፡ ደረስነ፡እንጂ፡ በክርስቶስ፡ ወንጌል።

፲፭፡ ከመጠናችንም፡ ይልቅ፡ *የምንመካ፡ አይደለነም፡ በሌሎች፡ድካም። ነገር፡ግን፡ ተስፋ፡አለነ፡ ሃይማኖታችሁ፡ ባደገች፡ ጊዜ፡ በላንት፡ከፍ፡ ከፍ፡ እንድንል፡እንደ፡መጠናችን፡የሚበልጥም። *ሮሜ፡ ፲፭፡ ፳።

፲፮፡ ከኋላችሁ፡ ደግሞ፡ እንግደ፡ እንሆን፡ ዘንድ፡ ወንጌልን፡ በመሰበክ። በሌሎች፡መጠን፡አንመካምና፡ በተዘጋጀው፡ ነገር።

፲፯፡ ነገር፡ ግን፡ የሚመካ፡ በእግዚአብሔር፡ ይመካ። ኤር፡ ፱፡ ፳፫፡ ፳፬። ፩፡ ቆሮ፡ ፩፡ ፴፩።

፲፰፡ ራሱን፡ያከበረ፡እርሱ፡ የከበረ፡ አይደለምና። እግዚአብሔር፡ያከበረው፡እንጂ። ፩፡ ቆሮ፡ ፬፡ ፭።

ምዕራፍ፡ ፲፩፡

፩፡ ምነው፡በታገሡኝ፡ ጥቂት፡ በስንፍናዬ። መሆኑንማ፡ ትታገሡኛላችሁ።

፪፡ እቀናባችኋለሁና፡ በእግዚአብሔር፡ ቅናት። አጭቻችኋለሁና፡ላንድ፡ሰው፡ንጹሕ፡ድንግል፡አድርጌ፡ ለክርስቶስ፡ ላቀርባችሁ። ኤፌ፡ ፭፡ ፳፮፡ ፳፯።

፫፡ እኔም፡ፈርቻለሁ፡ ምን፡ አልባት፡ እባብ፡*ሔዋንን፡በተንኰልዋ፡እንዳታለላት። እንደሁ፡ ሕሊናችሁ፡ እንዳትጠፋ፡ ከየውሃት፡ ከንጽሕናም፡ ወደ፡ ክርስቶስ። *ዘፍ፡ ፫፡ ፬፡ ፲፫።

፬፡ ያም፡ወደላንት፡መጥቶ፡አስተምርዋችሁ፡ እንደ፡ ሆነ፡ በሌላ፡ክርስቶስ፡ እኛ፡ ያላስተማርናችሁ። ሌላም፡መንፈስ፡ተቀብላችሁ፡እንደሆን፡ያልተቀበላችሁትን ። ወይም፡ ሌላ፡ ወንጌል፡ እንደለ፡ ያልወሰዳችሁት። ያነን፡ ስንኳ፡ በታገሣችሁ። ገላ፡ ፩፡ ፰፡ ፱።

፭፡ ለኔ፡ ግን፡ ይመስለኛል፡ አንዳች፡ አላጐደልሁባችሁም፡ በፊተኞች፡ ሐዋርያት። ም፡ ፲፪፡ ፲፩።
፩፡ ቆሮ፡ ፲፭፡ ፲። ገላ፡ ፪፡ ፮፡ ፱።

፮፡ በነገርም፡*ጥሬ፡ ብሆን። ነገር፡ ግን፡ በውቀት፡ እንደሀ፡ አይደለሁም። በነገርም፡ ሁሉ፡በማድረጋችንም፡ ሁሉ፡ ተገለጥነላችሁ። *፩፡ ቆሮ፡ ፪፡ ፩፡ ፪፡ ፲፫።
ኤፌ፡ ፫፡ ፬።

፯፡ ወይስ፡ ኃጢአትን፡ ሰራሁ፡ ራሴን፡ ማውረዴ፡ እላንት፡ ከፍ፡ ከፍ፡ትሉ፡ ዘንድ። የእግዚአብሔርን፡ ወንጌል፡ ያለ፡ *ዋጋ፡ ባስተማርኋችሁ፡ ጊዜ።
*፩፡ ቆሮ፡ ፱፡ ፲፪፡ ፲፰።

፰፡ ሌላውን፡ ቤተ፡ ክርስቲያን፡ ገፈፍሁ፡ ከርሳቸው፡ ዋጋ፡ በወሰድሁ፡ ጊዜ፡ እላንትን፡ ለማገልገል።
ፊል፡ ፬፡ ፲፡ ፲፭።

፱፡ ወደላንትም፡ በመጣሁ፡ ጊዜ፡ በሻሁም፡ ጊዜ፡ ከላንት፡ በማንም፡ *አላበረታሁም። ከመቄዶንያ፡ የመጡ፡ ወንድሞች፡ የሻሁትንን፡ ሁሉ፡ፈጽመዋልና። በነገሩም፡ ሁሉ፡ ሰውነቴን፡ጠበቅሁ፡ ሳላበረታባችሁ፡ እጠብቅማለሁ። *ም፡ ፲፪፡ ፲፫።

፲፡ የክርስቶስ፡ እውነት፡ ከኔ፡ ጋራ፡ ነውና። ይህ፡ ትምክሕት፡ከንቱ፡እንዳይሆን፡ በአካይያ፡አገር፡ሁሉ።
፩፡ ቆሮ፡ ፱፡ ፲፭።

፲፩፡ ያስ፡ ለምንድር፡ነው። እኔ፡አልወዳችሁምነን፡ ነው። እግዚአብሔር፡ያውቃል።

፲፪፡ የማደርገውን፡ ግን፡ አደርገዋለሁ፡ ደግሞ፡ ምክንያት፡ ከሚሹ፡ምክንያት፡ እቈርጥ፡ ዘንድ፡ እንደ ገኙ፡ በሚመኩበት፡ እኛ፡ ደግሞ፡ እንድንገኝ።
፩፡ ቆሮ፡ ፱፡ ፲፪።

፲፫፡ እንደለዚህ፡ ያሉት፡ያሰት፡ሐዋርያት፡ ናቸውና፡ የተንኰል፡ ሰራተኞች፡ በክርስቶስ፡ ሐዋርያት፡ የሚመስሉ። ም፡ ፪፡ ፲፯። ፊል፡ ፫፡ ፪።

፲፬፡ ይህም፡ ድንቅ፡ አይደለም። እርሱ፡ ሰይጣን፡ በብርሃን፡ መልአክ፡ ተለውጦ፡ ይመስላልና።

፲፭፡ ታላቅ፡ነገርም፡ አይደለም፡ሎሌልቱ፡ ምሳሌያቸውን፡ ቢወስዱ፡ የጽድቅ፡ ሎሌልት፡ እንደ፡ሆኑ። ፍጻሜያቸው፡ እንደ፡ ስራቸው፡የሚሆን።

፲፮፡ ደግሞም፡ እላለሁ። ማንም፡ እንዲደመስለው፡ እኔ፡ ሰነፍ፡ እንደ፡ ሆንሁ። ወይም፡ተቀበሉኝ፡ ሰነፎችን፡እንድትቀበሉ። እኔ፡ደግሞ፡ጥቂት፡ እመካ፡ ዘንድ። ም፡ ፲፪፡ ፮።

፲፯፡ ይህነንም፡ የምናገረውን፡ በእግዚአብሔር፡ የምል፡ አይደለሁም፡ ነገር፡ ግን፡ በስንፍና፡ በትምክሕት፡ ሰፍራ።

፲፰፡ ብዙ፡ ሰዎች፡ በሥጋ፡ ስለ፡ ተመኩ፡ እኔም፡ ደግሞ፡ እመካለሁ።

፲፱፡ እላንት፡ሰነፎችን፡ ትታገሡ፡ዘንድ፡ ትወዳላችሁና፡ እላንት፡ ብልሀተኞች፡ስትሆኑ።

፳፡ ማንም፡ ቢገዛችሁ። ማንም፡ቢበላችሁ። ማንም፡ ከብታችሁን፡ቢወስድባችሁ፡ማንም፡ቢኰራባችሁ፡ ማንም፡ፊታችሁን፡ ቢጸፋችሁ፡ትታገሡላችሁና።

፳፩፡ እኔም፡ ይህነን፡ እንደ፡ኀፍረት፡እላለሁ፡እኛ፡ እንደ፡ ደከምነ። ነገር፡ ግን፡ ማንም፡ በሚደፍርበቱ፡ (በስንፍና፡እናገራለሁ፡)እኔ፡ደግሞ፡እደፍርበታለሁ።

፳፪፡ ዕብራውያንን፡ናቸው። እኔም፡እንደሁ፡ነኝ። የእሥራኤል፡ ወገን፡ ናቸው። እኔም፡ ደግሞ። የአብርሃም፡ ዘር፡ ናቸውን። እኔም፡ ደግሞ። ፊል፡ ፫፡ ፭።

፳፫፡ የክርስቶስ፡አገልጋዮች፡ናቸውን። (በስንፍና፡ እናገራለሁ።) እኔ፡ *እበልጣለሁ። በድካም፡ብዝቼ። በመመታትም፡ መልቼ። በመታሠርም፡ አትርፊ። በልዩ፡ ልዩ፡ ሞትም፡ ብዙ፡ ጊዜ። *፩፡ ቆሮ፡ ፲፭፡ ፲።

፳፬፡ ከአይሁድ፡ አምስት፡ ጊዜ፡ ተገረፍሁ፡ አርባ፡ ግርፋት፡ አንድ፡ ጐድሎ። ዘዳግ፡ ፳፭፡ ፫።

፳፭፡ በበትር፡ተመታሁ፡*ሶስት፡ጊዜ። አንድ፡ጊዜ፡ ተተወገርሁ። ሶስት፡ ጊዜ፡ የነበርሁባት፡ መርከብ፡ተሰበረች። ሌትና፡ ቀን፡ በባሕር፡ ጥልቅ፡ ተቀመጥሁ።
*የሐዋ፡ ፲፮፡ ፳፪። †የሐዋ፡ ፲፬፡ ፲፱።

፳፮፡ በምንገድ፡ ብዙ፡ ጊዜ። በውኃ፡ ፍርሃትም። በወንበዶች፡ፍርሃትም። በዘመዶቼ፡ፍርሃትም።በአሕዛብ፡ፍርሃትም። ባገርም፡ በፍርሃት። በምድረ፡ በዳም፡ በፍርሃት። በባሕርም፡ በፍርሃት። ባሰተኞች፡ ወንድሞችም፡ በፍርሃት።

፳፯፡ በድካምና፡ በችጋር። በትጋት፡ ብዙ፡ ጊዜ። በራብ፡ በጥማትም። በጾምም፡ብዙ፡ጊዜ። በብርድና፡ በራቁትነት። ም፡ ፮፡ ፭።

፳፰፡ ሚደዋ፡ ነገርም፡ ሳይቈጠር፡ ዕለት፡ ዕለት፡ የምድርሰብኝ፡ያብያተ፡ክርስቲያናት፡ ሁሉ፡ *ተካዜና ት። የሐዋ፡ ፳፡ ፲፰።

፳፱፡ ማነው፡ የሚደክም፡ እኔም፡ ላልደክምን። ማነው፡ የሚሰናከል፡ እኔም፡ ላልቃጠልን።
፩፡ ቆሮ፡ ፱፡ ፳፪።

፴፡ ትምክሕትስ፡ ደገባ፡ እንደ፡ ሆነ፡ በድካሜ፡ እመካለሁ። ም፡ ፲፪፡ ፭።

፴፩፤ የዘላለም፡የተባረከ፡እግዚአብሔር፡የየሱስ፡ ክርስቶስም፡ የጌታችን፡ አባት፡ አስት፡ እንደልናገር፡ ያውቃል። ም፡ ፩፤ ፶፫።

፴፪፤ በደማስቀ፡የአሬጣስ፡ንጉሥ፡የጭፍሮቹ፡አለቃ፡የደማስቀን፡አገር፡አስጠበቀ፡ሊይዘኝ፡ወዶ።

፴፫፤ በቅጥር፡ ላይ፡ ባለውም፡ ምስኮት፡ በንቀብ፡ አወረዱኝ፡ ከጁም፡ አመለጥሁ።

የሐዋ፡ ፱፤ ፳፬፤ ፳፭።

## ምዕራፍ፡ ፲፪፤

፩፤ እመካ፡ዘንድ፡ አይረባኝም። ወደ፡ ራእይ፡ጌታም፡ ወደ፡ ተገለጠበቱ፡ እሔደለሁና።

፪፤ አንድ፡ ሰው፡ በክርስቶስ፡ አውቃለሁ፡ ካሥራ፡ አራት፡ አመት፡ በፊት። በሥጋ፡ እንደሆን፡ አላውቅም፡ ያለ፡ሥጋም፡ እንደሆን፡አላውቅም። እግዚአብሔር፡ ያውቃል። ወደ፡ሶስተኛው፡ሰማይ፡እንደ፡ ተነጠቀ።

፫፤ እኔም፡እንደሁ፡ያለውን፡ሰው፡አውቀዋለሁ። በሥጋ፡ እንደሆነ፡ ወይም፡ ያለ፡ ሥጋ፡ አላውቅም። *እግዚአብሔር፡ ያውቃል። *ም፡ ፲፩፤ ፲፩።

፬፤ ወደ፡ ተድላ፡ ገነት፡ እንደ፡ ተነጠቀ፡ የማይነገርም፡ነገር፡ሰማ፡ሰውም፡ይናገረው፡ዘንድ፡አይቻልም።

፭፤ በዚህ፡ እንደሁ፡ እመካለሁ፡ በሰውነቴ፡ ግን፡ አልመካም፡ *በመከራዬ፡ እንጂ። *ም፡ ፲፩፤ ፴።

፮፤ መመካትም፡ ብሻ፡ ሰነፍ፡ አይደለሁም፡ እውነት፡ እናገራለሁና። ነገር፡ግን፡እራራላችኋለሁ፡ለማንም፡ ስለኔ፡ ታላቅ፡ ነገር፡ እንደይመሰለው፡ ካየው፡ ከሰማውም፡ የሚበልጥ። *ም፡ ፲፤ ፰። ፍ፡ ፲፩፤ ፲፯።

፯፤ ስለ፡ ተገለጠልኝም፡ ታላቅነት፡ እንደልጓደድ፡ ሥጋዬን፡ የሚወጋው፡ ተሰጠኝ፡ የሰይጣን፡ መለክተኛ፡ *ያቈስለኝ፡ ዘንድ፡ እንደልጓደድ።

*ኢዮብ፡ ፪፤ ፯።

፰፤ ስለዚህም፡ ወደ፡ ጌታ፡ ለመንሁ፡ ሶስት፡ ጊዜ፡ ከኔ፡ ያርቀው፡ ዘንድ።

፱፤ አለኝም፡ ጸጋዬ፡ ይበቃሃል፡ ኃይሌ፡ በድካም፡ ይፈጸማልና። የሚበልጠውንም፡ እኔ፡ በድካሜ፡ እመካለሁ፡ የክርስቶስ፡ ኃይል፡ ያድርብኝ፡ ዘንድ።

፲፤ ስለዚህም፡በድካሜ፡ደስ፡ይለኛል፡በስድብም፡ በመከራም፡ በስደትም፡ በመጨነቅም፡ ስለ፡ ክርስቶስ። በደከምሁ፡ ጊዜ፡ የዚያን፡ ጊዜ፡ እበረታለሁና።

ፊል፡ ፬፤ ፲፫።

፲፩፤ አሁንም፡ ሰነፍ፡ ሆንሁ፡ በመመካቴ፡ እላንተ፡ የግድ፡ ብላችሁኛልና፡ እኔ፡ግን፡በላንተ፡ዘንድ፡ ይገባኛል፡ ትመሰከሩልኝ፡ ዘንድ፡ እኔ፡ አንደኛ፡ ከፊተኞች፡ ሐዋርያት፡ አልጐድልምና፡ ምንም፡ እኔ፡ ምናምን፡ ብሆን።

፲፪፤ ነገር፡ ግን፡ የሐዋርያትን፡ ምልክት፡ በመካከላችሁ፡ ፈጽሜ፡ አደረግሁ። በትዕግሥት፡ ሁሉ፡ በምልክትም፡ በተአምራትም፡ በኃይልም። ም፡ ፲፩፤ ፭።

፲፫፤ ምንድር፡ ነው፡ የጐደላችሁ፡ ከሌሎች፡ አብያተ፡ ክርስቲያናት፡ እላንተን፡ *ካለመክበደ፡በቀር። ይህነን፡ ኃጢአት፡ ይቅር፡ በሉኝ። *ም፡ ፲፩፤ ፱።

፲፬፤ ይህ፡ እነሆ፡ ሶስት፡ ጊዜ፡ ነው፡ ከተዘጋጀሁ፡ ወደላንተ፡እመጣ፡ዘንድ፡አልከብድባችሁምም። ከብታችሁን፡ የምሻ፡ አይደለሁምና፡ እላንተን፡እንጂ፡ በልጆችም፡ አይገባም፡ላባቶቻቸው፡ከብት፡ ይሰበስቡ፡ ዘንድ፡ አባቶች፡ ለልጆች፡ እንጂ። ም፡ ፲፫፤ ፩።

፲፭፤ እኔም፡ እወደለሁ፡ እሰጥ፡ ዘንድ፡ ጉልበቴንም፡ *እለውጥ፡ ዘንድ፡ ስለ፡ ነፍሳችሁ። እኔስ፡ ብወደችሁ፡ እላንተ፡ ፍቅሬን፡ ታቀላላችሁ።

*ፊል፡ ፪፤ ፲፯።

፲፮፤ እንደሁም፡ ይሁን፡ አላከበድሁባችሁም፡ ነገር፡ግን፡ እኔ፡ መካር፡ ነኝና፡ በተንኰል፡ ወሰድኋችሁ።

፲፯፤ ወይስ፡ ባንድ፡ ሰው፡ ወደላንተ፡ በላክሁት፡ አንደኛ፡ በርሱ፡ እጅ፡ ወሰድሁባችሁን።

፲፰፤ ቲቶስን፡ ለመንሁት፡ ከርሱም፡ ጋራ፡ አንድ፡ ወንድም፡ ሰደድሁ። ወይስ፡ ቲቶስ፡ ሳሳባችሁን። ሁላችንስ፡ ባንድ፡ መንፈስ፡ እንሔድ፡ የለነምን። አንድስ፡ ፍለጋ፡ እንከተል፡ የለነምን።

*ም፡ ፰፤ ፯፤ ፲፯፤—፲፰።

፲፱፤ ደግሞ፡ ይመስላችኋልን፡ ስለ፡ ስውነታችን፡ ለላንተ፡ እንድንናገር። በእግዚአብሔር፡ ፊት፡ በክርስቶስ፡ እንናገራለን። ይህም፡ ሁሉ፡ ወዳጆቼ፡ለመሠራታችሁ፡ ነው።

፳፤ እኔ፡ እፈራለሁና፡ ወደላንተ፡ *በመጣሁ፡ ጊዜ፡ እንደላገኘቻሁ፡ እንደ፡ ወደድሁ። እኔንም፡ እላንተ፡ አታገኙኝም፡ እንደ፡ወደዳችሁ። ምን፡አልባት፡ መለያየት፡ ያለባችሁ፡ እንደሆን፡ ወይም፡ ቅናት፡ ቍጣም፡ ቢሆን። ጸብም፡ ቢሆን፡ ወይም፡ ማንጐርጐር። ዋዛም፡ ቢሆን፡ ተትዕቢትም፡ ቢሆን፡ ሁከትም፡ ቢሆን። *ም፡ ፲፤ ፪። †፩፤ ቆሮ፡ ፬፡ ፯።

፳፩፤ ወደላንትም፡ ደግሞ፡ በመጣሁ፡ ጊዜ፡ አምላኬ፡ ወደላንት፡ እንደያዋርደኝ፡አዝንማለሁ፡ለብዙ፡ ሰዎች፡ *ኃጢአት፡ ከሰሩት፡ አስቀድሞ። ንስሐም፡ አልገቡም፡ ከርኵሰና፡ ከዝሙትም፡ከሴሰኝነትም፡ ካደረጓት። *ም፡ ፪፤ ፩። ፍ፡ ፲፫፤ ፪።

## ምዕራፍ፡ ፲፫፤

፩፤ እነሆ፡ ይህ፡ ሶሰተኛዬ፡ነው፡ወደላንት፡ስመጣ። *በሁለት፡ ምስክሮች፡ አፍ፡ ወይም፡ በሶስት፡ ነገር፡ ሁሉ፡ ይጸናል። *ዘዳግ፡ ፲፱፤ ፲፭።

፪፤ ቀድሞም፡ አልኋችሁ፡ ደግሞም፡አሁን፡እላችኋለሁ፡ እንደለሁ፡ ሁለት፡ ጊዜ፡ ከላንት፡ ጋራ፡ሳለሁ፡ ከላንት፡ ርቄም፡ ይህነን፡ እጽፍላችኋለሁ፡ አስቀድመው፡ ኃጢአት፡ ለሰሩት፡ ሰዎች፡ ለቀሩትም፡ ሁሉ፡ ተመልሼ፡ ወደላንት፡በመጣሁ፡ጊዜ፡የምራራላችሁ፡ አይደለሁም።

፫፤ የክርስቶስ፡ ምልክት፡ ትሻላችሁና፡ እርሱ፡ በኔ፡

እንደ፡ናገር። በላንት፡ የማይደክመው፡ ነገር፡ ግን፡ የ
ሚበረታባችሁ።
፬፤ እርሱም፡በድካም፡*ቢሰቀል፡በእግዚአብሔር፡
ኀይል፡ ሕያው፡ ነውና። እኛም፡ ከርሱ፡ጋራ፡ደከምነ፡
ነገር፡ ግን፡ ሕያዋን፡ ነነ፡ ወደላንት፡ በሆነች፡ በእግዚአ
ብሔር፡ ኀይል። *ፊል፡ ፪፡ ፯፡ ፰።
፭፤ ራሳችሁን፡ መርምሩ፡ በሃይማኖት፡ ቈማችሁ፡
እንደሆን። *ራሳችሁን፡ ፈትኑ። ወይስ፡ አታውቁም
ን፡ የሱስ፡ ክርስቶስ፡ እንደደረባችሁ። ይህም፡ ካል
ሆነ፡ ያልጸናችሁ፡ ናችሁ። *፩፡ ቆሮ፡ ፲፩፡ ፳፰።
፮፤ እኔ፡ ግን፡ ተስፋ፡ አደርጋለሁ፡ እንድታውቁ፡ እ
ኛ፡ ያልጸናነ፡ እንዳልሆነ።
፯፤ ወደ፡ እግዚአብሔርም፡ እለምናለሁ፡እላንት፡
ክፉ፡ እንዳትሰሩ፡ የኛ፡ ክብር፡ እንዲታወቅ፡ አይደለ
ም፡ እላንት፡ መልካም፡ እንድትሰሩ፡ ነው፡ እንጂ።
እኛም፡ እንደ፡ ተጠቁ፡ ሰዎች፡ እንሆናለን።
፰፤ እውነትን፡እንጣላ፡ዘንድ፡አንችልምና። እኛ፡
ከውነት፡ ጋራ፡ ነነ፡ እንጂ።
፱፤ ደስ፡ ይለናልና፡ ደካሞች፡ ብንሆን፡ እላንትም፡
ኀያላን፡ ብትሆኑ። ከዚህም፡ ጋራ፡ እንጸልይላችኋለ
ን፡ ፈጹማን፡ ትሆኑ፡ ዘንድ።

፲፤ ስለዚህም፡ ይህን፡ ነገር፡ ከላንት፡ ርቄ፡ እጽፍላ
ችኋለሁ፡ እኔ፡ በመጣሁ፡ ጊዜ፡ለመቅጣት፡ እንዳልበ
ረታ፡ ጌታ፡ በሰጠኝ፡ *ስልጣን፡ ለመሠራታችሁ፡ለመ
ፈረሳችሁም፡አይደለም። *ም፡ ፲፡ ፲፩። †ም፡ ፲፡ ፰።
፲፩፤ አሁንም፡ ወንድሞቼ፡ሆይ፡ *ደስ፡ይበላችሁ።
ፈጹማን፡ ሁኑ። ባንድ፡ አሳብ፡ሁኑ። በመካከላችሁ፡
ፍቅር፡ ይሁን። እግዚአብሔርም፡ †የፍቅርና፡ የሰላ
ም፡ አምላክ፡ ከላንት፡ ጋራ፡ ይሆናል። *ፊል፡ ፬፡ ፬።
†ሮሜ፡ ፭፡ ፴፫።
፲፪፤ እርሱ፡ በርሳችሁ፡ ተገናኙ፡ በተቀደሰች፡ መሳ
ም። ቅዱሳን፡ ሁሉ፡ እንደት፡ ናችሁ፡ ይልዋችኋል።
፩፡ ቆሮ፡ ፲፮፡ ፳።
፲፫፤ የጌታችን፡ የየሱስ፡ክርስቶስ፡ጸጋ፡ የእግዚአብ
ሔርም፡ ፍቅር፡ የመንፈስ፡ ቅዱስም፡ አንድነት፡ከሁ
ላችሁ፡ ጋራ፡ ይሁን። አሜን።

ተፈጸመች፡ መልእክት፡ ሁለተኛዪቱ፡ ወደ፡ ቆሮንቶስ፡ ሰዎች። ተጻፈች፡ ከፊልጵስዩስ፡ ከመቄዶንያ፡ አገር፡ በቲቶስና፡ በሉቃስ፡ እጅ።

---

# የሐዋርያ፡ የጳውሎስ፡ መልእክት፡ ወደ፡ ገላትያ፡ ሰዎች።

## ምዕራፍ፡ ፩፤

፩፤ ከሐዋርያው፡ ከጳውሎስ። *ከሰው፡ የተላከ፡
አይደለም፡ በሰውም፡ አይደለም፡ በየሱስ፡ ክርስቶ
ስ፡ እንጂ፡ ከሙታን፡ †ባስነሣውም፡ በአምላክ፡ በ
አብ። *ቍ፡ ፲፩፡ ፲፪። †የሐዋ፡ ፫፡ ፭።
፪፤ ከኔ፡ ጋራ፡ ካሉም፡ ከወንድሞች፡ ሁሉ፡ወደ፡ገላ
ትያ፡ አብያተ፡ ክርስቲያናት።
፫፤ ጸጋ፡ ለላንት፡ ይሁን፡ ሰላምም፡ ከአብ፡ ካምላ
ክ፡ ከጌታችንም፡ ከየሱስ፡ ክርስቶስ።
*ሮሜ፡ ፩፡ ፯። ፩፡ ቆሮ፡ ፩፡ ፫።
፬፤ *ራሱን፡ የለወጠ፡ ስለ፡ ኃጢአታችን፡ ከዚህ፡
ተከክፉ፡ ዓለም፡ ያድነነ፡ ዘንድ፡ በእግዚአብሔር፡ ፈ
ቃድ፡ ባባታችን። *ም፡ ፪፡ ፳። ፩፡ ጢሞ፡ ፪፡ ፮።
ቲቶ፡ ፪፡ ፲፬። †፩፡ ዮሐ፡ ፭፡ ፲፱።
፭፤ *ምስጋና፡ የሚገባው፡ ለዘላለሙ፡ አሜን።
፪፡ ጢሞ፡ ፬፡ ፲፰።
፮፤ እኔ፡ እደነቃለሁ፡ እንደት፡ቸኰላችሁ፡ ወደ፡ ሌ
ላ፡ ወንጌል፡ ተመለሳችሁ፡ ከርሱ፡ በክርስቶስ፡ ጸጋ፡ ከ
ጸራችሁ።
፯፤ ሌላ፡ ያይደለ፡ነገር፡ግን፡ሰዎች፡ *ያውኳችኋል፡
የክርስቶስንም፡ ትምህርት፡ ይለውጡ፡ ዘንድ፡ ይወ
ዳሉ። *የሐዋ፡ ፲፭፡ ፩፡ ፳፬።
፰፤ ነገር፡ ግን፡ እኛም፡ ብንሆን፡ ወይም፡ መልአክ፡
ከሰማይ፡ ቢያስተምራችሁ፡ እኛ፡ ካስተማርናችሁ፡
ሌላ። *ውጉዝ፡ ይሁን። *፩፡ ቆሮ፡ ፲፮፡ ፳፪።
፱፤ አስቀድሜ፡ እንዳልሁ፡ አሁንም፡ ደግሜ፡ እላ
ለሁ፡ ማንም፡ ቢያስተምራችሁ፡ከኛ፡ ከተቀበላችሁ
ት፡ ሌላ። ውጉዝ፡ ይሁን።
፲፤ አሁንስ፡ *ሰውንን፡ ደስ፡ አሰኛለሁ፡ ወይስ፡ እግ
ዚአብሔርን። ወይስ፡ እሻለሁ፡ ስራዬን፡ ለሰው፡ አሳ
ምር፡ ዘንድ። ለሰውስ፡ ስራዬን፡ አሳምር፡ ዘንድ፡ ብ
ወድ፡ ለክርስቶስ፡ ባርያ፡ ባልሆንሁም።
፩፡ ተሰ፡ ፪፡ ፬።
፲፩፤ *አስታውቃችኋለሁ፡ ግን፡ ወንድሞቼ፡ ሆይ፡
በኔ፡ የተማራችኋት፡ ትምህርት፡ ከሰው፡ እንዳይደ
ለች። *፩፡ ቆሮ፡ ፲፭፡ ፩፡ ፫።
፲፪፤ እኔም፡ ደግሞ፡ *ከሰው፡ አልተቀበልኋትም፡
አልተማርኋትምም፡ በየሱስ፡ ክርስቶስ፡ መገለጥ፡
ነው፡ እንጂ። *፩፡ ቆሮ፡ ፲፩፡ ፳፫።
፲፫፤ ነገሬን፡ ሰምታችኋልና፡ እንደት፡ ነበረች፡ ቀድ
ሞ፡ በአይሁድነት፡ ሳለሁ፡ የእግዚአብሔርንም፡ *አ
ብያተ፡ ክርስቲያናት፡ እጅግ፡ እንደሰደድሁ፡ እንደፈ
ረስኋቸውም። *የሐዋ፡ ፳፮፡ ፱።
፲፬፤ በአይሁዳዊ፡ ሕግም፡ እበዛ፡ ነበርሁ፡አጽንቼ

ከብዙ፡ ከወገኖቼ፡ ይልቅ፡ እጅግም፡ እቀና፡ ነበርሁ፡ አባቶቼ፡ ላስተማሩኝ።

፲፭፡ እግዚአብሔር፡ ግን፡ በወደደ፡ ጊዜ፡ *ከናቴ፡ ማሕፀን፡ ያወጣኝ፡ በጸጋውም፡ *የጸራኝ።
*ሮሜ፡ ፩፡ ፩፡፡ ኤር፡ ፩፡ ፭፡፡

፲፮፡ ልጁን፡ *እንዲገልጥብኝ፡ †አሕዛብን፡ አስተ ምር፡ ዘንድ። የዚያን፡ ጊዜ፡ አልተማከርሁም፡ ከሥ ጋና፡ ከደም፡ ጋራ። *ማቴ፡ ፲፮፡ ፲፯፡፡ †ም፡ ፪፡ ፯፡፡

፲፯፡ ወደ፡ የሩሳሌምም፡ አልወጣሁም፡ ከኔ፡ በፊ ት፡ ወደ፡ ነበሩት፡ ሐዋርያት፡ ወደ፡ ዓረብ፡ አገር፡ ሔ ድሁ፡ እንጂ። ደግሞም፡ወደ፡ደማስቀ፡ተመለስሁ።

፲፰፡ ከሦስት፡ አመትም፡ በኋላ፡ ወደ፡ የሩሳሌም፡ ሔድሁ፡ ጴጥሮስን፡ አይ፡ ዘንድ፡ ከርሱ፡ ዘንድም፡ ተ ቀመጥሁ፡ አሥራ፡ አምስት፡ ቀን። የሐዋ፡ ፱፡ ፳፮፡፡

፲፱፡ ከሌሎችም፡ሐዋርያት፡አንድም፡አላየሁም፡ ከያዕቀብ፡ ከጌታ፡ወንድም፡ በቀር። ማቴ፡ ፲፫፡ ፶፭፡፡

፳፡ ወደላንትም፡ የጸፍሁበት፡ ነገር፡ እነሆ፡ እውነ ት፡ ነው፡ በእግዚአብሔር፡ ፊት፡ አስትም፡ አልናገ ርም።

፳፩፡ ከዚያም፡በኋላ፡ወደ፡ሶርያና፡ወደ፡ ቂልቅያ፡ አገር፡ መጣሁ። የሐዋ፡ ፱፡ ፴፡፡

፳፪፡ ፊቴንም፡ አያውቁኝም፡ ነበሩ፡ የክርስቶስ፡ አብያተ፡ ክርስቲያናት፡ በይሁዳ፡ ያሉት።

፳፫፡ ነገር፡ግን፡ ይሰሙ፡ ነበር፡ አስቀድሞ፡ያሳደን፡ የነበረ፡ ቀድሞ፡ ያፈርሰው፡ የነበረውን፡ ሃይማኖት፡ ዛሬ፡ ያስተምራል።

፳፬፡ በምክንያቴም፡እግዚአብሔርን፡ያመሰግኑ፡ ነበር።

ምዕራፍ፡ ፪፡

፩፡ ካሠራ፡ አራት፡ አመትም፡ በኋላ፡ ወደ፡ የሩሳ ሌም፡ ደግሞ፡ ሔድሁ፡ ከበርናባስ፡ ጋራ፡ ቲቶስንም፡ ከኔ፡ ጋራ፡ ወሰድሁት። የሐዋ፡ ፲፭፡ ፪፡፡

፪፡ መውጣቴም፡ በተገለጠልኝ፡ ነገር፡ ሆነ፡ለአሕዛ ብም፡ የማስተምራትን፡ ትምህርት፡ገለጥሁላቸው፡ ይልቁንም፡*አለቆች፡የሚመስሉ፡በከንቱ፡የምሮጥ፡ እንደልሆን፡ ወይስ፡ አስቀድሜ፡ በከንቱ፡ የሮጥሁ።
*ቆ፦፡ ፯፡ ፱፡፡

፫፡ ቲቶስም፡ ከኔ፡ ጋራ፡ ያለው፡ አረማዊም፡ ነበረ፡ ሊገዘር፡ ግድ፡ አላሉትም። የሐዋ፡ ፲፮፡ ፫፡፡

፬፡ ነገር፡ ግን፡ *ስላሰተኞች፡ ወንድሞች፡ በኾ፡ የገቡ ብን፡ በክርስቶስ፡ ያገኘናትን፡ አርነት፡ ሊጐበኙ፡ ደገ ዙን፡ ዘንድ። *የሐዋ፡ ፲፭፡ ፳፬፡፡

፭፡ አንዲት፡ሰዓትም፡ሰንኳ፡አልተገዛንላቸውም፡ የወንጌል፡ *እውነት፡ በላንተ፡ ዘንድ፡ እንዲጸና።
*ም፡ ፫፡ ፩፡፡

፮፡ ነገር፡ግን፡አለቆች፡የሚመስሉ። እርሳቸውም፡ ማንስ፡ ይሁኑ፡አይሁኑ፡ምን፡ አግደኝ። እግዚአብሔ ር፡ ለሰው፡ ፊት፡ *አያደላምና። እሌሀ፡አንደች፡ አል ጨመሩልኝም። *የሐዋ፡ ፲፡ ፴፬፡፡

፯፡ *ነገር፡ ግን፡ ቢያዩኝ፡ እኔ፡ያልተገዘሩትን፡ለማስ ተማር፡ እንደ፡ ታመንሁ፡ ጴጥሮስ፡ እንደ፡ ታመነ፡ በግ ዙራን፡ ዘንድ። *የሐዋ፡ ፲፫፡ ፵፯፡፡

፰፡ ለጴጥሮስም፡ መልእክት፡ የሰጠ፡ በግዙራን፡ ላይ፡ ለኔም፡ ሰጠኝ፡ በአሕዛብ፡ ላይ።

፱፡ ያዕቀብና፡ *ኬፋ፡ ዮሐንስም፡ አዕማድ፡ የተባ ሉ፡ የተሰጠችኝን፡ ጸጋ፡ ባወቁ፡ ጊዜ፡ ባንድነት፡ቀኝ፡ አ ገዙኝ፡እኔን፡በርናባስንም፡እኛ፡ለአሕዛብ፡ልንቀም። እርሳቸውም፡ በግዝረት፡ ሰዎች። ዮሐ፡ ፩፡ ፵፪፡፡

፲፡ ይልቁንም፡ ድኆችን፡ እናስብ፡ ዘንድ፡ ብቻ። እ ኔ፡ ደግሞ፡ ያነን፡ አደርግ፡ ዘንድ፡ ጥሬያለሁ።
የሐዋ፡ ፲፩፡ ፴፡፡ ፲፪፡ ፳፭፡፡

፲፩፡ ጴጥሮስ፡ ግን፡ ለአንጾክያ፡ በመጣ፡ ጊዜ፡ፊት፡ ለፊት፡ ተከራከርሁት፡ ይፈረድበት፡ ዘንድ፡ ይገባ፡ነበ ርና።

፲፪፡ ከያዕቀብ፡ ዘንድ፡ ሰዎች፡ ሳይመጡ፡ ከአሕዛ ብ፡ ጋራ፡ ይበላ፡ ነበርና። በመጡም፡ ጊዜ፡ ከዚያ፡ርቆ፡ ተለየ፡ ከግዝረት፡ ሰዎች፡ ፈርቶ። የሐዋ፡ ፲፩፡ ፫፡፡

፲፫፡ በዚያውም፡ የቀሩት፡ አይሁድ፡ መሰሉ፡ በርና ባስ፡ ሰንኳ፡ በመምሰላቸው፡ እስኪወስድ፡ ድረስ።

፲፬፡ ነገር፡ግን፡ እኔ፡ ባያቸው፡ በወንጌል፡ እውነት፡ እንደይሔዱ፡ ጴጥሮስን፡አልሁት፡በሁሉ፡ ፊት። አን ተ፡ አይሁዳዊ፡ ስትሆን፡ በአሕዛብ፡ ወግ፡ ትኖራለህ፡ በአይሁድም፡ አይደለም። እንጊደህ፡ለምን፡የግድ፡ ትላለህ፡ አሕዛብ፡ ወደ፡ አይሁድ፡ ሥርዓት፡ ይገቡ፡ ዘንድ።

፲፭፡ እኛ፡ አይሁድ፡ በፍጥረታችን፡ ከአሕዛብም፡ ከኃጥኣን፡ ወገን፡ አይደለነም።

፲፮፡ እናውቃለንና፡ ሰው፡ እንዲደጸድቅ፡ ኦሪትን፡ በመስራት፡ በየሱስ፡ ክርስቶስ፡ ሃይማኖት፡ እንጂ። እኛም፡ ፈጽመን፡ በየሱስ፡ ክርስቶስ፡ አመነ፡ በክርስ ቶስ፡ ሃይማኖት፡ እንጸድቅ፡ ዘንድ፡ ኦሪትንም፡ በመ ስራት፡ አይደለም፡ ኦሪትን፡ በመስራት፡ አይጸድቅ ምና፡ ሥጋ፡ የለበስ። የሐዋ፡ ፲፭፡ ፲፡ ፲፩፡፡
ሮሜ፡ ፫፡ ፳፡ ፳፰፡፡ ኤፌ፡ ፪፡ ፰፡፡

፲፯፡ በክርስቶስም፡ እንጸድቅ፡ ዘንድ፡ የምንሻ፡ ኃ ጢአተኞች፡ ሁነን፡ ከተገኘነ። በውኑ፡ ክርስቶስ፡ የኃ ጢአትን፡ አገልጋይ፡ ነው። አይደለም።

፲፰፡ ያፈረስሁትንስ፡ ተመልሼ፡ የምሠራው፡ ከሆ ንሁ፡ በራሴ፡ መሰከርሁ፡ ትእዛዝ፡አፍራሽ፡ እንደ፡ ሆ ንሁ።

፲፱፡ እኔ፡ ግን፡ በሕግ፡ፈጽሜ፡ ለሕግ፡ሞትሁ፡ *ለእ ግዚአብሔር፡ እኖር፡ ዘንድ። *ሮሜ፡ ፯፡ ፬፡፡

፳፡ ከክርስቶስ፡ ጋራ፡ ተሰቀልሁ። ሕያው፡ ነኝ፡ እኔ ም፡ አይደለሁም፡ ክርስቶስ፡ *በኔ፡ ሕያው፡ ነው፡ እን ጂ። ይህችም፡ ሕይወት፡ ዛሬ፡ *እኔ፡ ያለሁባት፡ በሥ ጋ፡ የሃይማኖት፡ ሕይወት፡ ናት፡ በእግዚአብሔር፡ ል ጅ፡ በወደደኝ፡ †ራሱንም፡ ስለኔ፡ በለወጠ።
*ዮሐ፡ ፲፬፡ ፳፫፡፡ †ም፡ ፩፡ ፬፡፡

፳፩፤ የእግዚአብሔርን፡ጸጋ፡አልክድም።ጽድቅስ፡ በኦሪት፡ ከሆነ፡ እንኪያስ፡ ክርስቶስ፡ በከንቱ፡ ሞተ።

## ምዕራፍ፡ ፫፤

፩፤ እላንተ፡ ስነፎች፡ የገላትያ፡ ሰዎች። ማነው፡ ያታለላችሁ፡ ለጽድቅ፡ እንዳትታዘዙ። ቀድሞስ፡ የሱስ፡ ክርስቶስ፡ ባይኖችሁ፡ፊት፡ ተሰቅሎ፡ተስሎባችሁ፡ ነበር።

፪፤ ይህነን፡ ብቻ፡ ከላንተ፡አውቅ፡ ዘንድ፡እሻለሁ። ኦሪትንን፡ በመስራት፡ መንፈስ፡ቅዱስን፡ወሰዳችሁ፡ ወይስ፡ ሃይማኖትን፡ በመስማት።

፫፤ እንዲህን፡ አታስተውሉም። በመንፈስ፡ ጀምራችሁ፡ አሁን፡ በሥጋን፡ ትጨርሳላችሁ።

፬፤ በውኑ፡ እንዲህ፡ ያለ፡ ድካም፡ በከንቱ፡ ተቀበላችሁ። በከንቱም፡ በሆነ።

፭፤ መንፈስ፡ ቅዱሰን፡ የሚሰጣችሁ፡ ኃይልም፡ የሚያደርግባችሁ። ኦሪትንን፡በመስራት፡ነው፡ወይስ፡ ሃይማኖትን፡በመስማት።

፮፤ አብርሃም፡ በእግዚአብሔር፡ እንደመነ፡ ጽድቅም፡ሁኖ፡ እንደ፡ ተቈጠረለት። ዘፍ፡ ፲፭፡ ፮።

፯፤ እንግዲህም፡ እወቁ፡ ሃይማኖት፡ ያላቸው፡ ሰዎች፡ እለዚያ፡ የአብርሃም፡ ልጆች፡ እንደሆኑ።

፰፤ አስቀድሞም፡መጽሐፍ፡አየ፡ እግዚአብሔር፡ በሃይማኖት፡ አሕዛብን፡ እንዲያጸድቅ፡ አስቀድሞም፡ ለአብርሃም፡ነገረው፡ እንዲህ፡ ሲል። ባንተ፡ ይባረካሉ፡ አሕዛብ፡ ሁሉ። *ዘፍ፡ ፲፪፡ ፫።

፱፤ ስለዚህም፡ ከሃይማኖት፡ ያሉ፡ ካመነው፡ ከአብርሃም፡ ጋራ፡ ይባረካሉ። ሮሜ፡ ፬፡ ፲፮።

፲፤ ኦሪትን፡ በማድረግ፡ያሉ፡ ሁሉ፡እርሳቸው፡ከመርገም፡በታች፡ናቸውና። እንደ፡ተጻፈ። *ርጉም፡ነው፡ በዚህ፡ ሕግ፡ የተጻፈውን፡ ሁሉ፡ የማይጠብቅ፡ ያደርገው፡ ዘንድ። *ዘዳግ፡ ፳፯፡ ፳፮።

፲፩፤ ኦሪትን፡ በመሰራት፡ ግን፡ ማንም፡ አይጸድቅም፡በእግዚአብሔር፡ዘንድ። ይህም፡የተገለጠ፡ነው። *ጻድቅ፡ በሃይማኖት፡ ይድናልና። *አንባ፡ ፪፡ ፬። ሮሜ፡ ፩፡ ፲፯።

፲፪፤ ኦሪት፡ ግን፡ ከሃይማኖት፡ አይደለችም፡ የሚያደርጋት፡ሰው፡ይኖርባታል፡እንጂ። ዘሌዋ፡ ፲፰፡ ፭።

፲፫፤ ክርስቶስ፡ ከኦሪት፡ መርገም፡ገዛነ፡ ስለኛ፡ *መርገም፡ ሁኖ። †ተጽፍዋልና፡ እንዲህ፡ ሲል። ርጉም፡ ነው፡ በንጨት፡ ላይ፡ የተሰቀለ፡ ሁሉ።

*ሮሜ፡ ፰፡ ፫። ፪፡ ቆሮ፡ ፭፡ ፳፩። †ዘዳግ፡ ፳፩፡ ፳፫።

፲፬፤ የአብርሃም፡ በረከት፡ ለአሐዛብ፡ ይሆን፡ ዘንድ፡ በክርስቶስ፡ የሱስ። እኛ፡ የመንፈስ፡ቅዱስን፡ተስፋ፡ እንወስድ፡ ዘንድ፡ በሃይማኖት።

፲፭፤ ወንድሞቼ፡ ሆይ፡ እኔ፡እናገራለሁ፡ ለሰው፡ እንዲገባ። የሰው፡ ኪዳን፡ የጸናች፡ከሆነች፡ ማንም፡ አይንቃትም፡ ከርስዋም፡ አንዳች፡ አይለውጥም።

፲፮፤ ለአብርሃም፡ ግን፡ለዘሩም፡ተስፋ፡ተደረገች። ለዘሮችም፡ አይልም፡ ለብዙ፡ እንዲባል። ላንድ፡ እንዲባል፡ እንጂ፡ ለዘርህ። እርሱም፡ ክርስቶስ። ዘፍ፡ ፳፪፡ ፲፰።

፲፯፤ ይህነንም፡ እላለሁ። እግዚአብሔር፡ የክርስቶስ፡ አስቀድሞ፡ ያቀመቸውን፡ኪዳን፡አራት፡መቶ፡ ከሠላሳ፡ አመት፡ በኋላ፡ *የሆነች፡ ሕግ፡ አታፈርሰውም፡ ተስፋውን፡ታስቀረው፡ ዘንድ። *ዘፀአ፡ ፲፪፡ ፵።

፲፰፤ መውረስም፡ በኦሪት፡ ከሆነ፡ በተስፋ፡ ባይሆን፡ ነበር፡ እግዚአብሔር፡ ግን፡ ለአብርሃም፡ በተስፋ፡ ሰጥቶታል።

፲፱፤ ኦሪት፡ እንግዲህ፡ ለምንድር፡ ናት። *ኦሪትስ፡ ስለ፡ ኃጢአት፡ ተሰራች፡ ተስፋ፡ ያለው፡ ዘር፡ እስኪመጣ፡ ድረስ፡ *ከመላእክት፡ ጋራም፡ተሰራች፡በመካከለኛው፡ እጅ። *ሮሜ፡ ፭፡ ፳። †የሐዋ፡ ፯፡ ፶፫።

፳፤ መካከለኛውም፡ ላንድ፡ አይደለም፡ እግዚአብሔር፡ግን፡አንድ፡ነው።

፳፩፤ ኦሪትስ፡ የእግዚአብሔርንን፡ ተስፋ፡ ትጻላለች። አይደለም። ሕይወትን፡ መስጠት፡ የሚቻላት፡ ኦሪት፡ከተሰጠች፡ጽድቅ፡ በውነት፡በኦሪት፡ ትሆን፡ ዘንድ፡ ነበረች። ሮሜ፡ ፰፡ ፪—፬።

፳፪፤ ነገር፡ ግን፡ *መጽሐፍ፡ ሁሉን፡ ከኃጢአት፡ በታች፡ ዘጋው፡ ተስፋ፡ በየሱስ፡ ክርስቶስ፡ ሃይማኖት፡ ለሚያምኑ፡ ትሰጥ፡ ዘንድ። *ሮሜ፡ ፫፡ ፱፡ ፲፱። ሮሜ፡ ፲፩፡ ፴፪።

፳፫፤ ሃይማኖትም፡ ሳትመጣ፡ ከኦሪት፡ በታች፡ ተጠብቀን፡ ነበርነ፡ ተዘግተን፡ ለሃይማኖት፡ ይገለጥ፡ ዘንድ፡ ያለው። ም፡ ፬፡ ፫።

፳፬፤ ኦሪትስ፡ ለኛ፡ ጠባቂ፡ ነበረች፡ እስከ፡ ክርስቶስ፡ በሃይማኖት፡ እንጸድቅ፡ ዘንድ።

፳፭፤ ሃይማኖትም፡ ከመጣች፡ በመሪ፡ እጅ፡ ደግሞ፡ አንሆንም። ሮሜ፡ ፲፡ ፬።

፳፮፤ እላንት፡ ሁላችሁ፡ የእግዚአብሔር፡ ልጆች፡ ናችሁና፡ በየሱስ፡ ክርስቶስ፡ ሃይማኖት። ዮሐ፡ ፩፡ ፲፪። ሮሜ፡ ፰፡ ፲፯።

፳፯፤ እላንትም፡ ሁላችሁ፡ በክርስቶስ፡ *የተጠመቃችሁ፡ †ክርስቶስን፡ ለበሳችሁ። *ሮሜ፡ ፮፡ ፫። †ሮሜ፡ ፲፫፡ ፲፬።

፳፰፤ በዚያም፡ አይሁዳዊ፡ የለም፡ አረማዊም፡ ባርያም፡የሰው፡ ልጅም፡ ወንድም፡ ሴትም። እላንት፡ ሁላችሁ፡ በክርስቶስ፡ የሱስ፡ አንድ፡ ናችሁና። ሮሜ፡ ፲፡ ፲፪። ፩፡ ቆሮ፡ ፲፪፡ ፲፫።

፳፱፤ ለክርስቶስም፡ ከሆናችሁ፡ እላንት፡ የአብርሃም፡ ልጆች፡ ናችሁ፡ በተስፋም፡ ወራሾች፡ ናችሁ። ቍ፡ ፯። ሮሜ፡ ፱፡ ፯።

## ምዕራፍ፡ ፬፤

፩፤ እኔም፡ እላለሁ፡ ወራሽ፡ ሕፃን፡ በሆነበት፡ ዘመን፡ ሁሉ፡ በርሱና፡በባርያ፡መካከል፡ ልዩነት፡የለውም፡ እርሱ፡ የሁሉ፡ ጌታ፡ ሲሆን።

፪፤ ነገር፡ግን፡ ካለቀችና፡ ከመጋቦች፡ በታች፡ነው፡ አ
ባቱ፡ እስካደረገለት፡ ዘመን፡ ድረስ።
፫፤ እኛም፡ እንደሁ፡ ደግሞ፡ ሕፃናት፡ ሳለን፡ ለዚ
ህም፡ ምሳሌ፡ እንገዛ፡ ነበርን።    ም፡ ፫፤ ፳፫፡፡ ፭፤ ፩፡፡
ቆለ፡ ፪፤ ፳፡፡
፬፤ የዘመኑ፡ ፍጸሜ፡ ግን፡ *በደረሰ፡ጊዜ፡ እግዚአብ
ሔር፡ ልጁን፡ ላከ፡ ከሴት፡ የተወለደውን፡ ከኦሪት፡
በታችም፡ የሆነውን።    *ኤፌ፡ ፩፤ ፲፡፡
፭፤ ከኦሪት፡ በታች፡ ያሉትን፡ ይበዥ፡ ዘንድ፡የልጅ
ነትን፡ መዝገብ፡ እንወስድ፡ ዘንድ።    ም፡ ፫፤ ፲፫፡፡
፮፤ ልጆችም፡ በሆናችሁ፡ ጊዜ፡ እግዚአብሔር፡ የል
ጁን፡ መንፈስ፡ በልባችሁ፡ ላከ፡ እንደሀ፡ የሚጸራ፡
አባታችን፡ አብ።    ሮሜ፡ ፰፤ ፲፭፡፡
፯፤ እንጊደሀ፡ ባርያ፡ አይደለህም፡ ልጅ፡ እንጂ።
ልጅም፡ከሆንህ፡የእግዚአብሔርም፡ወራሽ፡ ነህ፡ በክ
ርስቶስ።    ም፡ ፫፤ ፳፱፡፡ ሮሜ፡ ፰፤ ፲፮፤ ፲፯፡፡
፰፤ ነገር፡ ግን፡ የዚያን፡ ጊዜ፡ አምላክን፡ ሳታውቁ፡
ተገዛችሁ፡ በባሕርያቸው፡ አማልክት፡ ላልሆኑ።
፱፤ አሁን፡ ግን፡ ፈጽማችሁ፡ እግዚአብሔርን፡አወ
ቃችሁ፡ ይልቁንም፡ እግዚአብሔር፡ እላንትን፡ አወቃ
ችሁ። እንደትም፡ ትመለሳላችሁ፡ ደግሞ፡ ወደ፡ደከ
መቸ፡ ወደ፡ ተናቀችም፡ አምሳል፡ የምትወድዋት፡
ሁለተኛ፡ ደግሞ፡ ትገዙላት፡ ዘንድ።
፲፤ ቀን፡ ኢየቈጠራችሁ፡ ወራትም፡ ጊዜም፡ አመ
ታትም።    ሮሜ፡ ፲፬፤ ፭፡፡
፲፩፤ እፈራችኋለሁ፡ በከንቱ፡ በላንት፡ የደከምሁ፡
እንደልሆን።    ፪፤ ዮሐ። ቍ፡ ፰፡፡
፲፪፤ እንደኔ፡ ሁኑ፡ እኔም፡ ደግሞ፡ እንደላንት፡ሁኛ
ለሁና። እላንት፡ ወንድሞች፡ እለምናችኋለሁ። አን
ደችም፡ አልበደላችሁኝም።    ፪፤ ቆሮ፡ ፪፤ ፭፡፡
፲፫፤ እላንትም፡ ታውቃላችሁ፡ በሥጋዬ፡ ድካም፡
አስቀድሜ፡ እንደስተማርኋችሁ።    ፩፤ ቆሮ፡ ፪፤ ፫፡፡
፲፬፤ በሥጋዬም፡ ያለችውን፡ ፈተና፡ አልናቃችኋት
ም፡በዚያም፡አልተጸየፋችሁኝም። ነገር፡ግን፡ እንደ፡
እግዚአብሔር፡ መልአክ፡ ተቀበላችሁኝ፡ እንደ፡ የሱ
ስ፡ ክርስቶስም።
፲፭፤ አሁንስ፡ ወደት፡ አለ፡ መመሰገናችሁ። እመ
ሰክርላችሁማለሁ፡ በቻላችሁስ፡ዓይናችሁን፡ አውጥ
ታችሁ፡ በሰጣችሁኝ።
፲፮፤ በውኑ፡ ጸላትን፡ ሆንኋችሁ፡ በውነት፡ ስላስተ
ማርኋችሁ።    አሞ፡ ፭፤ ፲፡፡
፲፯፤ የሚቀኑባችሁ፡ መልካም፡ ነገር፡ አይሹላችሁ
ም፡ ነገር፡ ግን፡ ይሻሉ፡ ይዘጏችሁ፡ ዘንድ፡ እላንት፡ እ
ንድትቀኑባቸው።    ም፡ ፩፤ ፯፡፡
፲፰፤ ለመልካም፡ነገር፡ ግን፡ ሁለግዜ፡ትቀኑ፡ዘንድ፡
ይሻላል፡ ከላንትም፡ ዘንድ፡ ባለሁበት፡ ጊዜ፡ ብቻ፡ አ
ይደለም።

፲፱፤ ልጆቼ፡ ሆይ፡ እኔ፡ ደግሞ፡ ሁለተኛ፡ምጥ፡የም
ያዝባችሁ፡ ክርስቶስ፡ እስኪሣልባችሁ፡ ድረስ።
፩፤ ቆሮ፡ ፬፤ ፲፭፡፡
፳፤ እኔ፡ እመኘ፡ ነበርሁ፡ አሁን፡ በላንት፡ እሆን፡ ዘ
ንድ፡ ድምጼንም፡ ልለወጥ፡ በላንት፡ ስለ፡ተቸገርሁ።
፳፩፤ ንገሩኝ፡ እላንት፡ ከኦሪት፡ በታች፡ ትኖሩ፡ ዘን
ድ፡ የምትወደ፡ ኦሪትን፡ አትሰሙምን።
ቍ፡ ፱፡፡ ም፡ ፫፤ ፳፫፡፡
፳፪፤ ተጽፏዋልና፡ ለአብርሃም፡ ሁለት፡ ልጆች፡ እ
ንደ፡ ነበሩት፡ *አንዱ፡ ከባርያዪቱ፡ †ሁለተኛውም፡
ከመቤቲቱ።    *ዘፍ፡ ፲፮፤ ፲፭፡፡ †ዘፍ፡ ፳፩፤ ፪፡፡
፳፫፤ ነገር፡ ግን፡ የባርያዪቱ፡ ልጅ፡ እንደ፡ ሥጋ፡ ተወ
ለደ፡ ከመቤቲቱ፡ ግን፡ የተወለደው፡ በተስፋ፡ ነው።
ሮሜ፡ ፱፤ ፯—፱፡፡
፳፬፤ እርሳቸውም፡ ምሳሌ፡ ናቸው። እሌህ፡ ሁለ
ቱ፡ ሕገጋት፡ናቸውና። አንዲቱ፡ከደብረ፡ ሲና፡ልጆች፡
*ለባርነት፡ የምትወልድ፡ እርስዋም፡ አጋር፡ ናት።
*ም፡ ፭፤ ፩፡፡ ሮሜ፡ ፰፤ ፲፭፡፡
፳፭፤ አጋር፡ባረብ፡አገር፡ያለች፡ደብረ፡ ሲና፡ ናትና።
እርስዋም፡ ዛሬ፡ ያለችውን፡ የሩሳሌም፡ ትመስላለ
ች። በባርነትም፡ አለች፡ እርስዋ፡ ከልጆችዋ፡ ጋራ።
፳፮፤ የላይኛዪቱ፡ የሩሳሌም፡ ግን፡ እርስዋ፡ እመ
ቤት፡ ናት፡ እርስዋም፡ የኛ፡ የሁላችን፡ እናት፡ የምት
ሆን።    ዕብ፡ ፲፪፤ ፳፪፡፡
፳፯፤ *ተጽፏዋልና፡ እንደሀ፡ ሲል። ደስ፡ ይበልሽ፡
አንቺ፡መካን፡ ወልደሽ፡ የማታውቂ። እጅግ፡ደስ፡ ይ
በልሽ፡ እልልም፡ በዪ፡ አንቺ፡ አምፀሽ፡ የማታውቂ።
የመካኒቱ፡ ልጆች፡ በዝተዋልና፡ ባል፡ካላቱ፡ ይልቅ።
*ኢሳ፡ ፶፬፤ ፩፡፡
፳፰፤ እኛ፡ ግን፡ ወንድሞቼ፡ ሆይ፡የተስፋ፡ ልጆች፡
ነን፡እንደ፡ ይስሐቅ።    ሮሜ፡ ፱፤ ፯፡፡
፳፱፤ ነገር፡ግን፡ ያን፡ጊዜ፡እንደ፡ሥጋ፡የተወለደው፡
እንደ፡ መንፈስ፡የተወለደውን፡እንደሳደደው። ዛሬ
ም፡ እንደሀ፡ ነው።
፴፤ ነገር፡ ግን፡ ምን፡ ይላል፡ *መጽሐፉ። ባርያዪቱ
ን፡ አውጣ፡ ልጅዋንም። የባርያ፡ ልጅ፡ አይወርስም
ና፡ ከመቤት፡ ልጅ፡ ጋራ።    *ዘፍ፡ ፳፩፤ ፲፤ ፲፪፡፡
፴፩፤ አሁንም፡ ወንድሞቼ፡ ሆይ፡ እኛ፡ የባርያ፡ ል
ጆች፡ አይደለነም፡ የመቤት፡ እንጂ።    ም፡ ፫፤ ፳፱፡፡

## ምዕራፍ፡ ፭፤

፩፤ አሁንም፡ክርስቶስ፡ ባወጣነው፡ በሰው፡ ልጅነ
ት፡ጽኑ፡ ደግሞም፡ አትገዙ፡ ለባርነት፡ቀምበር።
ም፡ ፬፤ ፭፤ ፴፩፡፡ የሐዋ፡ ፲፭፤ ፳፡፡
፪፤ እነሆ፡እኔ፡ ጳውሎስ፡ እላችኋለሁ። የተገዛራች
ሁ፡ እንደሆን፡ ክርስቶስ፡ ምንም፡ አይረባችሁም።
፫፤ ደግሞም፡ ለተገዘረ፡ ሰው፡ ሁሉ፡ እመሰክራለ
ሁ፡በኦሪት፡ ያለውን፡ ሁሉ፡ መጠበቅ፡ እንዲገባው።

፬፤ ከክርስቶስ፡ *ጠፋችሁ፡ እላንት፡ በኦሪት፡ የም
ትጸድቁ፡ ከጸጋው፡ ወደቃችሁ። *ም፡ ፪፡ ፳፩።
ሮሜ፡ ፯፤ ፪፤ ፫።
፭፤ እኛ፡ግን፡ በመንፈስ፡ ከሃይማኖት፡ እንጸድቅ፡
ዘንድ፡ ተስፋ፡ እናደርጋለን። ፪፤ ጢሞ፡ ፬፤ ፰።
፮፤ በክርስቶስ፡ የሱስ፡ለግዝረት፡ አንዳች፡አይቻላ
ትምና፡ለቍላፍነትም፡ በፍቅር፡ለምትሰራ፡ ሃይማኖ
ት፡ እንጂ። ም፡ ፮፤ ፲፭። ፩፤ ቆሮ፡ ፯፤ ፲፱።
፯፤ ምን፡ያህል፡መልካም፡ነበረ፡ *ሩጫችሁ። ማን፡
ቈረጣችሁ፡ ለውነት፡ እንዳትታዘዙ። *ም፡ ፫፤ ፩።
፩፤ ቆሮ፡ ፱፤ ፳፬።
፰፤ ይህ፡መግበላችሁ፡ወደርሱ፡ወደ፡ጸራችሁ፡ አይ
ደለምና። ም፡ ፩፤ ፮።
፱፤ ጥቂት፡ እርሾ፡ ሊጡን፡ ሁሉ፡ ያመጸል።
፲፤ እኔስ፡*አምኛችሁ፡ አለሁ፡ በእግዚአብሔር፡ሌ
ላ፡እንዳታስቡ። †የሚያውካችሁም፡**ፍዳውን፡ ደ
ቀበላል፡የሆነ፡ሁና። *፪፤ ቆሮ፡ ፪፤ ፫። ና፡ ፰፤ ፳፫።
†ም፡ ፩፤ ፯። **፪፤ ቆሮ፡ ፲፩፤ ፲፭።
፲፩፤ እኔም፡ወንድሞቼ፡ ሆይ፡ ግዝረትን፡ ካስተማ
ርሁ፡ለምን፡ያሳደኛል።እንግዲህ፡ የመስቀሉ፡ *መሰ
ናክል፡ ተሻረ። *፩፤ ቆሮ፡ ፩፤ ፳፫፤
፲፪፤ ምነው፡ ቢቈረጡ፡ የሚያጫንቋችሁ።
መዝ፡ ፲፪፤ ፬፤
፲፫፤ እላንት፡ ወንድሞቼ፡ ሆይ፡ ለሰው፡ ልጅነት፡ተ
ጸርታችኋልና። *የሰው፡ልጅነታችሁ፡ ግን፡የሥጋ፡ ምክ
ንያት፡አይሁንባችሁ፡ ነገር፡ግን፡ በፍቅር፡ እርሱ፡ በርሳ
ችሁ፡ ተገዙ። *፩፤ ቆሮ፡ ፰፤ ፱።
፲፬፤ ሕግ፡ሁሉ፡ ባንድ፡ ነገር፡ ይፈጸማልና። ባልንጀ
ራህን፡ *ውደድ፡እንደ፡ ራስህ። *ዘሌዋ፡ ፲፱፤ ፲፰።
ማር፡ ፲፪፤ ፴፩።
፲፭፤ አንዴ፡ ግን፡ ሌላውን፡ ከነከሰው፡ *ከበላው
ም፡ ተጠንቀቁ፡ እርሱ፡ በርሳችሁ፡ እንዳትጠፉ።
*፪፤ ቆሮ፡ ፲፪፤ ፳።
፲፮፤ እላለሁም። በመንፈስ፡ ተመላለሱ፡ የሥጋን
ም፡ መመኘት፡ አትፈጽሙም።
፲፯፤ ሥጋ፡መንፈስ፡ *የሚጸላውን፡ ይወዳልና። መ
ንፈስም፡ሥጋ፡የሚጸላውን። እሌህም፡እርሱ፡ በርሳ
ቸው፡ይጸላሉ፡እላንት፡የምትወድዋትን፡ ነገር፡እንዳ
ታርጓት። *ሮሜ፡ ፯፤ ፲፭፤ ፳፫።
፲፰፤ በመንፈስ፡ግን፡ብትሔዱ፡ ከኦሪት፡ በታች፡ አ
ደደላችሁም።
፲፱፤ የሥጋም፡ስራ፡ የተገለጠች፡ናት። እርስዋም፡
ምንዝር፡ ዝሙትም፡ ርኵሳትም፡ አለማፈርም።
፩፤ ቆሮ፡ ፮፤ ፱።
፳፤ ጣዖትንም፡ማምለክ፡ መሠሪነትም፡ ጠላትነ
ትም።ጸብም፡መቃናትም። መቈጣትም፡ መከራከ
ርም፡ ሁከትም፡ መለያየትም።
፳፩፤ ቅናትኝነትም፡መግደልም፡*ስካርም፡ መሶል
ሶልም፡ይህነንም፡ሁሉ፡ የሚመስል። አስቀድሜም፡
እንደልኋችሁ፡እንደሁም፡ አሁን፡እላለሁ። እንደዚ
ኽ፡ያለኸውን፡ የሚያደርጉ፡ የእግዚአብሔርን፡ †መ
ንግሥት፡ አይወርሱም። *ሉቃ፡ ፳፩፤ ፴፬።
†ኤፌ፡ ፭፤ ፭። ራእ፡ ፳፪፤ ፲፭።
፳፪፤ የመንፈስ፡ *ፍሬ፡ግን፡ ፍቅር፡ናት፡ ደስታም፡
ሰላምም፡ ትዕግሥትም፡ ቸርነትም፡ በጐነትም፡ ሃይ
ማኖትም፡ ገርነትም፡ መሻትንም፡ መግዛት።
*ኤፌ፡ ፭፤ ፱።
፳፫፤ በዚኽ፡ተደዘው፡ በሚኖሩ፡ሰዎች፡ ላይ፡ ሕግ፡
የለባቸውም። ፩፤ ጢሞ፡ ፩፤ ፱።
፳፬፤ የክርስቶስ፡ ወገኖችም፡ ሥጋቸውን፡ ፈጽመ
ው፡ሰቀሉ፡ከሕማማትና፡ ከመመኘት፡ጋራ።
ሮሜ፡ ፯፤ ፮። ቈላ፡ ፫፤ ፭።
፳፭፤ በመንፈስ፡ብንኖር፡በመንፈሰም፡እንሒድ።
ሮሜ፡ ፰፤ ፩።
፳፮፤ ከንቱ፡ክብር፡ አንወድም፡ አንዳችን፡ ሌላው
ን፡ ለመበደል፡እርሱ፡ በርሳችነም፡ ለመቃናት።
ፊል፡ ፪፤ ፫።

## ምዕራፍ፡ ፮፤

፩፤ ወንድሞቼ፡ሆይ፡አንድ፡ ሰው፡ ከላንት፡ በችኰ
ላ፡ቢያዝ፡ከኃጢአት፡እላንት፡ በመንፈስ፡ያላችሁ፡
እንደዚህ፡ ያለውን፡ አጸናኑት፡ በትሕትና፡ መንፈስ፡
ለራስህ፡ ተጠብቀህ፡ አንተ፡ ደግሞ፡ እንዳትፈተን።
ማቴ፡ ፲፰፤ ፲፭። ያዕ፡ ፭፤ ፲፱።
፪፤ ከላንት፡እያንዳንዱ፡ የባልንጀራውን፡ ሸክም፡
ያንሣ፡ እንደሁም፡ የክርስቶስን፡ ትእዛዝ፡ ፈጽሙ።
ሮሜ፡ ፲፬፤ ፩።
፫፤ አንዱም፡ቢመስለው፡ምንም፡እንደ፡ሆነ፡ምን
ም፡ሳይሆን፡እርሱ፡ራሱን፡አታለለ።
፬፤ ከላንት፡እያንዳንዱ፡ ስራውን፡ ይመርምር፡ እ
ንጂ፡ ትምክሕቱም፡ ለራሱ፡ ብቻ፡ ይሆናል፡ ለባልንጀ
ራውም፡ አይደለውም። ፪፤ ቆሮ፡ ፲፫፤ ፭።
፭፤ ሁሉ፡ እያንዳንዱ፡ ሸክሙን፡ ያነሣልና።
፪፤ ቆሮ፡ ፭፤ ፲።
፮፤ ነገር፡የሚማር፡ላስተማሪው፡መልካምን፡ነገር፡
ሁሉ፡ያካፍለው። ፩፤ ቆሮ፡ ፱፤ ፲፬።
፯፤ አትሳቱ፡እግዚአብሔር፡አይላገጥምና። ሰው፡
ሁሉም፡የዘራውን፡ያጭዳልና።
፰፤ ለሥጋው፡ የዘራ፡ ከሥጋው፡ ጥፋትን፡ያጭዳል፡
ለመንፈስም፡ የዘራ፡ ከመንፈስ፡ የዘላለም፡ ሕይወ
ት፡ ያጭዳል። ሮሜ፡ ፰፤ ፲፫።
፱፤ መልካምንም፡በማድረግ፡አንታክት፡የምናጭ
ድበት፡ ጊዜ፡ አለንና፡ ካልደከምነ። ፪፤ ተሰ፡ ፫፤ ፲፫።
፲፤ አሁንም፡ጊዜ፡ካገኘ፡ለሁሉ፡መልካም፡እናድር
ግ፡ይልቁንም፡ለሃይማኖት፡ሰዎች። ፪፤ ጴጥ፡ ፩፤ ፯።
፲፩፤ እዩ፡ምን፡ያህል፡ ወረቀት፡ በጄ፡ጻፍሁላችሁ።
፲፪፤ በሥጋ፡ይመኩ፡ ዘንድ፡ የሚወዱ፡ ሰዎች፡ እር
ሳቸው፡የግድ፡ትገዘሩ፡ዘንድ፡ ይልዋችኋል። ለሌላ፡ነገ

ር፡አይደለም፡ ስለ፡ ክርስቶስ፡ መስቀል፡ *እንዳይሰደ ዱ፡ነው፡እንጂ። *ም፡ ፭፤ ፲፩፤ ፊል፡ ፫፤ ፲፰፡፡

፲፫፤ እርሳቸውም፡የሚገዘሩ፡እንኳ፡ኦሪትን፡አይ ጠብቁም፡ነገር፡ግን፡ በሥጋችሁ፡ይመኩ፡ ዘንድ፡ ብለ ው፡ትገዘሩ፡ ዘንድ፡ ይሸዋቹኋል።

፲፬፤ እኔ፡ግን፡ አልመካም፡ በጌታችን፡ በየሱስ፡ ክር ስቶስ፡ መስቀል፡ በቀር። በርሱ፡ ዓለሙ፡ተሰቅሎልኛ ልና፡እኔም፡ ለዓለም። ፩፤ ቆር፡ ፩፤ ፴፩፡፡ ፪፤ ፪፡፡

፲፭፤ በክርስቶስ፡የሱስ፡ ዘንድ፡ግዝረት፡አንዳች፡ አትጠቅምምና፡ ቍላፈነትም፡ነገር፡ ግን፡አዲስ፡ ፍጥ ረት። ም፡ ፭፤ ፮፡፡ ፩፤ ቆር፡ ፯፤ ፲፱፡፡

፲፮፤ በዚች፡ ሕግ፡ በሚሔዱ፡ ላይ፡ ሰላም፡ ይሁን፡ ምሕረትም፡ በእግዚአብሔር፡ *እሥራኤል፡ ላይም። *መዝ፡ ፻፳፭፤ ፭፡፡

፲፯፤ ከዚህም፡በኋላ፡ማንም፡አያድክመኝ፡ የጌታ ን፡ የየሱስን፡ ምልክት፡ በሥጋዬ፡ ተሸክሚያለሁና።

፲፰፤ የጌታችን፡ የየሱስ፡ ክርስቶስ፡ ጸጋ፡ ከመንፈሳ ችሁ፡ጋራ፡ይሁን፡ ወንድሞቼ፡ ሆይ። አሚን።

ወደ፡ገላትያ፡ሰዎች፡ተጻፈች፡ከሮምያ፡አገር።

# የሐዋርያው፡ የጳውሎስ፡ መልእክት፡ ወደ፡ ኤፌሶን፡ ሰዎች።

ምዕራፍ፡ ፩፤

፩፤ ከጳውሎስ፡ከየሱስ፡ክርስቶስ፡ ሐዋርያ፡ በእግ ዚአብሔር፡ፈቃድ፡ በኤፌሶን፡ ወደሚኖሩ፡ ቅዱሳን፡ በክርስቶስ፡ የሱስም፡ ያመኑ። ሮሜ፡ ፩፤ ፯፡፡ ፩፤ ቆር፡ ፩፤ ፪፡፡

፪፤ ጸጋ፡ ይድረሳችሁ፡ ሰላምም፡ ከእግዚአብሔር፡ ካባታችን፡ ከጌታም፡ ከየሱስ፡ ክርስቶስ።

፫፤ አምላክ፡ይመስገን፡የየሱስ፡ክርስቶስ፡ የጌታች ን፡አባት፡በመንፈሳዊ፡በረከት፡ሁሉ፡ የባረከነ፡ በሰማ ይ፡ በክርስቶስ። ም፡ ፪፤ ፮፡፡

፬፤ በርሱ፡እንደ፡ *መረጠነ፡ዓለም፡ሳይፈጠር፡ ተቀ ደሳን፡እንሆን፡ዘንድ፡በፊቱ፡ያለ፡ነውርም፡በፍቅር። *ዮሐ፡ ፲፭፤ ፲፮፡፡ ሮሜ፡ ፰፤ ፳፱፡፡ *ም፡ ፭፤ ፳፯፡፡

፭፤ አስቀድሞ፡ ለይቶናልና፡ ልጆች፡ ሊያደርገነ፡ በየ ሱስ፡ክርስቶስ፡ፈቃዱ፡እንደ፡ወደደች። ዮሐ፡ ፩፤ ፲፪፡፡

፮፤ ፈቃዱ፡ እንደ፡ወደደች። ለጸጋው፡ክብር፡ ትምክሕት። እርሱዋን፡የሰጠነ፡*በወዳጁ። *ማቴ፡ ፫፤ ፲፯፡፡

፯፤ በርሱ፡*መድኃኒት፡ የተቀበልነ፡ በደሙ፡ የኃጢ አት፡ ስርየት፡ ከጸጋው፡ ተባለጠግነት፡ የተነሣ። *ቈል፡ ፩፤ ፲፬፡፡ ተም፡ ፪፤ ፯፡፡ ፍ፡ ፫፤ ፰፤ ፲፮፡፡

፰፤ በኛ፡ ያስተረፈረፈው፡ በጥበብ፡ሁሉ፡ በውቀት ም፡ሁሉ።

፱፤ የፈቃዱንም፡ ምሥጢር፡ አስታወቀነ፡ እርሱ፡ እንደ፡ወደደ፡ አስቀድሞም፡ በራሱ፡እንደ፡ ሠራ። ም፡ ፫፤ ፱፡፡ ሮሜ፡ ፲፮፤ ፳፭፡፡

፲፤ ለዘመኑ፡ፍጻሜ፡ ሥርዓት፡ ሁሉ፡ በክርስቶስ፡ይ ፈጸም፡ዘንድ፡ በሰማይና፡ በምድር፡ ያለው።

፲፩፤ በርሱም፡እኛ፡ ደግሞ፡ ርስትን፡ ተቀበልነ፡ አስ ቀድመን፡*የተመደብነ። እንደ፡ አሳቡ፡ነገሩን፡ ሁሉ፡ የሚሰራ፡ እንደ፡ ፈቃዱ፡ ምክር። *ገላት፡ ፬፤ ፬፡፡

፲፪፤ ለምስጋናው፡*ትምክሕት፡እንሆን፡ ዘንድ፡ እ ኛ፡ አስቀድመን፡ ክርስቶስን፡ ተስፋ፡ ያደረግነ። *ገላት፡ ፫፤ ፳፫፤ ፳፭፡፡

፲፫፤ እላንትም፡ ደግሞ፡ በርሱ፡ አመናችሁበት፡ የ ውነት፡ነገር፡በሰማችሁ፡ጊዜ፡የደህንነታችሁ፡ወንጌል፡ የምትሆን። በርሱ፡ደግሞ፡ካመናችሁ፡በኋላ፡ ታተማ ችሁ፡ ተስፋ፡ በተሰጠው፡ መንፈስ፡ ቅድስ። ም፡ ፬፤ ፴፡፡ ፪፤ ቆር፡ ፩፤ ፳፪፡፡

፲፬፤ የርስታችን፡ *መያዣ፡ የሚሆን፡ እስከ፡ መድ ኃኒትን፡ የዋጀትን፡ ገንዘብ፡ ጊዜ፡ ለምስጋናው፡ ትም ክሕት። *፪፤ ቆር፡ ፩፤ ፳፪፡፡

፲፭፤ ስለዚህም፡እኔ፡በጌታችን፡ በየሱስ፡ ክርስቶስ፡ ማመናችሁን፡ከሰማሁ፡ጀምሬ፡ለቅዱሳንም፡ ሁሉ፡ ፍቅራችሁን። ቈለ፡ ፩፤ ፬፡፡

፲፮፤ ስላላንት፡ከማመስገን፡አልተውሁም፡በጸሎ ቴም፡እላንትን፡ ከማሰብ።

፲፯፤ እግዚአብሔር፡የጌታችን፡ የየሱስ፡ ክርስቶስ፡ አባት፡ የምስጋና፡ ጌታ፡ የጥበብ፡ መንፈስ፡ የመገለጥ ም፡ይሰጣችሁ፡ ዘንድ፡ እርሱን፡ በማወቅ። ሮሜ፡ ፮፤ ፬፡፡

፲፰፤ የልባችሁ፡ ዓይን፡ *ትበራ፡ ዘንድ፡ እንድታው ቁ፡የመጥራቱ፡ ተስፋ፡ እንዴት፡እንደሆነ፡ የርስቱ፡ ክ ብር፡ባለጠግነትስ፡ምንድር፡ ነው፡ በቅዱሳን። *፪፤ ቆር፡ ፬፤ ፬፡፡

፲፱፤ ምን፡ያህልም፡የኃይሉስ፡ታላቅነት፡ነው፡ በኛ፡ ባመነው፡ ላይ፡ እንደ፡ ኃይሉ፡ ጽናት፡ ስራ።

፳፤ በክርስቶስ፡ ያደረጋት፡ ከሙታን፡ ባስነሣው፡ጊ ዜ፡ በሰማያትም፡ በቀኙ፡ ባስቀመጠው፡ጊዜ። መዝ፡ ፻፲፤ ፩፡፡

፳፩፤ ባለቀች፡ ሁሉ፡ ላይ፡ በነገሥትም፡ በኃይላት ም፡ በአጋእዝትም፡ ከሚጸራውም፡ ስም፡ ሁሉ፡ በላ ይ፡በዚህ፡ዓለም፡ብቻ፡አይደለም፡ በሚመጣውም፡ እንጂ። ቈለ፡ ፪፤ ፲፡፡

፳፪፤ ሁሉንም፡አስገዛ፡ ከግሩ፡ በታች። *ራስም፡ አ ደረገው፡ ከሁሉ፡ በላይ፡ ለቤተ፡ ክርስቲያን። *ም፡ ፬፤ ፲፭፡፡ መዝ፡ ፰፤ ፮፡ ፰፡፡ ማቴ፡ ፳፰፤ ፲፰፡፡

፳፫፤ *ሥጋው፡ የምትሆን፡ እርስዋም፡ መጨረሻ ው፡ †ሁሉን፡ በሁሉ፡ ለሚጨርስ። *ሮሜ፡ ፲፪፡ ፭። ፩፡ቆር፡ ፲፪፡ ፳፯። †ም፡ ፬፡ ፲።

ምዕራፍ፡ ፪፤

፩፤ እላንተንም፡ፈጽሞ፡አደናችሁ፡ሙታን፡ስትሆ ኑ፡በመተላለፋችሁና፡በኃጢአታችሁ። ቆላ፡ ፪፡ ፲፫።

፪፤ አስቀድማችሁ፡*የሔዳችሁባት፡ እንደዚህ፡ዓ ለም፡ስራ። እንደ፡ተአለቃ፡ ቅሎት፡ በአየር፡ የሚገዛ፡ እንደ፡ መንፈስም፡ ዛሬ፡ የሚሰራ፡ በዓመፀ፡ ልጆች። *ቲቶ፡ ፫፡ ፫። †ኤፌ፡ ፮፡ ፲፪። ዮሐ፡ ፲፪፡ ፴፩።

፫፤ እኛ፡ሁላችን፡ከርሳቸው፡ጋራ፡ የሔድነ፡አስቀድ መን፡በሥጋችን፡ፈቃድ፡የሥጋንም፡ፈቃድ፡ እናደርግ፡ ነበርነ፡የልባችነንም፡አሳብ።በፍጥረታችንም፡የቍጣ፡ ልጆች፡ነበርነ፡እንደ፡ሌሎች።

፬፤ እግዚአብሔር፡ ግን፡ በምህረቱ፡ ባለጠጋ፡ የሚ ሆን፡ ስለ፡ ወደደነ፡ ስለ፡ ፍቅሩ፡ ብዛት።

፭፤ በኃጢአትም፡ *የሞትነ፡ ስንሆን፡ ከክርስቶስ፡ ጋራ፡አደነነ።በጸጋው፡ደናችሁ። *ሉቃ፡ ፲፭፡ ፳፬፡ ፴፪።

፮፤ ከርሱም፡ጋራ፡አስነሣነ፡ከርሱም፡ጋራ፡በሰማያ ት፡ አስቀመጠነ፡ በክርስቶስ፡ የሱስ። ሮሜ፡ ፰፡ ፲። ፊል፡ ፫፡ ፳።

፯፤ በሚመጣው፡ዓለም፡እጅግ፡ የበዛችውን፡ የጸ ጋውን፡ባለጠግነት፡ ሊገልጥ፡ በቸርነቱ፡ ለኛ፡ በምትሆ ን፡ በክርስቶስ፡ የሱስ። ም፡ ፩፡ ፯።

፰፤ በጸጋው፡ ድናችኋልና፡ በሃይማኖት። ይህም፡ ከላንት፡አይደለም፡የእግዚአብሔር፡ ስጥወታ፡ነው። ገላት፡ ፪፡ ፲፮።

፱፤ ከምግባር፡ አይደለም፡ ማንም፡ እንዳይመካ። ፩፡ ቆር፡ ፩፡ ፳፱።

፲፤ እኛ፡ፍጥረቱ፡ነንና፡በክርስቶስ፡የሱስም፡ተፈጠ ርነ፡ መልካም፡ ስራ፡ ለማድረግ፡ አስቀድሞ፡ እግዚአ ብሔር፡ያዘጋጀ፡ እንሔድባት፡ ዘንድ። ቲቶ፡ ፪፡ ፲፬።

፲፩፤ ስለዚህም፡አስቡ፡እላንት፡*የአሕዛብ፡ወገን፡ በድር፡ የነበራችሁ፡ በሥጋ፡ ቍላፍነት፡ እንደ፡ ተባላች ሁ፡ግዝረት፡በሚጸሩት፡ ዘንድ፡ እርሱም፡ እጅ፡ የሚ ያደርገው፡ በሥጋ። *ም፡ ፭፡ ፰።

፲፪፤ በዚያም፡ ዘመን፡ያለ፡ክርስቶስ፡ ነበራችሁ። ከ እሥራኤልም፡ሥርዓት፡ ልዩ፡ ነበራችሁ፡ *ከተስፋው ም፡ኪዳን። ተስፋም፡ አልነበራችሁም፡ በዓለምም ያለ፡አምላክ፡ ነበራችሁ። *ሮሜ፡ ፱፡ ፬።

፲፫፤ ዛሬ፡ግን፡በክርስቶስ፡ የሱስ፡ እላንት፡ ቀድሞ፡ ርቃችሁ፡የነበራችሁ፡ በክርስቶስ፡ ደም፡ቀረባችሁ።

፲፬፤ እርሱ፡ በመካከላችን፡ *አስማምትዋልና፡ ሁ ለቱንም፡†አንድ፡አደረገ፡ በመካከልም፡ የነበረውን፡ ግድግዳ፡አፈረሰው። *ኢሳ፡ ፱፡ ፮። †ገላት፡ ፫፡ ፳፰።

፲፭፤ በሥጋውም፡ጽልን፡ ፈታው፡ *የኦሪትንም፡ ት እዛዝ፡በሚደዊ፡ ሥርዓት፡የተያዘውን፡አስቀረው። በራሱ፡ሁለቱን፡ይፈጥር፡ ዘንድ፡†አዲስ፡ ሰው። *ቆላ፡ ፪፡ ፲፬። †፪፡ ቆር፡ ፭፡ ፲፯።

፲፮፤ ሁለቱንም፡ ለእግዚአብሔር፡ አስታረቀ፡ ባን ድ፡ ሥጋ፡ በመስቀሉ፡ ጽልንም፡ ገደለ፡ በአካሉ።

፲፯፤ በመጣም፡ጊዜ፡የምስራች፡ነገራችሁ፡ለላንት፡ ርቃችሁ፡ ለነበራችሁ፡ ቀርበውም፡ ለነበሩ። ኢሳ፡ ፶፯፡ ፲፱። ዘካ፡ ፱፡ ፲።

፲፰፤ በርሱ፡ምክንያት፡መቅረብ፡ ሁናልናልና፡ ለኛ፡ ለሁለቱ፡ባንድ፡ መንፈስ፡ ወደ፡አብ። ም፡ ፫፡ ፲፪።

፲፱፤ እንግዲህም፡ እንግዶችና፡ መጻተኞች፡ አይደ ላችሁም፡እላንት፡ የቅዱሳን፡ባላገሮችና፡ የእግዚአብ ሔር፡ ቤተ፡ ሰዎች፡ ናችሁ፡ እንጂ። ም፡ ፫፡ ፮። ዕብ፡ ፲፪፡ ፳፪፡ ፳፫።

፳፤ በሐዋርያትና፡በነቢያትም፡*መሠረት፡ ላይ፡ተ ሠራችሁ፡ †የማዝኑ፡ራስ፡ ደንጊያ፡እርሱ፡ የሱስ፡ ክር ስቶስ፡ ያለ። *ማቴ፡ ፲፮፡ ፲፰። †ኢሳ፡ ፳፰፡ ፲፮።

፳፩፤ በርሱ፡ላይ፡ስራው፡ ሁሉ፡ ተስማምቶበት፡ ለ ቅዱስ፡ ቤተ፡ መቅደስ፡ በጌታ፡ የሚያድግ።

፳፪፤ በርሱም፡እላንት፡ ደግሞ፡አንድ፡ ሁናችሁ፡ የ ምትስሩበት፡ለእግዚአብሔር፡ማደርያ፡ በመንፈስ። ፩፡ ጴጥ፡ ፪፡ ፭።

ምዕራፍ፡ ፫፤

፩፤ ስለዚህም፡ እኔ፡ ጳውሎስ፡ በክርስቶስ፡ የሱስ፡ ለላንት፡ ላሕዛብ፡ የታሠርሁ። ፊል፡ ፩፡ ፯፡ ፲፫።

፪፤ ስለላንት፡የተሰጠችኝን፡ የእግዚአብሔርን፡ ጸ ጋ፡ መጋቢነት፡ ሰምታችሁ፡ እንደ፡ ሆናችሁ።

፫፤ በራእይ፡ ምሥጢሩን፡ አስታውቀልኛልና፡ እን ደ፡ጻፍሁላችሁ፡በጥቂት፡ነገር። ም፡ ፩፡ ፱፡ ፲።

፬፤ ባነበባችሁት፡ ጊዜ፡ ማስተዋሌን፡ በክርስቶስ፡ ምሥጢር፡ ታውቁ፡ ዘንድ፡ እንዲቻላችሁ።

፭፤ ባለፈ፡ ዘመን፡ ለሰው፡ ልጆች፡ ያልተገለጠ። ዛ ሬ፡ ለቅዱሳን፡ ሐዋርያቱ፡ ለነቢያቱም፡ እንደ፡ ተገለ ጠች፡ በመንፈስ። ም፡ ፩፡ ፱።

፮፤ አሕዛብ፡ አንድ፡ ይሆኑ፡ ዘንድ፡ በርስቱ፡ አንድ ም፡ይሆኑ፡ዘንድ፡በሥጋው፡በክርስቶስ፡ተስፋም፡አን ድ፡ ይሆኑ፡ ዘንድ፡ በወንጌሉ። ም፡ ፪፡ ፲፫፡ ፲፰፡ ፲፱።

፯፤ እኔ፡አገልጋይ፡የሆንሁለት፡እንደ፡እግዚአብሔ ር፡ ጸጋ፡ ስጥወታ። እንደ፡ ቸሎቱ፡ ስራ፡ እንደ፡ ተሰጠ ችኝ።

፰፤ ለኔም፡ ከቅዱሳን፡ ሁሉ፡ *ለተጠቃሁ፡ ይህች፡ †ጸጋ፡ ተሰጠችኝ፡ ለአሕዛብ፡ የምስራች፡ እነግር፡ ዘን ድ፡የማትመረመረውን፡ የክርስቶስን፡ የጸጋ፡**ባለጠ ግነት። *፩፡ ቆር፡ ፲፭፡ ፱፡ ፲። †ገላት፡ ፩፡ ፲፮። **ም፡ ፩፡ ፯።

፱፤ ለሰውም፡ ሁሉ፡ የምሥጢሩን፡ ሥርዓት፡ አበ ራ፡ ዘንድ፡ተሸሽጎ፡ የነበረውን፡ *ከጥንት፡ ጀምሮ፡ በእ ግዚአብሔር፡ ዘንድ፡ †ሁሉን፡ በፈጠረ፡ በየሱስ፡ ክር ስቶስ። *ሮሜ፡ ፲፮፡ ፳፭። †ቆላ፡ ፩፡ ፲፮።

፲፡ ዛሬ፡ ላለቀችና፡ *ለሥልጣናትም፡ በሰማያት፡ የእግዚአብሔር፡ልዩ፡ ልዩ፡ †ጥበብ፡ በቤተ፡ ክርስቲያ ን፡ ትታወቅ፡ ዘንድ። *፩፡ ጴጥ፡ ፩፡ ፲፪።
†ሮሜ፡ ፲፩፡ ፴፫።

፲፩፡ እንደ፡ቀደመው፡ እንደ፡ ዘላለም፡*ፈቃዱ፡ በ ክርስቶስ፡ የሱስ፡ በጌታችን፡ እንደ፡ አደረጋት።
ም፡ ፩፡ ፲፩።

፲፪፡ በርሱ፡ *ድፍረትን፡ ያገኘነ፡ ያለ፡ መጠራጠር ም፡ ወደርሱ፡ †መግባትን፡ በሃይማኖቱ።
*ዮሐ፡ ፲፬፡ ፮። †ዕብ፡ ፬፡ ፲፮።

፲፫፡ ስለዚህም፡ በላንቴ፡ ምክንያት፡ በምትደርስ ብኝ፡*በመከራዬ፡እንደትደክሙ፡ አለምናለሁ፡ ክብ ራችሁ፡ናትና። *ቆላ፡ ፩፡ ፳፬።

፲፬፡ ስለዚህም፡ በጕልበቴ፡እምበረክካለሁ፡ወደ፡ ጌታችን፡ ወደ፡ የሱስ፡ ክርስቶስ፡*አብ። *ም፡ ፩፡ ፫።

፲፭፡ በርሱ፡ስም፡በሰማይና፡በምድር፡ያሉቾ፡አባት ነት፡ሁሉ፡ የሚጸራ።

፲፮፡ እንደ፡ ክብሩ፡ ባለጠግነት፡ ይሰጣችሁ፡ ዘንድ፡ በመንፈሱ፡ ኃይል፡ *ትጸኑ፡ ዘንድ፡ በውሥጡ፡ ሰውነ ታችሁ። *ም፡ ፩፡ ፯። ፪፡ ፯። †ም፡ ፯፡ ፲።

፲፯፡ ክርስቶስ፡ በሃይማኖት፡ *በልባችሁ፡ ያድርባች ሁ፡ ዘንድ፡ ሥርንም፡ መሠረትንም፡ በፍቅር፡ ቲዙ፡ ዘ ንድ። *ዮሐ፡ ፲፬፡ ፳፫።

፲፰፡ ትችሉ፡ዘንድ፡ ለማስተዋል፡ ከቅዱሳን፡ሁሉ፡ ጋራ።ምንድር፡እንደሆነ፡ርዝመቱ፡ *ስፋቱም፡መጥለ ቁም፡ ቁመቱም። *ኢዮብ፡ ፲፩፡ ፰፡ ፱።

፲፱፡ የክርስቶስንም፡ *ፍቅር፡ ከመታወቅ፡ የምት በልጠውን፡ታውቁ፡ዘንድ፡ ትፈጸሙ፡ ዘንድ፡ በእግዚ አብሔር፡ ምሉ፡ ፍጸሜ።

፳፡ ለርሱም፡በላያችን፡በጸናች፡ በኃይሉ፡ ከምንለ ምነው፡ ተስፋም፡ ከምናደርገው፡ ሁሉ፡ አብልጦ፡ ሊ ያደርግልን፡ ለሚችል። ሮሜ፡ ፲፮፡ ፳፭።

፳፩፡ ለርሱ፡ *ምስጋና፡ ይሁን፡ በቤተ፡ ክርስቲያኑ፡ ክርስቶስ፡በየሱስ፡ እስከ፡ልጅ፡ልጅ፡ ሁሉ፡ለዘላለሙ ም። አሜን። *ሮሜ፡ ፲፩፡ ፴፮። ፩፡ ጢሞ፡ ፩፡ ፲፯።

ምዕራፍ፡ ፬፡

፩፡ አሁንም፡ እኔ፡ የጌታ፡ እሥር፡ ለተጸራችሁባት፡ መጸራታችሁ፡ እንዲገባችሁ፡ ትሔዱ፡ ዘንድ፡ እለምነ ናችኋለሁ።

፪፡ *በትሕትናና፡ በገርነት፡ ሁሉ፡ በትዕግሥትም፡ እርሱ፡ በርሳችሁ፡ ስትቻቻሉ፡ በፍቅር።
*የሐዋ፡ ፳፡ ፲፱። ቆላ፡ ፫፡ ፲፪።

፫፡ የመንፈስንም፡ *አንድነት፡ በሰላም፡ ማሠርያ፡ ትጠብቁ፡ ዘንድ፡ ስትጋደሉ። *፩፡ ቆሮ፡ ፲፪፡ ፲፫።

፬፡ *አንድ፡ ሥጋ፡ ነው፡አንድ፡ መንፈስም። ለመጸ ራታችሁ፡ የተጸራችሁለት፡ ትስፋ፡ አንዲት፡ እንደ ለች። *ሮሜ፡ ፲፪፡ ፭።

፭፡ አንድ፡*ጌታም፡ አንዲት፡ ሃይማኖትም፡አንዲ ት፡ጥምቀትም። *ዘዳግ፡ ፮፡ ፬። ፩፡ ቆሮ፡ ፰፡ ፬፡ ፮።

፮፡ *አንድ፡ እግዚአብሔርም፡ የሁሉም፡ አባት። እርሱም፡ከሁሉ፡በላይ። በሁሉም።በላንተም፡ሁሉ።
*መልክ፡ ፪፡ ፲። ፩፡ ቆሮ፡ ፲፪፡ ፮።

፯፡ ከኛ፡ ግን፡ *ለያንዳንዱ፡ በክርስቶስ፡ ስጦታ፡ መጠን፡ ጸጋ፡ ተሰጠችነ። *ሮሜ፡ ፲፪፡ ፫።
፩፡ ቆሮ፡ ፲፪፡ ፲፩።

፰፡ ስለዚህ፡ ይላል። *ወደ፡ ሰማይ፡ ወጣ፡ †ምርኮ ንም፡ ማረከ፡ ለሰዎችም፡ **ስጦታ፡ ሰጠ።
*መዝ፡ ፷፰፡ ፲፰። †መሳ፡ ፭፡ ፲፪። ቆላ፡ ፪፡ ፲፭።
**የሐዋ፡ ፪፡ ፴፫።

፱፡ *መውጣቱስ፡ምንድር፡ ነው፡ በፊት፡ ወደ፡ ጥል ቅ፡ምድር፡ስለ፡ወረደ፡ ነው፡ እንጂ። *ዮሐ፡ ፫፡ ፲፫።

፲፡ የወረደው፡እርሱ፡ነው፡ከሰማያት፡ሁሉ፡በላይ፡ *የወጣው፡ሁሉን፡ ይመላ፡ ዘንድ። *የሐዋ፡ ፪፡ ፳፫።

፲፩፡ እርሱም፡ ሰጠ፡ እኩሌቶች፡ ሐዋርያት፡ እኩ ሌቶችም፡ ነቢያት፡ ሌሎችም፡ ሰባኮች፡ ሌሎችም፡ ጠ ባቂችና፡ አስተማሮች። የሐዋ፡ ፳፩፡ ፰።
፩፡ ቆሮ፡ ፲፪፡ ፳፰።

፲፪፡ ቅዱሳን፡ እንዲፈጸሙ፡ለማገልገል፡ስራ፡ የክ ርስቶስን፡ ሥጋ፡ ለመሥራት። ፩፡ ጴጥ፡ ፪፡ ፭።

፲፫፡ ሁላችን፡እስክንደርስ፡ድረስ፡ወደ፡ሃይማኖት፡ አንድነት፡ወደ፡እግዚአብሔር፡ልጅም፡ዕውቀት፡እስ ከ፡ ፍጹም፡ ሰው፡ ድረስ፡ እስከ፡ ክርስቶስ፡ አካል፡ እ ስከ፡*ፍጸሜው፡ ልክ፡ ድረስ። *ም፡ ፫፡ ፲፰፡ ፲፱።

፲፬፡ ሕፃናት፡ እንደንሆን፡ ሞገድ፡ ወዲህና፡ ወዲ ያ፡የሚገፉን። ከትምህርት፡ንፋስም፡ሁሉ፡ ጋራ፡የም ንሔድ፡ በሰዎች፡ ትንኰል፡ በምክራቸው፡ የሚያታ ሉ፡ ሊያጠፉ።

፲፭፡ በፍቅር፡ግን፡ እውነተኞች፡ እንሆን፡ ዘንድ፡ ወ ደርሱ፡ራስ፡ ወደሚሆን፡ እንድናድግ፡ እርሱም፡ *ክር ስቶስ። *ም፡ ፩፡ ፳፪። ፭፡ ፳፫። ቆላ፡ ፩፡ ፲፰።

፲፮፡ ሥጋ፡ሁሉ፡የሚዋደድበት፡በጅማትም፡ሁሉ፡ የሚሰማማበት፡ የሚታሠርም፡ ኢያንዳንዱ፡ በየክ ፍሉ፡ የሰጠውን፡ ያህል። ሥጋ፡ እንዲያድግበት፡ በፍ ቅር፡ ይሰራ፡ ዘንድ። ቆላ፡ ፪፡ ፲፱።

፲፯፡ ይህነንም፡እላለሁ፡ በእግዚአብሔርም፡እመ ሰክራለሁ፡እንደትሔዱ፡የቀሩት፡አሕዛብ፡እንዲሔ ዱ፡*በከንቱ፡ ማሰባቸው። *ሮሜ፡ ፩፡ ፳፩።

፲፰፡ በምክራቸውም፡ ጨለማ። እርሳቸውም፡ ከ እግዚአብሔር፡ ሕይወት፡ *የተለዩ። እውቀት፡ ስለ ሌላባቸው፡ስለ፡ልባቸውም፡ዕውርነት። *ም፡ ፪፡ ፲፪።

፲፱፡ እሊያ፡ልባቸውም፡ደነዘ፡ ራሳቸውን፡ ለሴስኝ ነት፡አሳልፈው፡የሰጡ። ርኵሰትን፡ሁሉ፡በሥሥት፡ሊ ማድረግ።

፳፡ እላንተ፡ ግን፡ ክርስቶስን፡ እንደህ፡ አልተማራ ችሁትም።

፳፩፡ በርሱ፡*ስምታችሁበት፡እንደ፡ሆናችሁ፡እው

ነቱንም፡ በየሱስ፡ እንደለች፡ አውቃችሁ፡ እንደ፡ ሆና
ችሁ። *ምዕ፡ ፩፤ ፲፫።
፳፪፤ እንደ፡ቀደም፡አካሔድ፡ያለውን፡*አሮጌው
ንም፡ሰው፡ በስሕተት፡ፈቃድ፡ የየጠፋውን፡ታወጡ፡
ዘንድ። *ሮሜ፡ ፮፡ ፮። ፍ፡ ፰፤ ፲፫። ቆላ፡ ፫፤ ፱።
†ገላት፡ ፮፤ ፰።
፳፫፤ በሕሊናችሁም፡ መንፈስ፡ ታደሱ፡ ዘንድ።
ሮሜ፡ ፲፪፤ ፪።
፳፬፤ አዲስንም፡ ሰው፡ትለብሱ፡ ዘንድ። *በእግዚ
አብሔር፡ምሳሌ፡በውነተኛ፡ ጽድቅና፡ በቅድስና፡ የተ
ፈጠረውን። *ዘፍ፡ ፩፤ ፳፮፤ ፳፯።
፳፭፤ ስለዚህም፡አስትን፡ሁሉ፡ ከላንት፡ አውልቃ
ችሁ፡በውነት፡ተናገሩ፡ ሁሉ፡ኢያንዳንዱ፡ ከባልንጀራ
ው፡ ጋራ። እኛ፡ እርሱ፡ በርሳችን፡ ብልቶች፡ ሁነናልና።
፳፮፤ *ተቈጡ፡ ኃጢአትም፡ አትስሩ። በቍጣች
ሁ፡ ጸሐይ፡ አይግባባችሁ። *መዝ፡ ፬፤ ፭።
ያዕ፡ ፩፤ ፲፱፤ ፳።
፳፯፤ ለስይጣንም፡ ስፍራውን፡ አትስጡ።
፳፰፤ የሰረቀም፡ እንግዲህ፡ አይሰረቅ፡ በጁ፡ ደደ
ከም፡እንጂ፡መልካምንም፡ ያድርግ፡ ለሚሻ፡ ለመስ
ጠት፡ ያገኝ፡ ዘንድ። ፩፤ ተሰ፡ ፬፤ ፲፩።
፳፱፤ *የማይጠቅም፡ ነገር፡ ሁሉ፡ ካፋችሁ፡ አይው
ጣ።መሻትን፡ተለረብ፡የሚያነጽና፡ መልካም፡ ያለ፡እ
ንጂ፡ለሚሰሙት፡ጸጋ፡ታመጣ፡ዘንድ። *ምዕ፡ ፭፤ ፬።
†ቆላ፡ ፫፤ ፲፮፤ ፲፯። ፍ፡ ፬፤ ፮።
፴፤ የእግዚአብሔርንም፡ቅዱስ፡መንፈሱን፡ለመ
ድኃኒት፡ ቀን፡ *የታተማችሁበትን፡ †አታሳዝኑ።
*ምዕ፡ ፩፤ ፲፫። †ኢሳ፡ ፷፫፤ ፲።
፴፩፤ የመረረ፡ ነገር፡ሁሉ፡ መዓትም፡ ቍጣም፡ ጩ
ኸትም፡ ስድብም፡ከላንት፡ ይራቅ፡ ከክፋት፡ ሁሉ፡ጋ
ራ። ቆላ፡ ፫፤ ፰።
፴፪፤ እርሱ፡ በርሳችሁም፡ ቸርች፡ የምትራሩም፡
ሁኑ።እርሱ፡በርሳችሁም፡ ይቅር፡ በሉ። እግዚአብሔ
ር፡ ደግሞ፡ እላንትን፡ በክርስቶስ፡ ይቅር፡ እንደለላ
ችሁ። ማቴ፡ ፮፤ ፲፬። ፍ፡ ፲፰፤ ፳፯—፴፭።
ቆላ፡ ፫፤ ፲፫።

ምዕራፍ፡ ፭፤

፩፤ እንግዲህ፡እግዚአብሔርን፡ ምሰሉ፡ እንደ፡ ተ
ወደዱ፡ ልጆች። ማቴ፡ ፭፤ ፵፰።
፪፤ *በፍቅርም፡ተመላለሱ፡ ክርስቶስ፡ ደግሞ፡እን
ደ፡ወደደነ፡ ራሱንም፡ ስለኛ፡ አሳልፎ፡ እንደ፡ሰጠ፡ቍ
ርባን፡መሥዋዕትም፡አድርጎ፡ ለእግዚአብሔር፡ መዐ
ዛው፡ያማረ፡ሽቱ። *ማር፡ ፲፪፤ ፴፩። ዕብ፡ ፲፤ ፲።
፫፤ ዝሙትና፡ርኵሰት፡ሁሉ፡ግን፡ሥሥትም፡ ከቶ፡
አይሰማባችሁ፡ለቅዱሳን፡እንደሚገባ። ቆላ፡ ፫፤ ፭።
፬፤ እንደሁም፡ ነውረኛ፡ ነገር፡ የስንፍና፡ ነገርም፡ የ
ማይገባ፡ ዋዛም፡ ምስጋና፡ እንጂ። ምዕ፡ ፬፤ ፳፱።
፭፤ ይህነን፡አውቃችኋልና፡አመንዝራ፡ቢሆን፡ርኩ
ስም፡ቢሆን፡ገለጠግነትንም፡የሚወድ፡ ቢሆን፡እርሱ
ም፡ጣዖት፡ የሚያመልክ። ለሌህ፡ ሁሉ፡ርስት፡ የላቸ
ውም፡ በእግዚአብሔርና፡ በክርስቶስ፡ መንግሥት።
፩፤ ቆሮ፡ ፮፤ ፱፤ ፲።
፮፤ ማንም፡ አያታልቻችሁ፡ በምናምን፡ ነገር፡ በዚህ፡
ነገር፡ምክንያት፡የእግዚአብሔር፡ ቍጣ፡ ይመጣልና፡
በማይታዘዙ፡ ልጆች፡ ላይ።
፯፤ ባልንጅሮቻቸውም፡ አትሁኑዋቸው።
፰፤ ቀድሞ፡ጨለማ፡ነበራችሁና፡ ዛሬ፡ግን፡ብርሃን፡
ናችሁ፡በጌታው። ምዕ፡ ፪፤ ፲፩። ፩፤ ጴጥ፡ ፪፤ ፱።
፱፤ እንደ፡*ብርሃን፡ልጆች፡ተመላለሱ። የመንፈስ፡
ፍሬ፡ በበጎነት፡ሁሉ፡ በጽድቅም፡ በውነትም፡ነውና።
*ሉቃ፡ ፲፮፤ ፰። ዮሐ፡ ፲፪፤ ፴፮።
፲፤ መርምራችሁ፡እግዚአብሔር፡ደስ፡ የሚያሰኝ፡
ስራ፡ምን፡ እንደ፡ ሆነ። ቈ፡ ፲፯። ሮሜ፡ ፲፪፤ ፪።
፲፩፤ ፍሬ፡ ከሌለው፡ ግን፡ ከጨለማ፡ስራ፡ ጋራ፡ አን
ድ፡ አትሁኑ፡ ገሥጽዋቸው፡ እንጂ።
፲፪፤ ከርሳቸው፡በሰውር፡የሚሆነው፡ በርሱ፡መናገ
ር፡ ደግሞ፡ ነውር፡ ነውና። ሮሜ፡ ፩፤ ፳፬።
፲፫፤ የምትገሠጽ፡ስራ፡ግን፡ከብርሃን፡ትገለጣለች፡
የተገለጠ፡ሁሉ፡ነገር፡ብርሃን፡ነውና። ዮሐ፡ ፫፤ ፳፩።
፲፬፤ ስለዚህም፡ይላል።ንቃ፡የተኛህ፡ከሙታንም፡
ተነሣ፡ ክርስቶስም፡ ያበራልሃል። ኢሳ፡ ፷፤ ፩።
ሮሜ፡ ፲፫፤ ፲፩።
፲፭፤ አሁንም፡ እዩ፡ እንዴት፡ ተጠንቅቃችሁ፡ እን
ድትመላለሱ፡እንደ፡ሰነፎች፡አይደለም፡ እንደ፡ ጠቢ
ባን፡ እንጂ። ማቴ፡ ፲፤ ፲፮። ቆላ፡ ፬፤ ፭።
፲፮፤ ዘመኑን፡ የምትዋጁ፡ ሁኑ፡ ይህች፡ ወራት፡ ክ
ፉ፡ወራት፡ ናትና። ሮሜ፡ ፲፪፤ ፲፩።
፲፯፤ ስለዚህም፡ ሰነፎች፡ አትሁኑ፡እግዚአብሔር፡
የሚወደውን፡ አስተውሉ፡ እንጂ። ቈ፡ ፲።
፲፰፤ በጠጅም፡ አትስከሩ፡ ጥፋት፡ ያለበት፡ መንፈ
ስ፡ይሞላባችሁ፡ እንጂ። ሉቃ፡ ፳፩፤ ፴፬።
፲፱፤ እርሱ፡ በርሳችሁም፡ ተናገሩ፡ በመዝሙር፡
በምስጋናም፡ በመንፈሳዊም፡ ዝማሬ፡ ለእግዚአብ
ሔር፡ ስትቀኙ፡ ስታዘምሩም፡ በልባችሁ።
መዝ፡ ፴፫፤ ፪፤ ፫፤ ቆላ፡ ፫፤ ፲፮።
፳፤ ሁልግዜም፡ስለ፡ሁሉም፡ በየሱስ፡ ክርስቶስ፡ በ
ጌታችን፡ ስም፡ ለእግዚአብሔርና፡ለአብ፡አመስግኑ።
፳፩፤ እርሱ፡ በርሳችሁም፡ በእግዚአብሔር፡ ፍርሃ
ት፡ተገዙ። ፩፤ ጴጥ፡ ፭፤ ፭።
፳፪፤ እላንት፡ ሴቶች፡ ለባሎቻችሁ፡ ተገዙ፡ ለጌታ፡
እንደምትገዙ። ዘፍ፡ ፫፤ ፲፮። ቆላ፡ ፫፤ ፲፰።
፩፤ ጴጥ፡ ፫፤ ፩።
፳፫፤ *ወንድ፡የሴት፡ራስ፡ ነውና፡ ክርስቶስ፡ የቤተ፡
ክርስቲያን፡ ራስ፡ እንደሆነ። እርሱም፡ ሥጋውን፡ የሚ
ያድን፡ነው። *፩፤ ቆሮ፡ ፲፩፤ ፫።
፳፬፤ ቤተ፡ክርስቲያንም፡ለክርስቶስ፡ እንድትገዛ፡
እንደሁም፡ ሴቶች፡ ለባሎቻቸው፡ ይገዙ፡ በሁሉ።

፳፭፡ እላንተ፡ ወንዶች፡ ምሽቶቻችሁን፡ ውደዱ፡ ክርስቶስ፡ቤተ፡ክርስቲያኒቱን፡ እንደ፡ ወደደ፡ ስለርስ ዋም፡ራሱን፡እንደ፡ለወጠ። ቆላ፡ ፫፡ ፲፱።

፳፮፡ *በውኃ፡ ማፀብያ፡ በቃሉም፡ ያነጻት፡ ዘንድ፡ ይቀድሳትም፡ ዘንድ፡ *ቲቶ፡ ፫፡ ፭፡

፳፯፡ እርሰዋን፡ ለማቀም፡ ለርሱ፡ የተመሰገነች፡ አድርጎ፡እድፍ፡ ርኩስትም፡እንደዚህ፡ ያለውንም፡ ሁሉ፡ የሚመስል፡የሌለባት፡ ንጽሕት፡ እንድትሆን፡እ ንጂ፡ያለ፡ነውርም። መዝ፡ ፵፭፡ ፲፩። ፪፡ ቆሮ፡ ፲፩፡ ፪።

፳፰፡ እንደሁም፡ ይገባል፡ ለወንዶች፡ ሴቶቻቸው ን፡እንደ፡ሥጋቸው፡ይወዱ፡ ዘንድ። ምሽቱን፡ የሚወ ድ፡ራሱን፡ይወዳልና።

፳፱፡ ማንም፡ ሥጋውን፡ የሚጠላ፡ ከቶ፡ የለምና፡ ይመግባዋል፡እንጂ፡ያቅፈዋልም፡ ክርስቶስም፡ ለቤ ተ፡ክርስቲያኒቱ፡ እንደደረገ።

፴፡ እኛ፡ የሥጋው፡ ብልቶች፡ ነንና፡ ከሥጋው፡ ካጽ ንቱም። ም፡ ፩፡ ፳፫። ፩፡ ቆሮ፡ ፮፡ ፲፭።

፴፩፡ ስለዚህም፡ ሰው፡ አባቱንና፡ እናቱን፡ ይተዋ ል፡ለምሽቱም፡ይጣበቃል። ሁለቱም፡አንድ፡ ሥጋ፡ይ ሆናሉ። ዘፍ፡ ፪፡ ፳፬። ማቴ፡ ፲፱፡ ፭።

፴፪፡ ይህም፡ምሥጢር፡ታላቅ፡ነው፡እኔ፡ግን፡ ስለ፡ ክርስቶስና፡ስለ፡ ቤተ፡ ክርስቲያን፡ ተናግሬያለሁ።

፴፫፡ ይህም፡ሳይቀር፡ከላንትም፡ኢያንዳንዳችሁ፡ ምሽቱን፡ይውደድ፡ እንደ፡ራሱ። ምሽቱም፡ባልዋን፡ የምትፈራ፡ ትሁን።

ምዕራፍ፡ ፮፡

፩፡ *ልጆች፡ለወለጆቻችሁ፡ታዘዙ፡በጌታችን፡ ይህ፡ የቀና፡ ነውና። *ቆላ፡ ፫፡ ፳።

፪፡ አባትህንና፡ እናትህን፡ አክብር ። ከትእዛዛቱ፡ ይህች፡ መጀመርያዪቱ፡ ናትና፡ ከተስፋ፡ ጋራ፡ የም ትገባል። ዘፀአ፡ ፳፡ ፲፪።

፫፡ መልካም፡ እንዲሆንልህ፡ ዕድሜህም፡ እንዲ ረዝም፡ በምድር፡ላይ።

፬፡ እላንትም፡አባቶች፡ ልጆቻችሁን፡ አታስቈጡ፡ አሳድጓቸው፡ እንጂ፡ በእግዚአብሔር፡ ተግሣጽና፡በ ምክሩ። ዘዳግ፡ ፮፡ ፯፡ ፳። መዝ፡ ፸፰፡ ፬። ምሳ፡ ፲፱፡ ፲፰። ቆላ፡ ፫፡ ፳፩።

፭፡ እላንትም፡ ባሮች፡ ለጌቶቻችሁ፡ በሥጋ፡ ተገዙ፡ በፍርሃት፡ በድንጋጼም፡ በልባችሁ፡ ቅንነት፡ ለክርስቶ ስ፡ እንድትገዙ። ቲቶ፡ ፪፡ ፱። ፩፡ ጴጥ፡ ፪፡ ፲፰።

፮፡ መገዛታችሁም፡አይሁን፡በዓይን፡ፊት፡ሰውን፡ ደስ፡ለማሰኘት፡ነገር፡ግን፡እንደ፡ክርስቶስ፡ባሮች፡ የእ ግዚአብሔርን፡ፈቃድ፡እንደሚያደርጉ፡ከነፍሳችሁ።

፯፡ በመልካም፡ አሳብ፡ተገዙ፡ ለእግዚአብሔር፡እ ንዲገዛ፡ ለሰውም፡ አይደለም።

፰፡ አውቃችሁ፡ሁሉ፡የሚያደርገውን፡ መልካም፡ ነገር፡ እንዲቀበል፡ ከእግዚአብሔር፡ዘንድ፡ ባርያም፡ ቢሆን፡ የሰው፡ልጅም፡ቢሆን። ፪፡ ቆሮ፡ ፭፡ ፲።

፱፡ እላንትም፡ *ጌቶች፡ እንደህ፡ አድርጉባቸው፡ ቍጣውንም፡ ተውት፡ አውቃችኋልና፡ የላንትም፡ ደ ግሞ፡ጌታችሁ፡በሰማይ፡እንደ፡ለ፡ †አድልዎም፡ የለበ ትም። *ቆላ፡ ፬፡ ፩። †ዮሐዋ፡ ፲፡ ፴፬።

፲፡ በቀረውም፡ ወንድሞቼ፡ ሆይ፡ በእግዚአብሔ ር፡ ጽኑ፡ በኃይሉም፡ ችሎት። ፩፡ ቆሮ፡ ፲፮፡ ፲፫። ፩፡ ዮሐ፡ ፪፡ ፲፬።

፲፩፡ የእግዚአብሔርን፡እቃ፡ጦር፡ሁሉ፡ልበሱ፡ የሰ ይጣንን፡ተንኰል፡ትቋቋሙ፡ዘንድ፡እንዲቻላችሁ። ፪፡ ቆሮ፡ ፲፡ ፬።

፲፪፡ መታገላችን፡ከሥጋና፡ከደም፡ጋራ፡ አይደለም ና፡*ከገዦችና፡ ከሥልጣናት፡ጋራ፡ እንጂ፡ በዚህ፡ ዓለ ም፡ጨለማ፡ላይ፡ከሚገዙ፡ ጋራ፡ እንጂ፡ በሰማይም፡ ታች፡ ከምትኖር፡ ከመንፈሳዊት፡ ዓመፃ፡ ጋራ። *ዮሐ፡ ፲፬፡ ፴። ኤፌ፡ ፪፡ ፪።

፲፫፡ ስለዚህም፡ የእግዚአብሔርን፡ እቃ፡ጦር፡ ሁ ሉ፡ልበሱ፡ በክፉ፡ቀን፡መቋቋምሁ፡ ስራውንም፡ ሁሉ፡ በፈጸማችሁ፡ ጊዜ፡ መቆም፡ እንድትችሉ።

፲፬፡ አሁንም፡ *ቁሙ፡ ወገባችሁንም፡ በውነት፡ ታ ጠቁ፡የጽድቅንም፡†ጥሩር፡ልበሱ። *ሉቃ፡ ፲፪፡ ፴፭። ፩፡ ጴጥ፡ ፩፡ ፲፫። †ኢሳ፡ ፶፱፡ ፲፯።

፲፭፡ እግራችሁም፡ ተጫምታ፡ ትሁን፡ በሰላም፡ወ ንጌል፡ መዘጋጀት።

፲፮፡ ከዚህም፡ ሁሉ፡ ጋራ፡*የሃይማኖትን፡ ጋሻ፡ ው ሰዱ።እሳት፡ የምታቃጥለውን፡ የክፉውን፡ ፍላፃ፡ሁ ሉ፡ታጠፉ፡ ዘንድ፡ የምትችሉበት። *፩ ጴጥ፡ ፭፡ ፱። ፩፡ ዮሐ፡ ፭፡ ፬።

፲፯፡ በራሳችሁም፡ የመድኃኒት፡ ራስ፡ ቍር፡ ጫኑ፡ የመንፈስንም፡ ሰይፍ፡ ውሰዱ። እርሱም፡ የእግዚአ ብሔር፡ቃል፡ያለ። ፩፡ ተሰ፡ ፭፡ ፰።

፲፰፡ በጸሎትና፡ በልመናም፡ ሁሉ፡ሁለግዜ፡ በመን ፈስ፡ ጸልዩ፡ ለዚህም፡ትጉ፡ አዘውትራችሁ፡ ስትለም ኑ፡ስለ፡ ቅዱሳን፡ ሁሉ።

፲፱፡ *ስለኔም፡ ደግሞ፡ ነገር፡ ይሰጠኝ፡ ዘንድ፡ †ገ ፈ፡ መክፈቻ፡ የወንጌልን፡ መሥጢር፡ ገልጬ፡ ለመና ገር። ቆላ፡ ፬፡ ፫። ፪፡ ተሰ፡ ፫፡ ፩። †ዮሐዋ፡ ፬፡ ፴፬።

፳፡ እኔ፡ በምክንያቱ፡ በሰንሰለት፡ ታሥሬበት፡ ያ ለሁ፡ መልክተኛው፡ ስሆንለት፡እገልጠው፡ዘንድ፡ መ ናገር፡ እንዲገባኝ። *፪፡ ቆሮ፡ ፭፡ ፳።

፳፩፡ እላንትም፡ ደግሞ፡ ታውቁ፡ ዘንድ፡ ምን፡የ ምሰራውን፡ ሁሉን፡ ይነግራችኋል፡ *ጢኪቆስ፡ የተወ ደደ፡ ወንድም፡ የታመነም፡ አገልጋይ፡ በጌታችን። *ዮሐዋ፡ ፳፡ ፬። ፪፡ ጢሞ፡ ፬፡ ፲፪።

፳፪፤ ወደላንት፡ የላክሁት፡በዚህ፡ ነገር፡በኔ፡ ዘንድ፡
ያለውን፡ ታውቁ፡ ዘንድ፡ ልባችሁንም፡ ያጽና፡ዘንድ።
ቆላ፡ ፬፤ ፯፤፤
፳፫፤ ሰላም፡ በወንድሞቻችን፡ ላይ፡ ይሁን፡ ፍቅር
ም፡ ከሃይማኖት፡ ጋራ፡ ከአብ፡ ከእግዚአብሔር፡ከጌ
ታችንም፡ ከየሱስ፡ ክርስቶስ።
፳፬፤ *ጸጋ፡ ይሁን፡ ጌታችንነንም፡ የሱስ፡ ክርስቶስን፡
ባለ፡ መለወጥ፡ ለሚወዱት፡ ሁሉ። አሜን።
*፪፤ ቆሮ፡ ፲፫፤ ፲፫፤፤

ወደ፡ ኤፌሶን፡ ሰዎች፡ ከሮሚ፡ ተጻፈች፡ በ
ጢኪቆስ፡ እጅ።

# የሐዋርያ ፡ የጳውሎስ ፡ መልእክት ፡ ወደ ፡ ፊልጵስዩስ ፡ ሰዎች ፡

ምዕራፍ፡ ፩፤

፩፤ ከጳውሎስና፡ ከጢሞቴዎስ፡ የየሱስ፡ ክርስቶ
ስ፡ ባሮች። *ወደ፡ ቅዱሳን፡ ሁሉ፡ በክርስቶስ፡ የሱስ፡
በፊልጵስዩስ፡ የሚኖሩ፡ ከኤጲስቆጶሳት፡ ከዲያቆና
ትም፡ ጋራ። *፩፤ ቆሮ፡ ፩፤ ፪፤፤ ፩፤ ጢሞ፡ ፫፤ ፩፤ ፰፤፤
፪፤ ጸጋ፡ ለላንት፡ ይሁን፡ ሰላምም፡ ከእግዚአብሔ
ር፡ ካባታችን፡ ከጌታም፡ ከየሱስ፡ ክርስቶስ።
ሮሜ፡ ፩፤ ፯፤፤
፫፤ አምላኬን፡ *አመሰግናለሁ፡ በማሰባችሁ፡ አሳ
ብ፡ ሁሉ። *ሮሜ፡ ፩፤ ፰፤፤ ፩፤ ቆሮ፡ ፩፤ ፬፤፤
፬፤ ሁሉግዜ፡በልመናዬ፡ ሁሉ፡ ስለላንት፡ ስለ፡ ሁላ
ችሁ፡ ልመናዬን፡ ሳደርግ፡ በደስታ።
፭፤ በወንጌል፡ ስላላቻችሁ፡ አንድነት፡ በፊተኛው፡
ቀን፡ ጀምራችሁ፡ እስከ፡ ዛሬ፡ ድረስ።
፮፤ በዚህ፡ አምኜ፡ በላንት፡ መልካሙን፡ ስራ፡የጀ
መረ፡ እርሱ፡ደግሞ፡ እንፈጽመው፡እስከ፡የሱስ፡ ክ
ርስቶስ፡ቀን፡ ድረስ። ም፡ ፪፤ ፫፤፤ ፩፤ ቆሮ፡ ፩፤ ፮፤—፰፤፤
፯፤ ለኔ፡ እንደሚገባ፡ ይህነን፡ በላንት፡ በሁላችሁ፡
አምን፡ ዘንድ፡ በልቤ፡ ስለ፡ ኖራችሁ፡ *በሥራቴም፡ በ
ምላሼም፡በወንጌልም፡ መጽናት፡ እላንት፡ሁላችሁ፡
ከኔ፡ ጋራ፡ በጸጋ፡ ተካፋዮች፡ ናችሁና።
*ኤፌ፡ ፫፤ ፩፤፤ ፮፡ ፬፤ ፩፤፤
፰፤ እግዚአብሔር፡ ይመሰክርልኛልና፡ ለሁላችሁ፡
እንድናፈቅላችሁ፡ በክርስቶስ፡ የሱስ፡ ምህረት።
፱፤ ይህነንም፡ እጸልያለሁ፡ ፍቅራችሁ፡ ኢያደገች፡
ትበዛ፡ ዘንድ፡ በብዙ፡ *እውቀት፡ በመንፈሳዊት፡ ፍ
ርድም፡ ሁሉ። *ኤፌ፡ ፩፤ ፰፤፤
፲፤ የሚሻለው፡ ነገር፡ ትፈትኑ፡ዘንድ፡ ፍጹማንም፡
ትሆኑ፡ ዘንድ፡ ያለ፡ *ዕንቅፋትም፡ እስከ፡ ክርስቶስ፡
ቀን፡ ድረስ። *ሮሜ፡ ፲፪፤ ፪፤፤ ፩፤ ተሰ፡ ፭፤ ፳፫፤፤
፲፩፤ ከየሱስ፡ ክርሰቶስም፡ የሚገኘውን፡ የጽድቅ
ን፡ *ፍሬ፡ ትመሉ፡ዘንድ፡ለእግዚአብሔር፡ምስጋናና፡
ክብር። *ኤፌ፡ ፭፤ ፱፤፤
፲፪፤ እወዳለሁ፡ ግን፡ ወንድሞቼ፡ ሆይ፡ ታውቁ፡ ዘ
ንድ፡ በኔ፡ ያለው፡ መከራ፡ ወንጌል፡ አብዝቶ፡ እንደ
ጸና። ፪፤ ጢሞ፡ ፪፤ ፱፤፤
፲፫፤ እሥራቴም፡ በክርስቶስ፡ ፈጽሞ፡እንደ፡ ተገለ
ጠ፡ በፍርድ፡ ቤት፡ ሁሉ፡ በቀረውም፡ ስፍራ፡ ሁሉ።
ም፡ ፬፤ ፳፪፤፤
፲፬፤ ከወንድሞችም፡ የሚበልጡቱ፡ በጌታ፡ አመ
ኑ፡ *በመታሠሬ፡ በብዙ፡ ድፍረትም፡ ጨመሩ፡ የእግ
ዚአብሔርን፡ ነገር፡ ይናገሩ፡ ዘንድ፡ ያለ፡ ፍርሃት።
*ኤፌ፡ ፫፤ ፲፫፤፤ ፩፤ ተሰ፡ ፫፤ ፫፤፤
፲፭፤ ከሰዎችም፡ ተከፍለው፡ ስለ፡ ቅናትና፡ ስለ፡
ምቀኝነት፡ የቀሩትም፡ ከበጎ፡ ፈቃድ፡ *በክርስቶስ፡
ያስተምራሉ። ፪፤ ቆሮ፡ ፪፤ ፲፯፤፤
፲፮፤ እሌህም፡በፍቅር፡የሚያስተምሩ፡ያውቃሉ፡
ስለ፡ ወንጌል፡ ምላሽ፡ እንደ፡ተቀመጥሁ።
፲፯፤ በምቀኝነት፡ ግን፡በክርስቶስ፡የሚያስተምሩ፡
ያለ፡ ንጽሕና፡ ያስተምሩታል፡ በሥራቴ፡ ላይ፡ መጨነ
ቅ፡ ይጨምሩ፡ ዘንድ፡ ቢመስላቸው። ቍ፡ ፯፤፤
፲፰፤ ነገር፡ ግን፡ ይህ፡ ምን ፡ ያደርጋል። በሁሉ፡ ነገር፡
በምቀኝነት፡ ቢሆን፡ በውነትም፡ ቢሆን፡ በክርስቶስ፡
ያስተምራሉ። *በዚህም፡ ደስ፡ አለኝ፡ ደግሞም፡ ደ
ስ፡ ይለኛል። *ም፡ ፪፤ ፲፯፤ ፲፰፤፤
፲፱፤ አውቃለሁና፡ ይህ፡ ለደህንነት፡ እንዲበጀኝ፡
*በጸሎታችሁ፡ በየሱስ፡ ክርስቶስም፡ መንፈስ፡ ስጦ
ወታ። *፪፤ ቆሮ፡ ፩፤ ፲፩፤፤
፳፤ ተስፋ፡ እንደደረግሁ፡ደግሞም፡ ተስፋ፡ አደር
ጋለሁ፡ በሁሉ፡ እንዳላፍር፡ በደፍረት፡ ሁሉ፡ ግን፡ ሁለ
ግዜ፡ እንደ፡ ሆነ፡ አሁንም፡ ደግሞ፡ ክርስቶስ፡ እንዲ
መሰገን፡ በሥጋዬ፡ በሕይወቴም፡ ቢሆን፡ በሞቴም፡
ቢሆን። ፩፤ ጴጥ፡ ፬፤ ፲፮፤፤
፳፩፤ ሕይወቴ፡ ለኔ፡ ክርስቶስ፡ ነውና፡ መሞትም፡
ለኔ፡ ጥቅሜ፡ ነው። ገላት፡ ፪፤ ፳፤፤
፳፪፤ በሥጋዬ፡ ግን፡ ሕያው፡ብሆን፡ ይህ፡ ፍሬ፡ ለስ
ራዬ፡ የምመርጠውንም፡ አላውቅም።
ሮሜ፡ ፩፤ ፲፫፤፤
፳፫፤ እሌህም፡ ሁለቱ፡ ነገር፡ *አስጨነቁኝ። እወደ
ለሁና፡እፈልስ፡ዘንድ፡ ከክርስቶስም፡ ጋራ፡ እኖር፡ ዘን
ድ። ይህም፡ ለኔ፡ ይሻለኝ፡ በሆነ። *፩፤ ነገሥ፡ ፲፱፤ ፬፤፤
፪፤ ቆሮ፡ ፭፤ ፰፤፤
፳፬፤ በሥጋዬ፡ግን፡መኖር፡ይህ፡ስለላንት፡ይገደል።

፳፭፡ አምናለሁም፡*አውቅማለሁ፡እንድኖር፡ከ
ላንት፡ከሁላችሁ፡ጋራ፡አበረ፡ለማደጋችሁ፡ለሃይማ
ኖታችሁም፡ደስታ፡እንድኖር። ም፡ ፪፡ ፳፬፡፡
፳፮፡ ትምክሕታችሁ፡ደበዛ፡ዘንድ፡በክርስቶስ፡የ
ሱስ፡በምክንያቴ፡ወደላንት፡ደግሞ፡ በመጣሁ፡ጊዜ።
፳፯፡ ተሠረ፡ብቻ፡ለክርስቶስ፡ወንጌል፡እንደ፡ገባ፡
ከመጣሁ፡ጊዜ፡ በዚያው፡እንደያችሁ፡ባልመጣም፡
ስለላንት፡ እሰማ፡ ዘንድ፡ ባንድ፡ መንፈስ፡ እንደ፡ ጸና
ችሁ፡ ባንድም፡ ነፍስ፡ እንድትዋጉ፡ ስለ፡ ወንጌል፡ ሃይ
ማኖት። *ቆል፡ ፩፡ ፲፡፡ ፩፡ ተሰ፡ ፪፡ ፲፪፡፡
፩፡ ጢሞ፡ ፩፡ ፲፰፡ ፲፱፡፡
፳፰፡ ከጸላቶችም፡ ባንድ፡ ነገር፡ እንዳትደነግጡ።
ጥፋታቸው፡በዚህ፡ደገለጣልና፡የላንትም፡ደህንነት።
ደህም፡ ከእግዚአብሔር፡ ዘንድ። ፩፡ ጴጥ፡ ፫፡ ፲፬፡፡
፳፱፡ ለላንት፡ደህ፡ጸጋ፡ ተሰጥትዋችኋልና፡ በክርስ
ቶስ፡ ታምኑ፡ ዘንድ፡ብቻ፡ አይደለም፡ መከራም፡ ደግ
ሞ፡ ትቀበሉ፡ ዘንድ፡ ነው፡ እንጂ፡ በመክንያቱ።
ሮሜ፡ ፭፡ ፫፡፡
፴፡ *መጋደልንም፡ ስትጋደሉ፡ በኔ፡ እንደያችሁት፡
አሁንም፡ ስምታችኋል፡ በኔ፡ እንደለ።
*የሐዋ፡ ፲፯፡ ፳፪፡፡ ቆለ፡ ፩፡ ፳፱፡፡

ምዕራፍ፡ ፪፡

፩፡ ማጽናናትም፡ እንደላችሁ፡ በክርስቶስ፡ ወደ
ም፡የልብ፡ደስታ፡ በፍቅር፡ ወደም፡ *ከመንፈስ፡ ቅዱ
ስ፡ ጋራ፡ አንድነት፡ ወደም፡ ምሀረት፡ ደቅርታም።
*ኤፌ፡ ፬፡ ፩—፫፡፡
፪፡ ደስታዬን፡ ፈጽሙ፡ አንድ፡ ምክር፡ እንዲሆንላ
ችሁ፡ እንዲ፡ትም፡ፍቅር። የነፍስም፡አንድነት፡ አንድ፡
ልብም። ሮሜ፡ ፲፪፡ ፲፮፡፡ ፩፡ ቆር፡ ፩፡ ፲፡፡
፫፡ ምንም፡አታድርጉ፡በጸብ፡በከንቱም፡ ውደሴ።
ነገር፡ ግን፡ በልብ፡ ትሕትና፡ ከላንት፡ኢያንዳንዲ፡ ባል
ንጀራውን፡ ከራሱ፡ አልቀ፡ ያክብር። ገላት፡ ፭፡ ፳፯፡፡
ሮሜ፡ ፲፪፡ ፲፡፡
፬፡ ያም፡ያም፡ *ለራሱ፡ብቻ፡ አይመልከት፡ለባልን
ጀራውም፡ እንጂ፡ ደግሞ። ፩፡ ቆሮ፡ ፲፡ ፳፬፡ ፴፫፡፡
፭፡ በላንትም፡በክርስቶስ፡የሱስ፡የነበረ፡ልብ፡ ደሁ
ንባችሁ። ዮሐ፡ ፲፫፡ ፲፭፡፡
፮፡ እርሱ፡በእግዚአብሔር፡ *መልክ፡ ሲኖር፡ ከእግ
ዚአብሔር፡ጋራ፡ ደተካከል፡ ዘንድ፡ መቅማትን፡ አል
ቈጠረም። *ቆለ፡ ፩፡ ፲፭፡፡ ዮሐ፡ ፩፡ ፩፡ ፪፡፡ ፲፮፡ ፭፡፡
ዘፍ፡ጥ፡ ፫፡ ፭፡፡
፯፡ ራሱን፡ለምናምን፡አደረገ፡ *የባርያውንም፡መ
ልክ፡ ደዞ፡ በሰዎች፡ ምሳሌ፡ ሆነ። *ኢሳ፡ ፶፫፡ ፫፡፡
፪፡ ቆሮ፡ ፰፡ ፱፡፡ ዕብ፡ ፪፡ ፲፬፡ ፲፮፡፡
፰፡ በመልኩም፡ ሰው፡ሁኖ፡ተገኘ፡ራሱንም፡ *አዋ
ረደ፡እስከ፡ ሞት፡ ድረስም፡ የታዘዘ፡ሆነ፡ እስከ፡ መስ
ቀል፡ ሞት፡ ድረስ። *ዕብ፡ ፲፪፡ ፪፡፡ ፭፡ ፰፡፡
፱፡ ስለዚህም፡እግዚአብሔር፡አጅግ፡አላቀው፡ከ
ስም፡ ሁሉ፡ የሚበልጠውን፡ ስም፡ ሰጠው።
የሐዋ፡ ፪፡ ፴፫፡፡ ኤፌ፡ ፩፡ ፳፩፡፡ ዕብ፡ ፩፡ ፫፡ ፬፡፡
፲፡ በየሱስ፡ስም፡ *ጉልበት፡ ሁሉ፡ደጐነብስ፡ ዘንድ፡
በሰማይ፡በምድርም፡ከምድር፡በታችም፡ ያለ፡ሁሉ።
*ዮሐ፡ ፭፡ ፳፫፡፡ ራእ፡ ፭፡ ፲፫፡፡ ኢሳ፡ ፵፭፡ ፳፫፡፡
፲፩፡ መላስም፡ ሁሉ፡ የሱስ፡ ክርስቶስ፡ጌታ፡ እንደ፡
ሆነ፡ያስታውቅ፡ዘንድ፡ለእግዚአብሔር፡አብ፡ ክብር።
የሐዋ፡ ፪፡ ፴፮፡፡ ፲፡ ፴፮፡፡ ዮሐ፡ ፭፡ ፳፫፡፡
፲፪፡ ስለዚህም፡ ወደጆቼ፡ሆይ፡እንደ፡ ታዘዛችሁል
ኝ፡ሁለግዜ፡ከላንት፡ጋራ፡ ሳለሁ፡ አይደለም፡ ደልቁን
ም፡ ከሌለሁ፡ እንጂ፡ በፍርሃት፡ *በድንጋጼም፡ መድ
ኃኒታችሁ፡የሚገኝበቱን፡አድርጉ። ፩፡ ጴጥ፡ ፩፡ ፲፯፡፡
*መዝ፡ ፪፡ ፲፩፡፡
፲፫፡ እርሱ፡ እግዚአብሔር፡ ያደርግባችኋልና፡ ትወ
ዲ፡ዘንድ፡ ታደርጉም፡ ዘንድ፡ እንደ፡ ፈቃዲ።
ዮሐ፡ ፲፭፡ ፭፡፡ ፪፡ ቆር፡ ፫፡ ፭፡፡
፲፬፡ የምታደርጉትን፡ሁሉ፡ ያለ፡ ማንጐርጐር፡አድ
ርጉ፡ያለ፡ክርክርም። ፩፡ ጴጥ፡ ፬፡ ፱፡፡
፲፭፡ ያለ፡ነውር፡የማደበድሉም፡ትሆኑ፡ዘንድ፡እን
ደ፡*ንጹሓን፡እንደ፡እግዚአብሔር፡ልጆች፡ በጠማማ
ና፡ በከፋ፡ ትውልድ፡ መካከል። በመካከላቸው፡ እን
ደ፡ተብርሃን፡በዚህ፡ዓለም፡የምታበሩ። *ም፡ ፩፡ ፲፡፡
ተማቴ፡ ፭፡ ፲፬፡፡ ኤፌ፡ ፭፡ ፰፡፡
፲፮፡ በሕይወት፡ቃል፡ተደዛችሁ፡እኔ፡ *እንድመካ፡
በክርስቶስ፡ ቀን፡ ተበከንቱ፡ እንዳልሮጥሁ፡ በዝምብ
ሎም፡እንዳልደከምሁ። ፩፡ ተሰ፡ ፪፡ ፲፱፡፡
ተኢሳ፡ ፵፱፡ ፬፡፡ ገላት፡ ፪፡ ፪፡፡ ቲጦ፡ ፩፡ ፱፡፡
፲፯፡ ነገር፡ግን፡ *ብሠዋም፡ደግሞ፡ስለ፡ሃይማኖታች
ሁ፡መሥዋዕት፡ስለ፡ ማገልገልዋም። እጅግ፡ደስ፡ደለ
ኛል፡ከሁላችሁ፡ ጋራ። ፪፡ ጢሞ፡ ፬፡ ፮፡፡
፲፰፡ በዚህም፡ ደግሞ፡ እላንት፡ ደስ፡ ደበላችሁ፡
ከኔ፡ ጋራ። ም፡ ፫፡ ፩፡፡ ፬፡ ፬፡፡
፲፱፡ ነገር፡ ግን፡ በጌታ፡ በየሱስ፡ ተስፋ፡ አደርጋለሁ፡
ጢሞቴዎስን፡ ፈጥኜ፡ ወደላንት፡ እሰደው፡ ዘንድ፡ ም
ውነቴ፡ታርፍ፡ ዘንድ፡እንደት፡ እንደላችሁ፡ ባወቅሁ፡
ጊዜ።
፳፡ ማንም፡ እንደ፡ ራሴ፡ የሚያስብ፡ የለኝምና፡
*ከርሱ፡ በቀር። *፩፡ ቆር፡ ፲፮፡ ፲፡፡
፳፩፡ ሁሉ፡ የራሳቸውን፡ መርባት፡ ብቻ፡ ደሻሉና፡የ
የሱስ፡ ክርስቶስንም፡ አይደለም።
፪፡ ጢሞ፡ ፬፡ ፲፡ ፲፮፡፡
፳፪፡ እላንት፡ግን፡ደህነን፡ሰው፡ አውቃችሁታል፡እ
ንደ፡ልጅ፡ ካባቱ፡ ጋራ፡ እንደገለገለ፡ ከኔ፡ጋራ፡ በወንጌ
ል። ፩፡ ጢሞ፡ ፩፡ ፪፡፡
፳፫፡ እርሱን፡ተስፋ፡አደርጋለሁ፡እሰደው፡ ዘንድ፡
የሚሆነውን፡ ነገሬን፡ ባየሁ፡ጊዜ።
፳፬፡ በእግዚአብሔርም፡ አምናለሁ፡ እኔም፡ ወደ
ላንት፡ እንድመጣ፡ ፈጥኜ። ም፡ ፩፡ ፳፭፡፡
፳፭፡ አሁን፡ግን፡አስብሁ፡ወንድምን፡ *ኤጳፍሮዲ

ጦስን፡እልክላችሁ፡ ዘንድ፡ እንዲገባ። እርሱም፡ ባል ንጀራዬ፡ ከኔም፡ጋራ፡አብሮ፡ የሚሰራና፡ የሚዋጋ፡ ለ ላንት፡ መለክተኛ፡ የሚሆን፡ የምሻውንም፡ የሚፈ ጽም። *ም፡ ፬፡ ፲፰፡፡ ፪፡ ቆሮ፡ ፰፡ ፳፫፡፡

፳፮፡ ደናፍቅ፡ ነበርና፡ ሁላችሁን፡ ያያችሁ፡ ዘንድ፡ ልቡም፡አዝኖ፡ነበር፡ መታመሙን፡ ብትሰሙ።

፳፯፡ በውነትም፡ፈጽሞ፡ ታመመ፡ ለሞት፡ እስኪ ደርስ። ነገር፡ግን፡እግዚአብሔር፡ማረው፡ እርሱንም፡ ብቻ፡ አይደለም፡ እኔንም፡ እንጂ፡ ደግሞ። አዘኔ፡ መ ጨነቄም፡እንዳይበዛ። ዮሐ፡ ፬፡ ፵፯፡፡ ኢሳ፡ ፴፰፡ ፩፡፡

፳፰፡ አሁንም፡ቀልጥፌ፡ ሰደድሁት፡ ደስ፡ እንዲላ ችሁ፡ባያችሁት፡ጊዜ፡ ደግሞ፡ እኔም፡ ደግሞ፡ ያላዘን፡ እንድሆን።

፳፱፡ እንጊዲህ፡በእግዚአብሔር፡*ተቀበሉት፡በደ ስታ፡ሁሉ፡እንደለዚያ፡ ሰዎችም፡ በላንት፡ዘንድ፡ የከ በሩ፡ ይሁኑ። ፩፡ ቆሮ፡ ፲፮፡ ፲፰፡፡ *ሮሜ፡ ፲፮፡ ፪፡፡

፴፡ ስለ፡ክርስቶስ፡ ስራ፡ ወደ፡ ሞት፡ ደርሰዋልና፡ ስ ውነቱንም፡ደፈረ፡ በላንት፡ ዘንድ፡ የጐለውን፡ ይፈጽ ም፡ ዘንድ፡ *ለኔ፡ በማገልገል። *፩፡ ቆሮ፡ ፲፮፡ ፲፡ ፲፯፡፡ ዮሐ፡ ፳፡ ፳፬፡፡

ምዕራፍ፡ ፫፡

፩፡ አሁንም፡ወንድሞቼ፡ሆይ፡በእግዚአብሔር፡ደ ስ፡ ይበላችሁ። ይህነን፡ደግሞ፡እጽፍላችሁ፡ዘንድ፡ እ ልታክትም፡እላንትን፡ለማጽናት፡ ነውና። ም፡ ፪፡ ፲፰፡፡ ፬፡ ፬፡፡

፪፡ *ከውሾች፡ ተጠበቁ፡ ክፉ፡ ከሚያደርጉ፡ ተጠበ ቁ። ካስተኛ፡ ግዝረት፡ ሰዎች፡ ተጠበቁ። *ራእ፡ ፳፪፡ ፲፭፡፡ ኢሳ፡ ፶፮፡ ፲፩፡ ፲፪፡፡

፫፡ እኛ፡ነንና፡በውነት፡ የተገዘርነ፡እግዚአብሔርን፡ የምናመልክ፡ በመንፈስ ። በክርስቶስ፡ የሱስም፡ እን መካለን፡ በሥጋም፡ አንታመንም። ሮሜ፡ ፪፡ ፳፱፡፡

፬፡ ምንስ፡በሥጋ፡ደግሞ፡ መታመን፡ ቢሆንልኝ፡ማ ንም፡ ቢመስለው፡ በሥጋው፡ እንዲታመን፡*እኔ፡ ከር ሱ፡ እበልጣለሁ። *፪፡ ቆሮ፡ ፲፩፡ ፲፰፡ ፳፪፡፡

፭፡ የተገዘርሁ፡ነኝና፡በስምንተኛ፡ቀን፡ከእሥራኤ ል፡ትውልድ፡ ከብንያሚን፡ ወገን። ዕብራዊ፡ ከዕብራ ውያን። በኦሪት፡ ሕግ፡ ፈሪሳዊ። የሐዋ፡ ፳፮፡ ፭፡፡

፮፡ በቅናት፡ የቤተ፡ ክርስቲያን፡ አሳደጅ፡ በኦሪት፡ ጽድቅ፡ ያለ፡ ነውር፡ ነበርሁ።

፯፡ ይህነን፡ ሁሉ፡ ግን፡ለኔ፡*ይረባኝ፡ የነበረውን፡ እ ንደ፡ ጉሰቋላ፡ ቈጠርሁት፡ ስለ፡ ክርስቶስ። *ማቴ፡ ፲፫፡ ፵፬፡፡

፰፡ ሁሉንም፡ ደግሞ፡እንደ፡ምናምን፡ እቈጥራለ ሁ፡ስለ፡ጌታዬ፡ስለ፡የሱስ፡ክርስቶስ፡*እውቀት። ይህ፡ ነገሬን፡ ሁሉ፡ ስለርሱ፡ የናቅሁ፡ እንደ፡ጉድፍ፡ም፡የቈ ጠርሁት፡ ክርስቶስን፡ እረባ፡ ዘንድ። *ኢሳ፡ ፶፫፡ ፲፩፡፡

፱፡ በርሱም፡እገኝ፡ዘንድ፡በኦሪትም፡*ጽድቅ፡ እን ደሌለኝ፡ነገር፡ ግን፡ በክርስቶስ፡ ሃይማኖት፡ ከእግዚአ ብሔር፡የሚሆን፡ ጽድቅ፡ በሃይማኖት፡ እንጂ። *ሮሜ፡ ፫፡ ፳፩፡ ፳፪፡፡

፲፡ እርሱን፡አውቀው፡ዘንድ፡ *የትንሣኤውንም፡ ኃይል። †በሕማሙም፡ አንድ፡እሆን፡ ዘንድ፡ በሞቱ ም፡ እመስለው፡ ዘንድ። *ሮሜ፡ ፮፡ ፫፡—፭፡፡ †ሮሜ፡ ፰፡ ፲፯፡፡ ገላት፡ ፮፡ ፲፯፡፡

፲፩፡ ምናልባት ፡ ወደ፡ ሙታን ፡ ትንሣኤ፡ እደርስ፡ ዘንድ።

፲፪፡ እኔም፡ ይህነን፡ *ገና፡ የወሰድሁ፡ የተፈጸምሁ በትም፡አይደለሁም። ነገር፡ግን፡እሮጣለሁ፡አገኘው፡ እንደሆን፡ እኔ፡ †ከየሱስ፡ ክርስቶስ ፡ ተገኝቻለሁና። *፩፡ ጢሞ፡ ፮፡ ፲፪፡፡ †የሐዋ፡ ፱፡ ፮፡፡

፲፫፡ ወንድሞቼ፡ሆይ፡እኔ፡ ግን፡ በሰውነቴ፡ እላስብ ም፡ ፍጻሜ፡ እንደገኘሁ። ዕብ፡ ፲፩፡ ፳፮፡፡

፲፬፡ ነገር፡ግን፡አንድ፡ ነገር፡ አለኝ። በኋላዬ፡ ያለው ን፡ኢየረስሁ፡በፊቴ፡ ወደለው፡ ምልክትንም፡ ኢየተ ዘረጋሁ፡ ኢየተመለከትሁ፡ ወደ፡ *ዋጋውም፡ ፈጥኜ፡ እሮጣለሁ፡ እግዚአብሔር፡ በሰማያዊ፡ መጽራቱ፡ ወ ደመለከተኝ፡በየሱስ፡ክርስቶስ። ፩፡ ቆሮ፡ ፱፡ ፳፬፡፡ ቆላ፡ ፫፡ ፪፡፡

፲፭፡ ፍጹምም፡ የሆነ፡ ሁሉ፡ ይህነን፡ ያስብ። ላላን ትም፡ ቢመስላችሁ፡ ከዚህ፡ ሌላ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይ ህነን፡ ደግሞ፡ ይገልጥላችኋል። ዕብ፡ ፭፡ ፲፬፡፡ ፪፡ ቆሮ፡ ፲፫፡ ፲፩፡፡ ሮሜ፡ ፲፬፡ ፩፡—፮፡፡

፲፮፡ ይህነን፡ ነገር፡ አስቡት፡ እንደገኘኛችሁት፡ መጠ ን፡ ባንድ፡ *መንገድ፡ ትሔዱ፡ ዘንድ፡ ባንድ፡ †አሳብ፡ ትሆኑ፡ ዘንድ። ገላት፡ ፮፡ ፲፮፡፡ †፩፡ ጴጥ፡ ፫፡ ፰፡፡

፲፯፡ እኔን፡*የምትመስሉ፡ሁኑ፡ ወንድሞቼ፡ ሆይ። እንደህም፡የሚሔዱትን፡ተመልከቱ፡ እኛ፡ ምሳሌ፡ እንደ፡ ሆነላችሁ። *፩፡ ቆሮ፡ ፲፩፡ ፩፡፡

፲፰፡ ብዙ፡ሰዎች፡ይሔዳሉና፡ ከርሳቸውም፡ ብዙ፡ ጊዜ፡ ያልኋችሁ፡ አሁንም፡ ደግሞ፡አልቅሼ፡ እላለሁ፡ የክርስቶስ፡የመስቀሉ፡*ጸላቶች፡ እንደሆኑ። *፩፡ ቆሮ፡ ፩፡ ፳፫፡፡ ገላት፡ ፮፡ ፲፪፡፡

፲፱፡ ፍጻሜያቸው፡ ጥፋት፡ያለ። አምላካቸው፡ሆ ደቸው፡ያለ።ክብራቸውም፡በኀፍረታቸው፡ያለ።አሳ ባቸውም፡ በምድር፡ያለ። ሮሜ፡ ፲፮፡ ፲፰፡፡

፳፡ እኛ፡ግን፡*አገራችን፡ በሰማይ፡ ናት፡ ከዚያም፡ መድኃኒታችነን፡ ጌታችነን፡ የሱስ፡ ክርስቶስን፡ እንጠ ብቃለን። *ኤፌ፡ ፪፡ ፮፡፡ ቆላ፡ ፫፡ ፩፡፡ ዕብ፡ ፲፪፡ ፳፪፡፡ ቲቶ፡ ፪፡ ፲፫፡፡

፳፩፡ እርሱ፡ የተዋረደውን፡ *ሥጋችነን፡ የሚለው ጥ፡ለክብረም፡ ሥጋ፡ የሚያስመስለው፡ሁሉን፡ ያስገ ዛባት፡ ዘንድ፡ በሚችል፡ በኃይሉ፡ ታላቅነት። *፩፡ ቆሮ፡ ፲፭፡ ፵፫፡ ፵፱፡ ፶፫፡፡

ምዕራፍ፡ ፬፤

፩፤ አሁንም፡ የምወዳችሁና፡ የምናፍቃችሁ፡ ወን ድሞቼ፡ሆይ፡*ደስታዬ፡አክሊሌም። እንዲሁ፡በጌታ፡ ጽኑ፡ ወዳጆቼ፡ ሆይ። *፪፡ ቆሮ፡ ፩፤ ፲፬፡፡
፩፡ ተሰ፡ ፪፤ ፲፱፤ ፳፡፡

፪፤ ኤዎድያን፡ እኔ፡ እለምናለሁም፡ እንዲሁም፡ ስንጢኪን፡እለምናለሁ፡ አሳባቸው፡አንድ፡ ይሆን፡ዘ ንድ፡ በእግዚአብሔር። ምዕ፡ ፪፤ ፪፡፡

፫፤ ደግሞም፡ እለምንሃለሁ፡ የተመረጥህ፡ የተወ ደድህም፡ አጋዤ፡ ሆይ፡ ታግዛቸው፡ ዘንድ፡ ከኔ፡ ጋራ፡ በወንጌል፡ደክመዋልና፡ከቀሌምንጦስም፡ጋራ፡ ከቀ ሩትም፡ባልንጀሮቼ፡በማገልገል፡*ስማቸው፡የተጻፈ፡ በሕይወት፡ መጽሐፍ። ፊል፡ ፪፡፡ *ራእ፡ ፲፫፤ ፰፡፡
ሉቃ፡ ፲፤ ፳፡፡

፬፤ በእግዚአብሔር፡ *ደስ፡ይበላችሁ፡ ሁልጊዜ። ደ ግሞም፡ እላለሁ፡ደስ፡ ይበላችሁ። *ምዕ፡ ፫፤ ፩፡፡
፪፡ ቆሮ፡ ፲፫፤ ፲፩፡፡ ኢሳ፡ ፷፩፤ ፲፡፡

፭፤ *የውሃታችሁ፡ለሰዎች፡ ሁሉ፡ ትታወቅ። እግዚ አብሔር፡ተቀርብ፡ነው። *ቲቶ፡ ፫፤ ፪፡፡ ያዕ፡ ፭፤ ፰፤ ፱፡፡
†፩፡ ቆሮ፡ ፲፤ ፲፩፡፡

፮፤ በምንም፡ *አታስቡ፡ ነገር፡ ግን፡ በሁሉ፡ †በጸሎ ትና፡በልመና፡ ከምስጋና፡ ጋራ፡ መሻታችሁ፡ በእግዚአ ብሔር፡ ዘንድ፡ ትታወቅ። *ማቴ፡ ፮፤ ፳፭፡፡
፩፡ ጴጥ፡ ፭፤ ፯፡፡ †መዝ፡ ፻፵፭፤ ፲፰፡፡

፯፤ ከአእምሮም፡ ሁሉ፡ የበለጠ፡ *የእግዚአብሔ ር፡ሰላም፡ ልባችሁንና፡ አሳባችሁን፡ ይጠብቅ፡ በክርስ ቶስ፡የሱስ። *ዮሐ፡ ፲፬፤ ፳፯፡፡ ቆላ፡ ፫፤ ፲፭፡፡
ሮሜ፡ ፭፤ ፩፡፡

፰፤ በቀረውም፡ ወንድሞቼ፡ ሆይ፡ *እውነትን፡ ሁ ሉ፡ያዙ፡ ቅንንም፡ ሁሉ፡ ጽድቁንም፡ ሁሉ፡ ንጽሕናን ም፡ሁሉ፡የተወደደውንም፡ስራ፡ሁሉ፡ስሙሙንም፡ ሁሉ፡ በጐነትም፡ ቢሆን፡ ምስጋናም፡ ቢሆን፡ ይህነን፡ አስቡ። *ሮሜ፡ ፲፪፤ ፲፯፡፡

፱፤ ከኔ፡ የተማራችሁትን፡ የወሰዳችሁትንም፡ ከኔ ም፡ የሰማችሁትን፡ በኔም፡ ያያችሁትን። ይህችን፡ አ ድርጊት፡ *የሰላምም፡ አምላክ፡ ከላንት፡ ጋራ፡ ይሆ ናል። *፩፡ ተሰ፡ ፭፤ ፳፫፡፡

፲፤ ነገር፡ ግን፡ እጅግ፡ ደስ፡አለኝ፡ በእግዚአብሔር፡ እንደ፡ጀመራችሁ፡ታስቡኝ፡ ዘንድ፡ደግሞ፡ ምንስ፡ቀ ድሞ፡ታስቡኝ፡ነበራችሁ፡ ነገር፡ግን፡ጊዜ፡ አልሆነችላች ሁም። ፪፡ ቆሮ፡ ፲፩፤ ፱፡፡

፲፩፤ ይህነንም፡ የምል፡ እኔ፡ ስለ፡ሻሁ፡ አይደለም፡ አውቃለሁና፡ *እንዲበቃኝ፡ በሆነልኝ፡ ነገር።
*፩፡ ጢሞ፡ ፮፤ ፮፡፡

፲፪፤ እዋረድ፡ዘንድም፡ አውቃለሁ፡ ከፍ፡ ከፍ፡ም፡ እል፡ዘንድ። በሁሉ፡ጊዜ፡በሁሉም፡ነገር፡ተምሬያለሁ ና፡ይበቃኝ፡ዘንድ፡በጽጋብና፡*በረኃብ፡ በትርፍና፡በመ ጒደል። *፪፡ ቆሮ፡ ፮፤ ፲፡፡ ፲፩፤ ፳፯፡፡

፲፫፤ በሁሉም፡ *እችላለሁ፡ በክርስቶስ፡ በሚያስች ለኝ። *፪፡ ቆሮ፡ ፲፪፤ ፲፡፡ ኢሳ፡ ፵፤ ፳፱፤—፴፩፡፡

፲፬፤ ነገር፡ ግን፡ መልካም፡ አደረጋችሁ፡ አንድ፡ በመ ሆናችሁ፡ ከኔ፡ ጋራ፡ በመከራዬ።

፲፭፤ እላንትም፡ ታውቃላችሁ፡ እላንት፡ የፊልጵስ ዩስ፡ሰዎች፡ በመጀመርያ፡ወንጌል፡ባስተማርሁ፡ጊዜ፡ ከመቄዶንያም፡በወጣሁ፡ ጊዜ፡ ከኔ፡ ጋራ፡ ባንድ፡ የሆ ነ፡የለም፡ አንድ፡ስንኳ፡ *ከአብያተ፡ ክርስቲያናት፡ በ ግቢና፡ በውጭ፡ እላንት፡ ብቻ፡ እንጂ።
፩፤ ጢሞ፡ ፩፤ ፫፡፡ ፪፤ ቆሮ፡ ፲፩፤ ፱፡፡

፲፮፤ በተሰሎንቄ፡ደግሞ፡አንድግዜ፡ ሁለተግዜም፡ የምሻውን፡ ሰደዳችሁልኝልና። የሐዋ፡ ፲፯፤ ፩፡፡

፲፯፤ መስጠታችሁን፡ግን፡ የምሻ፡ አይደለሁም፡ ነገ ር፡ግን፡ ፍሬያችሁ፡ትበዛ፡ዘንድ፡ነው፡ በላንት፡ ምክን ያት። ፩፤ ቆሮ፡ ፱፤ ፲፩፡፡ ቲቶ፡ ፫፤ ፲፬፡፡

፲፰፤ ሁሉን፡ተቀበልሁ፡ከኔም፡ተረፈ። ጸገብሁ፡የደ ከማችሁበትን፡ *ከኤጳፍሮዲጦስ፡ ጋራ፡ በጨበጥሁ፡ ጊዜ፡መዓዛው፡ ያማረውን፡ሽቱ። የተቀበለች፡ መሥ ዋዕት፡ ያለች፡ እግዚአብሔርን፡ደስ፡ የምታሰኝ።
*ምዕ፡ ፪፤ ፳፭፡፡ ኤፌ፡ ፭፤ ፪፡፡ ዕብ፡ ፲፫፤ ፲፮፡፡

፲፱፤ አምላኬም፡ ይከፈላችሁ፡ ከርሱ፡ የምትሹት ን፡ሁሉ፡እንደ፡ክብሩ፡ባለጠግነት፡ በክርስቶስ፡የሱስ።
፪፤ ቆሮ፡ ፱፤ ፰፡፡

፳፤ ለእግዚአብሔርም፡ ላባታችን፡ ምስጋና፡ ይድ ረሰው፡ ለዘላለሙ። አሜን። ገላት፡ ፲፤ ፬፤ ፭፡፡

፳፩፤ ቅዱሳንን፡ሁሉ፡እንደት፡ናችሁ፡ በሉ፡በክርስ ቶስ፡ የሱስ። እንደት፡ ናችሁ፡ ይልዋችኋል፡ ወንድሞ ች፡ ሁሉ፡ ከኔ፡ ጋራ፡ ያሉት። ፩፤ ቆሮ፡ ፲፮፤ ፳፡፡

፳፪፤ ቅዱሳን፡ሁሉ፡እንደት፡ናችሁ፡ ይልዋችኋል፡ ይልቁንንም፡በቄሣር፡ቤት፡ያሉት። ፪፤ ቆሮ፡ ፲፫፤ ፲፪፡፡

፳፫፤ የጌታችን፡የየሱስ፡ክርስቶስ፡ጸጋ፡ ከሁላችሁ፡ ጋራ፡ትኑር። አሜን። ፩፤ ቆሮ፡ ፲፮፤ ፲፫፡፡ ቆላ፡ ፬፤ ፲፰፡፡

ወደ፡ ፊልጵስዩስ፡ ሰዎች፡ ተጻፈች፡ ከሮምያ። ተላከችም፡ ከኤጳፍሮዲጦስ፡ ጋራ።

# የሐዋርያ ፡ የጳውሎስ ፡ መልእክት ፡ ወደ ፡ ቈላሳይስ ፡ ሰዎች ።

ምዕራፍ፡ ፩፤

፩፤ ከጳውሎስ፡ከየሱስ፡ ክርስተስ፡ ሐዋርያ፡ በእግ
ዚአብሔር ፡ ፈቃድ፡ ከጢሞቴዎስም ፡ ከወንድም።
፪፤ ቆሮ፡ ፩፤ ፩።

፪፤ በቈላሳይስ ፡ ወደሚኖሩ ፡ ወንድሞች ፡ በክርስ
ተስ፡የተቀደሱ፡ ያመኑም።*ጸጋ፡ ለላንት፡ ይሁን፡ ሰላ
ምም፡ ካባታችን፡ ከአምላክ፡ከጌታም፡ ከየሱስ፡ ክር
ስተስ።
*ሮሜ፡ ፩፤ ፯።

፫፤ የጌታችንን፡የየሱስ፡ክርስተስን፡ አባት፡ እግዚአ
ብሔርን፡ እናመሰግናለን፡ ሁለግዜ ፡ ስለላንት፡ ስንጸ
ልይ።

፬፤ ከሰማነ፡ጊዜ፡በክርስተስ፡የሱስ፡ ማመናችሁን፡
ቅዱሳንንም፡ ሁሉ፡ መውደዳችሁን።
ኤፌ፡ ፩፤ ፲፭፤ ፲፮።

፭፤ በሰማይ፡ ስለ፡ተዘጋጀላችሁ፡ ስለ፡*ተስፋችሁ፡
ቀድሞ፡ የሰማችሁበት፡ በወንጌል፡ †እውነት፡ ነገር።
*፩፤ ጴጥ፡ ፩፤ ፫፤ ፬። †፪፤ ቆሮ፡ ፮፤ ፯።

፮፤ ወደላንት፡ የደረሰች፡ በዓለሙ፡ ሁሉ፡ ደግሞ፡
እንደለች። እርስዋም፡ ፍሬን፡ የምታፈራ፡ናት፡በላን
ት፡እንደፈራች፡ደግሞ። የእግዚአብሔርን፡ ጸጋ፡በው
ነት፡ ከሰማችሁ፡ ካወቃችሁም፡ቀን፡ ጀምሮ።
ሮሜ፡ ፲፤ ፲፰።

፯፤ እንደ፡ ተማራችሁም፡ ከኤጳፍራ፡ ወደጀችን
ና፡ባልንጀራችን፡ በማገልገል። እርሱ፡የታመነ፡ አገልጋ
ይ፡ በክርስተስ፡ ስለላንት፡ ያለ።
*ም፡ ፬፤ ፲፪።

፰፤ ፍቅራችሁንም፡ በመንፈስ፡ ያስታወቀን።
ም፡ ፪፡ ፩።

፱፤ ስለዚህም፡እኛ፡ *ከሰማነ፡ጀምረን፡ ጸሎት፡ አ
ልተውነም፡ ስለላንት፡ ኢየለመነ፡ የፈቃዱን፡ እውቀ
ት፡ በጥበብ፡ ሁሉ፡ በመንፈሳዊም፡ ማስተዋል፡ ትመ
ሉበት፡ ዘንድ።
*ኤፌ፡ ፩፤ ፲፭፤ ፲፮።

፲፤ ለእግዚአብሔርን፡ የሚገባው፡ *አካሔድ፡ ት
ሔዱ፡ዘንድ፡እንደ፡ፈቃዱ፡ሁሉ፡የመልካሙን፡ ስራ፡
ሁሉ፡ ፍሬ፡አፍርታችሁ፡ እግዚአብሔርንም፡ በማወ
ቅ፡ አድጋችሁ።
*ኤፌ፡ ፬፤ ፩። ፊል፡ ፩፤ ፳፯።

፲፩፤ ከኃይልም፡ሁሉ፡ *በርትታችሁ፡እንደ፡ክብሩ፡
ችሎት፡ለትዕግሥት፡ሁሉ፡ልብንም፡ ለማስፋት፡ በደ
ስታ።
*፩ ቆሮ፡ ፩፤ ፭።

፲፪፤ አብን፡ ስታመሰግኑ፡ ለቅዱሳን፡ ርስት፡ መክፈ
ልት፡ በብርሃን፡ ያበጀነውን።
ኤፌ፡ ፩፡ ፲፩።

፲፫፤ በጨለማ፡ሥልጣን፡ያደነ፡ወደ፡ ወደደውም፡
ወደ፡ልጁ፡መንግሥት፡የወሰደን፡ተከለነ። ም፡ ፪፡ ፲፭።

፲፬፤ በርሱ፡ መድኃኒት፡ የተቀበልነ፡ በደሙ፡ የኃጢ
አትን፡ ይቅርታ።
ኤፌ ፩፤ ፯።

፲፭፤ እርሱም፡ የእግዚአብሔር፡ ምሳሌ፡ የማይታ
ይ፡የፍጥራት፡ ሁሉ፡ መጀመርያ።
ዕብ፡ ፩፤ ፫።

፲፮፤ ነገር፡ሁሉ ፡ በርሱ፡ ተፈጥርዋልና ፡ በሰማያት፡
ያለ፡ሁሉ፡በምድርም፡ያለ።የሚታይ፡የማይታይም፡
መናብርትም፡ አጋእዝትም፡ ሊቃናትም ፡ ሥልጣናት
ም።ሁሉ፡በርሱ፡ለርሱም፡ ተፈጠረ።
ዮሐ፡ ፩፤ ፫፤ ፲።

፲፯፤ እርሱም፡ከሁሉ፡*በፊት፡ ነው። ዓለሙም፡ሁ
ሉ፡ በርሱ፡ ጸና።
*ምሳ፡ ፰፤ ፳፭፤ ፳፮፤ ፳፯።

፲፰፤ እርሱም፡የሥጋው፡ የቤተ፡ክርስቲያን፡*ራስ።
እርሱም፡ መጀመርያ፡ የሙታንም፡ †በኵር። እርሱ፡
በፊት፡ይሆን፡ ዘንድ፡ በሁሉ።
*ኤፌ፡ ፬፤ ፲፭።
†ዮሐ፡ ፳፮፤ ፳፫። ራእ፡ ፩፤ ፭።

፲፱፤ አብ፡ፍጻሜ፡ *ሁሉ፡ በርሱ፡ ያድርበት፡ ዘንድ፡
ወድዋልና።
*ም፡ ፪፤ ፱። ዮሐ፡ ፩፤ ፲፮።

፳፤ በርሱም፡ዓለሙን፡ *ሁሉ፡ለራሱ፡ይቷረቅ፡ዘን
ድ። በመስቀሉ፡ደምም፡ በምድር፡ ያሉን፡ ፍጥረትና፡
በሰማይ፡ ያሉን፡ ፍጥረት፡ አስታረቀ።
*ኤፌ፡ ፩፤ ፲። ፪፤ ፲፬፤ ፲፮። ፩፤ ዮሐ፡ ፪፤ ፪።

፳፩፤ እላንትንም፡ ደግሞ፡በፊት፡ ልዩ፡ የነበራችሁ
ትን፡*ጸላትም፡በስራችሁ፡ ክፋት፡ በሕሊናችሁም፡ዛ
ሬ፡አስታረቃችሁ። ሮሜ፡፭፤ ፲። *ኤፌ፡፪፤፲፪። ፬፤፲፰።

፳፪፤ በሰውነቱ፡ ሥጋ፡ በሞቱ፡ በፊቱ፡ ያቀማችሁ፡
ዘንድ፡ ቅዱሳን፡ አድርጎ፡ ያለ፡ *ነውር፡ ያለ፡ መነቀፍ
ም።
*ኤፌ፡ ፭፤ ፳፯።

፳፫፤ እላንተ፡ ብትጸኑ፡ በሃይማኖታች ፡ *በጽኑም፡
በመሠረታችሁ፡ ኃይል። ከሰማችኋትም፡ ከወንጌል፡
ተስፋ፡ባትናወጡ። †የተሰበከባት፡ ከሰማይ፡ በታች፡
ባለ፡ በዓለሙ፡ ሁሉ። እኔ፡ ጳውሎስ፡ አገልጋይ፡ የሆን
ሁላት።
*፩፤ ቆሮ፡ ፲፭፤ ፶፰። የሐዋ፡ ፬፤ ፲፪።
†ማር፡ ፲፮፤ ፲፭።

፳፬፡ ዛሬ፡ ደስ፡ *ይለኛል፡ በመከራዬ፡ ስለላንት።
የክርስተስንም፡ የመከራውን፡ ጕደይ፡ በሥጋዬ፡ እፈ
ጽማለሁ። ስለ፡ ሥጋው፡ እርሱም፡ ቤተ፡ ክርስቲያን፡
የሚሆን።
*ኤፌ፡ ፫፤ ፲፫። ፩፤ ጴጥ፡ ፩፤ ፲፩።

፳፭፤ ይህች፡እኔ፡አገልጋይ፡ የሆንሁላት፡እንደ፡እግ
ዚአብሔር፡ ሥርዓት፡ለኔ፡ የሰጠው፡ወደላንት፡ የእግ
አብሔርን፡ነገር፡እፈጽም፡ዘንድ።
*ኤፌ፡ ፫፤ ፪፤ ፯።

፳፮፤ ከዓለም፡ ከትውልድም፡ አስቀድሞ ፡ የተሰ
ወረውን፡ምሥጢር።አሁን፡ግን፡ለቅዱሳን፡ተገለጠ።
ሮሜ፡ ፲፮፤ ፳፭።

፳፯፤ እግዚአብሔር፡ የወደደቸው፡ ያስተውቃቸ
ው፡ዘንድ፡ የዚህ፡ ምሥጢር፡ ክብር፡ባለጠግነት፡ምን
ድር፡እንደ፡ ሆነ፡ በአሕዛብ። እርሱም፡ ክርስተስ፡ በላ
ንት፡ የሚሆን፡ *የክብር፡ ተስፋ።
*ኤፌ፡ ፫፤ ፬—፮፤ ፲፯። ሮሜ፡ ፭፤ ፪።

፳፰፥ እርሱ፡ እኛ፡ የምንነግርበት ፡ ሰውን፡ *ሁሉ፡ ኢየገሠጽነ፡ በጥበብም፡ ሁሉ፡ ኢያስተማርነ ። ሰውን፡ ሁሉ፡ ፍጹም፡አድርገን፡እናጸናው፡ ዘንድ፡ በክርስቶስ፡የሱስ። *ቍ፡ ፳፪። ኤፌ፡ ፫፥ ፱። ፬፥ ፲፫። ፭፥ ፳፯።
፳፱፥ በዚህም፡ነገር፡እደክማለሁ፡ ስጋደል፡ እርሱ፡ በኔ፡እንደደረገው፡ ማድረግ፡ በኋይሉ።

## ምዕራፍ፡ ፪፥

፩፥ ታውቁ፡ ዘንድ ፡ እወዳለሁና፡እንዴት፡ ያለ፡ *ገድል፡ ተጋደልሁ፡ ስለላንት፡ በላዶቅያም፡ ስላሉ፡ ሰዎች፡ፊቴንም፡ በሥጋ፡ ስላላዩ፡ ሁሉ። ፊል፡ ፩፥ ፴።

፪፥ ልባቸው፡ይጸና፡ዘንድ፡ወደኝድ፡ምክርም፡ይቀርቡ፡ዘንድ፡በፍቅር።ወደ፡ባለጠግነትም፡ሁሉ፡ጥበብ፡ የመላበት። የእግዚአብሔርን፡ የአብ፡ የክርስቶስንም፡ *ምሥጢር፡ ወደ፡ ማወቅ። ዮሐ፡ ፲፯፥ ፫።
፫፥ በርሱ፡ የጥበብና፡ የውቀት፡ *መዝገብ፡ ሁሉ፡ የተሰወረበት። *፩፥ ቆሮ፡ ፩፥ ፳፬፥ ፴።

፬፥ ይህነንም፡ ማለቴ፡ ማንም ፡ እንዳያጠፋችሁ፡ ነው፡*በሸንገላ፡ ነገር። *ሮሜ፡ ፲፮፥ ፲፰።
፭፥ *በሥጋም፡ከላንት፡ጋራ፡ባልኖር፡ እኔ፡ ግን፡ በመንፈስ፡ ከላንት፡ ጋራ፡ አለሁ። †እጅግም፡ ደስ፡ ይለኛል፡ቅንነታችሁን፡ አይቼ፡ በክርስቶስ፡ ማመናችሁም፡ እንደ፡ጸና። *፩፥ ቆሮ፡ ፭፥ ፫። ፲፬፥ ፵።
፮፥ እንግዴህ፡ ጌታችነን፡ የሱስ፡ ክርስቶስን፡እንደ፡ ተቀበላችሁ፡ በርሱ፡ ሒዱ።
፯፥ ሥርን፡ይዛችሁ፡በርሱም፡ *ተሠርታችሁ፡በሃይማኖታችሁም፡ ጸንታችሁ። እንደ፡ ተማራችሁ፡ በርስዋ፡ ትበዙ፡ ዘንድ፡ †ስታመሰግኑ። ኤፌ፡ ፫፥ ፲፯።
ኤፌ፡ ፪፥ ፳፪። †፩፥ ተሰ፡ ፭፥ ፲፰።

፰፥ ተጠበቁ፡ማንም፡እንዳይማርካችሁ፡በጥበብ፡ በከንቱም፡ ሸንገላ፡እንደ፡ ሰዎች፡ትምህርት፡ በዚህ፡ ዓለም፡ ፍጥረት፡ የሚኖሩ፡እንደ፡ ክርስቶስም፡ ያይደለ። ቍ፡ ፳።
፱፥ በርሱ፡የአምላክነት፡ፍጻሜ፡ሁሉ፡በሥጋው፡አድሮበታልና። ዮሐ፡ ፩፥ ፲፬፥ ፲፮። ፩፥ ጢሞ፡ ፫፥ ፲፮።
፲፥ በርሱም፡የተፈጸማችሁ፡ ናችሁ። እርሱ፡ ያለቆች፡ ሁሉ፡ *አለቃ፡ የሚሆን፡ የሥልጣናትም።
*ኤፌ፡ ፩፥ ፳፩።
፲፩፥ በርሱም፡ደግሞ፡ *የተገዘራችሁ፡በጅ፡ ያልሆነች፡ግዝረት ። ከሥጋ፡ ኋጢአት፡ ሰውነት ፡ በመገፈፍ፡ ነው፡እንጅ፡ በክርስቶስ፡ ግዝረት። ፩፥ ጴጥ፡ ፫፥ ፳፩።
ሮሜ፡ ፪፥ ፳፱።
፲፪፥ ከርሱ፡ ጋራም፡ ተቀበራችሁ፡ በጥምቀት። በርስዋ፡*የተነሣችሁባት፡ደግሞ፡ከርሱ፡ጋራ፡ባመናችሁ፡ ጊዜ፡ከሙታን፡ ባስነሣው፡ በእግዚአብሔር፡ ስራ።
*ሮሜ፡ ፮፥ ፬፥ ፭። ኤፌ፡ ፩፥ ፲፱፥ ፳።
፲፫፥ እላንትንም፡ ሙታችሁ፡ የነበራችሁ፡ በኋጢአት፡በሥጋችሁም፡ ቍላፍነት፡ ከርሱ፡ጋራ፡ *አደናችሁ፡ ኋጢአታችሁን፡ †ሁሉ፡ ይቅር፡ ብሎ።
*ኤፌ፡ ፪፥ ፩፥ ፭፥ ፲፩። †ሉቃ፡ ፯፥ ፵፪።
፲፬፥ በኛ፡ ላይ፡ የተጻፈውን፡ ጽፈት፡ባጠፋ፡ ጊዜ፡ለኛ፡ጸላት፡ የነበረውን፡ *ከመካከላችንም፡ አወጣው፡ በመስቀሉም፡ቸነከረው። *ኤፌ፡ ፪፥ ፲፭።
ኤር፡ ፲፯፥ ፩። ሮሜ፡ ፲፥ ፱።
፲፭፥ አለቆችንም፡ ሥልጣናትንም፡ *በገፈፈ፡ ጊዜ፡ በግልጥ፡ አሳያቸው፡ በርሱም፡ አሳፈራቸው።
*ም፡ ፩፥ ፲፫። ኤፌ፡ ፮፥ ፲፪። ሉቃ፡ ፲፩፥ ፳፪።
፲፮፥ አሁንም፡ ማንም፡ አይፍረድባችሁ፡ በመብልና፡ በመጠጥ። በዓልም፡ በመጠበቅ። ጨረቃንም፡ በመቍጠር። በሰንበትም። *ሮሜ፡ ፲፬፥ ፪፥ ፫።
፲፯፥ ይህችም ፡ *ምሳሌ፡ የምትሆን፡ ለምትመጣው፡ሥጋ፡ግን፡እርሱ፡ ለክርስቶስ፡ነው። *ዕብ፡ ፰፥ ፭።
፲፰፥ *ተጠበቁ፡ማንም፡እንዳያታላችሁ፡ በልብ፡ትሕትና፡ከራሱ፡ፈቃድ፡በመላእክትም፡አምልኮ።ወደዚያ፡ ወደላየው፡ ሲገባ፡ ይታበይማል ፡ በሥጋው፡ ምክር። *ቍ፡ ፳፫። ፊል፡ ፫፥ ፲፬።
፲፱፥ ሥጋም ፡ ሁሉ፡ በሚዋደድበት፡ ራስ፡ አይያዝም፡ በጅማት፡ የሚታሠር፡ በቍራጭም፡ሁሉ፡ ለእግዚአብሔርም ፡ ያድጋል። ኤፌ፡ ፬፥ ፲፭፥ ፲፮።
፳፥ ከክርስቶስ፡ ጋራም፡ የሞታችሁ፡ ከሆናችሁ፡ ከዚህ፡ ዓለም፡ መደብ። ስለ፡ ምን፡ ይህችን፡ ሥርዓት፡ ትቀበልዋታላችሁ፡ በዓለም፡ እንደምትኖሩ።
ገላ፡ ፬፥ ፫፥ ፱።
፳፩፥ አትንካ። አትቅመስ። አትቅረብ።
ዘሌዋ፡ ፭፥ ፪። ፩፥ ጢሞ፡ ፬፥ ፫።
፳፪፥ ይህች፡ ወደ ፡ ጥፋት፡ ታልፋለችና። እርስዋም፡ የሰው፡ ትምህርት፡የሰው፡ *ትእዛዝም፡ናት።
*ኢሳ፡ ፳፱፥ ፲፫። ማቴ፡ ፲፭፥ ፱።
፳፫፥ በርስዋም፡የውቀት፡ ምሳሌ፡ነው፡በገዛ፡ፈቃድ፡ማገልገል፡በትሕትና፡ምሳይ፡ በሥጋም፡ጭንቀት። በከበረች፡ ነገር፡አይደለም፡ ሥጋ፡ይጸግብበት፡ ዘንድ።
፩፥ ጢሞ፡ ፬፥ ፫።

## ምዕራፍ፡ ፫፥

፩፥ እንግዴህ፡ ከክርስቶስ፡ ጋራ፡ *የተነሣችሁ፡ እንደ፡ ሆናችሁ፡ በላይ፡ ያለውን፡እሹ፡ ክርስቶስ፡ በእግዚአብሔር፡ቀኝ፡ ተቀምጦ፡ ወደለበቱ። *ም፡ ፪፥ ፲፪።
ሮሜ፡ ፮፥ ፭።
፪፥ በላይ፡ ያለቸውን፡ *አስቡ፡ በምድርም ፡ ያለቸውን፡ አይደለም። *ማቴ፡ ፮፥ ፫።
ዕብ፡ ፲፪፥ ፳፪። ፲፪፥ ፲፬።
፫፥ ፈጽማችሁ፡ሙታችኋልና፡ ሕይወታችሁም፡ በእግዚአብሔር፡ ተሠውራለች፡ ከክርስቶስ፡ ጋራ።
*ሮሜ፡ ፮፥ ፪። ፊል፡ ፩፥ ፳፩።
፬፥ ሕይወታችንም፡ ክርስቶስ፡በተገለጠ፡ጊዜ፡በዚያን፡ጊዜ፡እላንትም፡ ከርሱ፡ ጋራ፡*በክብር፡ ትገለጣላችሁ። ፩፥ ቆሮ፡ ፲፭፥ ፵፫።

፭፤ *አሁንም፡ በምድር፡ ያሉቾውን፡ ሕዋሳታቸሁን፡ግደሉ፡ †ዝሙት፡ ርኩሰት። ሕማማት፡ ክፉ፡ ፍትወት፡ ብር፡ መውደድ፡እርሱም፡ ጣዖት፡ ማምለክ፡ ነው።
*ሮሜ፡ ፮፡ ፮። ምሳ፡ ፳፡ ፲፫። †ኤፌ፡ ፭፡ ፫።

፮፤ ስለርስዋ፡*የእግዚአብሔር፡ቍጣ፡የሚመጣ፡ በዓመፀኞች፡ ልጆች፡ ላይ።
*ኤፌ፡ ፭፡ ፮።

፯፤ እላንትም፡ደግሞ፡ ቀድሞ፡ *ትሔዱባት፡ የነበራችሁ፡ በርስዋ፡ ስትኖሩ።
*ኤፌ፡ ፪፡ ፩፡—፫።

፰፤ ዛሬ፡ግን፡ ይህነን፡ ሁሉ፡ ደግሞ፡ጣሉት። ቍጣ፡ ጽል፡ ክፋት፡ ስድብ፡ ምናምን፡ ነገርም፡ ካፉቸሁ።
ኤፌ፡ ፬፡ ፳፱፡ ፴፩። ፭፡ ፬።

፱፤ እርሱ፡በርሳቸሁ፡ አሰት፡ አትናገሩ። አሮጌውንም፡ ሰውነት፡ አሰወግዱ፡ ከስራው፡ ጋራ።
ኤፌ፡ ፬፡ ፳፪፡ ፳፭።

፲፤ አዲሱንም፡ሰውነት፡*ልበሱ፡ በውቀት፡ የሚታደስ፡ በሚፈጥረው፡ †ምሳሌ።
*ኤፌ፡ ፬፡ ፳፬። †ዘፍ፡ ፩፡ ፳፯።

፲፩፤ አረሚ ፡ የሌለበት ፡ አይሁደዊም ። ግዙርም፡ ቍላፍም፡ በርበርም፡አጀምም። ባርያም፡ የሰው፡ ልጅም፡ነገር፡ ግን፡ ክርስቶስ፡ሁሉ፡ ነው፡ በሁሉም፡ ነው።
ገላት፡ ፫፡ ፳፰። ሮሜ፡ ፲፡ ፲፪።

፲፪፤ አሁንም፡እግዚአብሔር፡እንደ፡*መረጣቸሁ፡ እላንት፡ ቅዱሳን ፡ የምትሆኑ ፡ የተወደዳቸሁም፡ ምህረትን፡ልበሱ፡ርኅራኄንም፡ቸርነትንም፡ ትሕትናውንም፡ገርነትንም፡ ትዕግሥትንም።
*፩፡ ጴጥ፡ ፪፡ ፱። ኤፌ፡ ፬፡ ፴፪።

፲፫፤ እርሱ፡ በርሳቸሁም፡ ተቻቻሉ፡ እርሱ፡ በርሳቸሁም፡ ይቅር፡ ተባባሉ፡ለማንም፡ መክሰሻ፡ቢኖር፡ በባልንጀራው፡ላይ። ክርስቶስ፡ይቅር፡እንዳላቸሁ፡ እላንትም፡ እንዲህ፡ ይቅር፡በሉ።
ማቴ፡ ፮፡ ፲፬።

፲፬፤ በዚህም፡ ነገር፡ ሁሉ፡ላይ፡ ፍቅርን፡ ልበሱ፡ እርሱ፡ የፍጻሜ፡ማሠርያ፡ ነውና።
ሮሜ፡ ፲፫፡ ፰፡ ፲።

፲፭፤ የእግዚአብሔር፡ *ሳላም ፡ በልባቸሁ፡ ይግዛ። ወደርሱ፡ የተጸራቸሁ፡ናቸሁና፡ባንድ፡ ሥጋ፡የምታመሰግኑም፡ ሁኑ።
*ፊል፡ ፬፡ ፯። ኤፌ፡ ፬፡ ፬።

፲፮፤ የእግዚአብሔር፡ ቃልም፡ በምላት፡ ይደርባቸሁ፡እርሱ፡ በርሳቸሁም፡ በጥበብ፡ ሁሉ፡ አስተምሩ፡ለየባልንጀራቸሁ ፡ ልብም፡ ተናገገሩ። *በመዝሙር፡ በምስጋናም፡በመንፈሳዊት፡ዝማሬም፡ በጸጋ፡ አዝምሩ፡ ለእግዚአብሔር፡ በልባቸሁ።
*ኤፌ፡ ፭፡ ፲፱።

፲፯፤ በቃልም፡በስራም፡የምታደርጉት፡ሁሉ፡በየሱስ፡ክርስቶስ፡በጌታቸን፡ስም፡አድርጉት፡እግዚአብሔርንም፡ አብን፡ በርሱ፡ አመስግኑ።
፩፡ ቆሮ፡ ፲፡ ፴፩። ኤፌ፡ ፭፡ ፳።

፲፰፤ እላንት ፡ ሴቶች፡ ለባሎቻቸሁ፡ ተገዙ፡ በጌታ፡ እንዲገባ።
ኤፌ፡ ፭፡ ፳፪፡—፳፬።

፲፱፤ እላንት፡ወንዶች፡ ሴቶቻቸሁን፡ ውደዱ፡በርሳቸውም፡ አትቈጡ።
፩፡ ጴጥ፡ ፫፡ ፯።

፳፤ እላንት፡ ልጆች፡ ላባቶቻቸሁ፡ታዘዙ፡ በነገሩ፡ ሁሉ፡ይህ፡ እግዚአብሔርን፡ ደስ፡ ያሰኘዋልና።
ኤፌ፡ ፮፡ ፩፡—፱።

፳፩፤ እላንት ፡ አባቶች ፡ ልጆቻቸሁን ፡ አታስመሩ፡ ልባቸው፡ እንዳይዝል፡ እንዳያዝኑ።

፳፪፤ እላንት፡ባሮች፡ለጌቶቻቸሁ፡በሥጋ፡ታዘዙ፡ በሁሉ፡ መታዘዛቸሁም፡በግብዝ፡ አይሁን፡ ለሰዎች፡ደስ፡እንደምታሰኙ። ነገር፡ግን፡ በቅን፡ልቡና፡ እግዚአብሔርንም፡ በመፍራት።
ኤፌ፡ ፮፡ ፭፡—፲።

፳፫፤ ያደረጋቸሁትም፡ሁሉ፡ከለልባቸሁ፡ ይሁን፡ለእግዚአብሔር፡እንዲደረግ፡ ለሰውም፡ አይደለም።

፳፬፤ አውቃቸሁ፡ከእግዚአብሔር፡ዘንድ፡ የርስትን፡ፈንታ፡ እንድትወሰዱ፡ ለጌታ፡ ለክርስቶስ፡ ታገለግላላቸሁና።

፳፭፤ የሚበድልም፡ የበደሉን፡ ብድራት ፡ ይቀበላል፡ በፊቱም፡አድልዎ፡ የለበትም።
ሮሜ፡ ፪፡ ፲፩።

ምዕራፍ፡ ፬፤

፩፤ እላንት፡ *ጌቶች፡ ለባሮቻቸሁ፡ የውነት፡ ፍርድ፡ አድርጉ፡አስተካክልዋቸውም፡ለላንትም፡ደግሞ፡ ጌታ፡ በሰማይ፡ እንዳለ፡ የምታውቁ፡ሁኑ።
*ዘሌዋ፡ ፳፭፡ ፵፫፡ ፶፫። ኤፌ፡ ፮፡ ፱።

፪፤ ጸሎትን፡ *የምታዘወትሩ፡ ሁኑ ፡ በርስዋም፡ ትጉ፡ስታመሰግኑ።
*፩፡ ተሰ፡ ፭፡ ፲፯። ፊል፡ ፬፡ ፮።

፫፤ ለኛም፡ደግሞ፡*ስትጸልዩ፡እግዚአብሔር፡የመናገር፡ †ደጅ፡ ይከፍትልን፡ ዘንድ፡ የክርስቶስን፡ ምሥጢር፡ ልናወጣ፡እኔ፡ ስለርሱ፡ የታሠርሁለት።
*ሮሜ፡ ፲፭፡ ፴። ኤፌ፡ ፮፡ ፲፱። ፪፡ ተሰ፡ ፫፡ ፩።
†፩፡ ቆሮ፡ ፲፮፡ ፱።

፬፤ እገልጠው፡ ዘንድ፡ መናገር፡ እንዲገባኝ።

፭፤ በጥበብ፡ሒዱ፡ በሜደ፡ ሰዎች፡ ዘንድ፡ ዘመኑንም፡ ግዙ።
ኤፌ፡ ፭፡ ፲፭፡ ፲፮። ፩፡ ተሰ፡ ፬፡ ፲፪።

፮፤ ነገራቸሁ፡ ሁለግዜ፡ *በጸጋ፡ ይሁን፡ †በጨው፡ እንዲጣፍጥ ። የሚገባቸሁን፡ ታውቁ፡ ዘንድ፡ ለማንም፡እንደት፡ እንድትመልሱ።
*ኤፌ፡ ፬፡ ፳፱። †ማር፡ ፱፡ ፶።

፯፤ ነገር፡ ግን፡ከኔ፡ዘንድ፡ያለውን፡ጢኪቆስ፡ የተወደደ፡ ወንድም፡ ይነግራቸኋል። የታመነም፡ አገልጋይ፡ ባልንጀራቸንም፡ በጌታ፡ ስራ።

፰፤ ወደላንት፡የላክሁት፡በዚህ፡ስራ። በላንት፡ ያለውን፡ሁሉ፡ያውቅ፡ዘንድ፡ልባቸሁንም፡ ያጽና፡ዘንድ።
ኤፌ፡ ፮፡ ፳፪።

፱፤ ከታመነ፡ከአኔሲሞስ፡ጋራ፡የተወደደም፡ወንድም፡እርሱም፡ከላንት፡አንድ፡የሚሆን። እርሳቸው፡ከዚህ፡ያለውን፡ሁሉ፡ያስታውቅዋቸኋል።*ፊልሞ፡ ፲።

፲፤ *አርስጠርኮስ፡ ከኔ፡ጋራ፡ የተማረከ፡ እንደት፡ ናቸሁ፡ይላቸኋል። ማርቆስም፡የገርናባስ፡የወንድሙ፡ ልጅ። ስለርሱ፡ ያዘዝኋቸሁ። በመጣባቸሁ፡ ጊዜ፡ ተቀበሉት።
*የሐዋ፡ ፲፱፡ ፳፱፡

፲፩፡ የሱስም፡ ዮስጦስ፡ የሚባል። እሌሁ፡ ከግዝረት፡ ወገን፡ የሚሆኑ። እሌህም፡ ብቻቸው፡ የስራ፡ ባልንጀሮቼ፡በእግዚአብሔር፡ መንግሥት፡ ናቸው፡ ያጽኑኝም፡ ነበሩ።

፲፪፡ እንደ፡ት፡ ናችሁ፡ ይላችኋል፡ *ኤጳፍራስ፡ እርሱ፡ ከላንት፡ ወገን፡ የሚሆን፡ የክርስቶስ፡ ባርያ። እርሱም፡ ሁለግዜ፡ ስለላንት፡ በጸሎት፡ ይደክማል፡ ትቆሙ፡ ዘንድ፡ ተፈጽማችሁ፡ እግዚአብሔርን፡ በሁሉ፡ ደስ፡ በማሰኘት። *ም፡ ፩፡ ፯፡፡

፲፫፡ እኔም፡ እመሰክርለታለሁ፡ እጅግ፡ ቅናት፡ እንደ፡ለበት፡ ስለላንት፡ በላዶቅያም፡ ስለሚኖሩ፡ ሰዎች፡ በሔራጶሊስም፡ ስለሚኖሩ።

፲፬፡ እንደ፡ት፡ናችሁ፡ ይላችኋል፡*ሉቃስ፡ ባለ፡ መድኃኒቱ፡ወዳጃችን፡ደማስም። *፪፡ ጢሞ፡ ፬፡ ፲፡ ፲፩፡፡ ፊልሞ፡ ፳፬፡፡

፲፭፡ በላዶቅያ፡ያሉን፡ወንድሞች፡እንደ፡ት፡ናችሁ፡ በሉ፡ኒምፋስንም፡ በቤቱም፡ ያለችውን፡ ቤተ፡ ክርስቲያን።

፲፮፡ ደህችም፡ መልእክት፡ ከላንት፡ ዘንድ፡ በተነበበች፡ጊዜ፡ስደድዋት፡ በላዶቅያ፡ ቤተ፡ ክርስቲያን፡ ትነበብ፡ ዘንድ፡ደግሞ። የላዶቅያንም፡ መልእክት፡እላንት፡ ደግሞ፡ አንብዋት። ፊልሞ፡ ፪፡፡

፲፯፡ አርኪጶስንም፡በሉት። ተጠበቅ፡ከጌታ፡የተቀበልሃትን፡ መልእክት፡ ትፈጽማት፡ ዘንድ።

፲፰፡ ደህን፡ ሰላም፡ እኔ፡ ጳውሎስ፡ በጄ፡ ጻፍሁት። መታሠሬን፡ አስቡ ። ጸጋ፡ ከላንት፡ ጋራ፡ ይሁን ። አሜን። ፩፡ ቆሮ፡ ፲፮፡ ፳፩፡፡ ፪፡ ተሰ፡ ፫፡ ፲፯፡፡

ወደ፡ ቈላሳይስ፡ ሰዎች፡ ተጻፈች፡ ከሮምያ፡ ተላከችም፡ ከጢኪቆስና፡ ከኦኔሲሞስ፡ ጋራ።

# የሐዋርያ ፡ የጳውሎስ ፡ መልእክት ፡ መጀመርያዪቱ ፡ ወደ ፡ ተሰሎንቄ ፡ ሰዎች ።

## ምዕራፍ፡ ፩፡

፩፡ ከጳውሎስ፡*ከስልዋኖስም፡ ከጢሞቴዎስም፡ ወደ፡ ተሰሎንቄ፡ ሰዎች፡ ቤተ፡ ክርስቲያን፡ በእግዚአብሔር፡ አብ፡ የምትሆን፡ በጌታችንም፡ በየሱስ፡ ክርስቶስ። ጸጋ፡ ይድረሳችሁ፡ ሰላምም፡ ከእግዚአብሔር፡ ካባታችን፡ ከጌታችንም፡ ከየሱስ፡ ክርስቶስ። *የሐዋ፡ ፲፯፡ ፲፱፡፡ ፲፰፡ ፩፡ ፲፡፡ ፪፡ ተሰ፡ ፩፡ ፩፡፡

፪፡ እግዚአብሔርን፡ እናመሰግናለን፡ ሁለግዜ፡ በሁላችሁ፡ምክንያት፡እላንተንም፡ በጸሎታችን፡ ማሰብ፡ እናዘወትራለን፡ ሳናስቀር።

፫፡ የሃይማኖታችሁን፡ ስራ፡ *እናስባለንና፡ የፍቅራችሁንም፡ ድካም፡ የተስፋችሁንም፡ ትዕግሥት፡በጌታችን፡ በየሱስ፡ ክርስቶስ፡ በእግዚአብሔር፡ ባባታችን፡ ፊት። *ዮሐ፡ ፮፡ ፳፱፡፡ ፩፡ ቆሮ፡ ፲፫፡ ፲፫፡፡

፬፡ እኛም፡ እናውቃለን፡ እላንት፡ ወንድሞቻችን፡ የእግዚአብሔር፡ ወዳጆች፡ *የተመረጣችሁ፡ እንደ፡ ሆናችሁ። *ቆላ፡ ፫፡ ፲፪፡፡

፭፡ የወንጌል፡ ማስተማራችን፡ በነገር፡ ብቻ፡ አልሆነላችሁምና፡ በኃይል፡ *እንጂ፡ በመንፈስ፡ ቅዱስም። በብዙም፡ ማጽናናት፡ እንድታውቁ፡ እንደ፡ት፡ ነበርነ፡ በላንት፡ ዘንድ፡ ስለላንት። *፩፡ ቆሮ፡ ፪፡ ፬፡፡

፮፡ እላንትም፡ በኛ፡ *ተመስላችሁ፡ በጌታም፡ ነገሪቱን፡ በመቀበላችሁ፡ በጽኑ፡ መከራ፡ በመንፈስ፡ ቅዱስ፡ ደስታ። *፩፡ ቆሮ፡ ፬፡ ፲፮፡፡

፯፡ ምሳሌ፡ ትሆኑ፡ ዘንድ፡ *በመቄዶንያና፡ በአካይያ፡ላሉ፡ ምእምናን፡ ሁሉ። *ም፡ ፬፡ ፲፡፡

፰፡ የጌታ፡ ቃል፡ ከላንት፡ ዘንድ፡ ወጥትዋልና፡ በመቄዶንያና፡በአካይያ፡ብቻ፡አይደለም፡ በሁሉ፡ስፍራ፡ *ሃይማኖታችሁ፡ተሰምትዋል፡እንጂ፡በእግዚአብሔር፡የሚሆን። እኛ፡ በላንት፡ ምንም፡ እንናገር፡ ዘንድ፡ የማያሻን፡ እስኪሆን፡ ድረስ። *ሮሜ፡ ፩፡ ፰፡፡

፱፡ እርሳቸው፡ስለኛ፡ ይናገራሉና፡ ወደላንት፡ መግባታችን፡ እንደ፡ት፡ እንደሆነ። እንደ፡ትስ፡ ከጣዖታት፡ ወደ፡ እግዚአብሔር፡ *ተመለሳችሁ፡ ሕያውን፡ እውነተኛውንም፡ አምላክ፡ ታመልኩ፡ ዘንድ። *፩፡ ቆሮ፡ ፲፪፡ ፪፡፡

፲፡ ልጁንም፡ *ትቈዩ፡ ዘንድ፡ ከሰማያት፡ ከሙታን፡ ያስነሣውን፡ የሱስን፡ ከሚመጣው፡ ቍጣ፡ ያደነን። *የሐዋ፡ ፩፡ ፲፩፡፡ ፊል፡ ፫፡ ፳፡፡ ቲቶ፡ ፪፡ ፲፫፡፡

## ምዕራፍ፡ ፪፡

፩፡ እላንት፡ራሳችሁ፡ ታውቃላችሁና፡ ወንድሞቼ፡ ሆይ፡ ወደላንት፡ *መግባታችን፡ ከንቱ፡ እንዳልሆነ። ም፡ ፩፡ ፭፡ ፱፡፡

፪፡ ነገር፡ ግን፡ አስቀድመን፡ መከራ፡ ከተቀበልነ፡ በኋላ፡*ከተሰደብነም፡በፊልጵስዩስ፡ እላንት፡ እንድታውቁ። በላንትም፡ደግሞ፡ አወራነ፡ ባምላካችን፡ የእግዚአብሔርንም፡ወንጌል፡ በብዙ፡ገድል፡ ነገርናችሁ። *የሐዋ፡ ፲፮፡ ፳፪፡፡ ፍ፡ ፲፯፡ ፭፡፡

፫፡ ማስተማራችን፡ከጥፋት፡ወገን፡ አይደለውምና፡ ከርኵሰትም፡ ከተንኰልም።

፬፡ ነገር፡ ግን፡ ከእግዚአብሔር፡ እንደ፡ ሆነ፡ በማስ

ተማር፡ *እንታመን፡ ዘንድ፡ እንደሁ፡ እንናገራለን፡ ሰውን፡ ደስ፡ እንደሚያሰኙ፡ አይደለም፡ †ልባችነን፡ ለሚመረምር፡ ለእግዚአብሔር፡ ነው፡ እንጂ።

*፩፡ ጢሞ፡ ፩፡ ፲፩፡፡ †ገላት፡ ፩፡ ፲፡፡

፭፡ በተንኰልም፡ከቶ፡ አልተናገርነም፡ እላንት፡እንድታውቁ፡ከብት፡ወደ፡መሻትም፡ልባችን፡አልተመለሰም። ያነንም፡ እግዚአብሔር፡ ይመሰክራል።

፮፡ ከሰውም፡*ብር፡አልሻነም፡ ከላንትም፡ ከሌሎችም፡ምንስ፡ ቢገባ፡†እናከብድ፡ ዘንድ፡ የክርስቶስ፡ መለክተኞች፡ ስለሆነ። *ዮሐ፡ ፭፡ ፵፩፡ ፵፬፡፡

†ዮሐዋ፡ ፰፡ ፴፫፡፡

፯፡ ነገር፡ግን፡በላንት፡ዘንድ፡የተዋረድነ፡ሆነ፡ ልጆችዋን፡ እንድታሳድግ፡ ሞግዚት።

፰፡ እንደሁ፡ ወደላንት፡ እንወደለን፡ እንሰጣችሁም፡ ዘንድ፡እንመኛለን፡ የእግዚአብሔርን፡ ወንጌል፡ብቻ፡አይደለም፡ራሳችነንም፡ እንጂ፡ ደግሞ፡ ለኛ፡ወደጆች፡ ሁናችሁልናልና።

፱፡ ድካማችነን፡ ታስባላችሁና፡ ወንድሞቼ፡ ሆይ፡ *ጣራችነንም። በሌትና፡ በቀን፡ እንሰራ፡ ነበርነና፡ ከላንት፡ባንዷ፡ እንደናከብድ። እንደሁም፡ የእግዚአብሔርን፡ወንጌል፡አስተማርናችሁ። *፩፡ ቆሮ፡ ፬፡ ፲፪፡፡

፲፡ እላንት፡ ትመሰክራላችሁ፡ እግዚአብሔርም፡ ይመሰክራል፡በንጽሕና፡ በጽድቅም፡ያለ፡ *ነውርም፡ እንደ፡ ነበርነ፡ በላንት፡ ባመናችሁ፡ ሁሉ፡ ዘንድ።

*፩፡ ጢሞ፡ ፫፡ ፪፡፡

፲፩፡ እንድታውቁ፡አባት፡ልጁን፡እንዲመክር፡እንደሁ፡ ከላንት፡ ኢያንዳንዱን፡ እንመክር፡ እንደ፡ ነበርነ።

፲፪፡ ልባችሁንም፡እናጸናና፡ነበርነ፡ እንመሰክርም፡ ነበርነ፡ *እንድትሔዱ፡ ለእግዚአብሔር፡ እንዲገባ። ወደ፡ መንግሥቱ፡ ወደ፡ ክብሩም፡ ለጸራችሁ።

*ኤፌ፡ ፬፡ ፩፡፡ ፊል፡ ፩፡ ፳፯፡፡

፲፫፡ ስለዚህም፡ እኛ፡ ደግሞ፡ እግዚአብሔርን፡ እናመሰግናለን፡ ሳናስቀር። ከኛ፡ የሰማችሁትን፡ ነገር፡ እንደ፡ ሰው፡ ነገር፡ አልተቀበላችሁምና፡ ነገር፡ግን፡ እንደ፡እግዚአብሔር፡ነገር፡በውነት፡እንደ፡ሆነ፡በላንት፡ ደግሞ፡*የሚያደርግባችሁ፡ እላንት፡ ያመናችሁ።

*ም፡ ፩፡ ፭፡፡ ገላት፡ ፩፡ ፲፩፡፡

፲፬፡ እላንት፡ በእግዚአብሔር፡ አብያተ፡ ክርስቲያናት፡መስላችኋልና፡ወንድሞች፡ ሆይ፡ በይሁዳ፡ በሚኖሩ፡ በክርስቶስ፡ የሱስ። እላንትንም፡ ደግሞ፡ ያች፡ መከራ፡አግኝታችኋለችና፡ከወገናቻችሁ። እርሳቸውን፡ እንደገኘቻቸው፡ ከአይሁድ።

፲፭፡ እርሳቸው፡ የሱስንም፡*ጌታችነን፡ የገደሉ፡ነቢያትንም፡ እኛንም፡ አሳደዱ፡እግዚአብሔርንም፡ደስ፡ አያሰኙም፡ ሰውንም፡ ሁሉ፡ ይጣላሉ።

*ዮሐዋ፡ ፪፡ ፷፪፡፡ ና፡ ፫፡ ፴፫፡፡

፲፮፡ አሕዛብንም፡ከማስተማር፡ ይከለክሉናል፡እንደይድኑ፡ *ኃጢአታቸውን፡ ይጨርሱ፡ ዘንድ፡ ሁለጊዜ፡ ቍጣ፡ ወርዳባቸዋልና፡ ለፍጻሜው።

*ማቴ፡ ፳፫፡ ፴፪፡ ፴፫፡፡

፲፯፡ እኛ፡ግን፡ ወንድሞቼ፡ ሆይ፡ እላንትን፡ ብናጣችሁ፡ጥቂት፡ጊዜ፡ ፊት፡ ለፊት፡ ነው፡ በልብም፡ አይደለውም፡ እጅግም፡ ጣርነ፡ *ፊታችሁን፡ እናይ፡ ዘንድ፡ በብዙ፡ መናፈቅ። *ሮሜ፡ ፩፡ ፲፩፡፡

፲፰፡ ስለዚህም፡ወደድነ፡ወደላንት፡እንመጣ፡ ዘንድ፡እኔም፡ጳውሎስ፡ አንደግዜ፡ ሁለተግዜም፡ ሰይጣን፡ግን፡ አዘገየኝ።

፲፱፡ ተስፋችንም፡ *ማነው፡ ደስታችንስ፡ የትምክሕታችንስ፡ አክሊል። እላንት፡ አይደላችሁምን፡ በጌታችን፡ በየሱስ፡ ክርስቶስ፡ ፊት፡ በመምጣቱ።

*ፊል፡ ፪፡ ፲፯፡፡ ና፡ ፬፡ ፩፡፡

፳፡ እላንት፡ ክብራችን፡ ደስታችንም፡ ናችሁና።

## ምዕራፍ፡ ፫፡

፩፡ ስለዚህም፡ እንታገሥ፡ ዘንድ፡ ባይቻለነ፡ *በአቴና፡ ብቻችነን፡ እንቀር፡ ዘንድ፡ ወደድነ።

*ዮሐዋ፡ ፲፯፡ ፲፬፡ ፲፭፡፡

፪፡ ወንድማችነንም፡ ጢሞቴዎስን፡ ላክነላችሁ፡ የእግዚአብሔርን፡አገልጋይ፡ በክርስቶስም፡ ወንጌል፡ የሚያግዘነ። ያጸናችሁ፡ዘንድ፡ደስም፡ ያሰኛችሁ፡ ዘንድ፡ በሃይማኔታችሁ።

፫፡ ማንም፡ *እንዳይናወጥ፡ በዚህ፡ መከራ፡ እላንት፡ ታውቃላችሁና፡ እኛ፡ ለዚህ፡ እንደ፡ ተቀመጥነ።

*ኤፌ፡ ፫፡ ፲፫፡፡ ፪፡ ጢሞ፡ ፫፡ ፲፪፡፡

፬፡ ደግሞ፡ከላንት፡ ዘንድ፡ ሳለነ፡ አስቀድመን፡ ነግረናችኋልና፡ መከራ፡ እንቀበል፡ ዘንድ፡ እንዳለነ፡ እንደ፡ሆነ፡ ደግሞ፡ እንደወቃችሁትም።

፭፡ ስለዚህ፡ ደግሞ፡ እኔ፡ ባልታገሥ፡ ሃይማናታችሁን፡አውቅ፡ዘንድ፡ላክሁ፡ፈታኝ፡ የፈተናችሁ፡ እንደ ይሆን፡ *ድካማችንም፡ ከንቱ፡ እንዲይሆን።

*ፊል፡ ፪፡ ፲፯፡፡

፮፡ አሁንም፡ *ጢሞቴዎስ፡ ከላንት፡ ወደኛ፡ በመጣ፡ጊዜ፡በሃይማናታችሁም፡በፍቅራችሁም፡በነገረነ፡ ጊዜ፡ መታሰባችንም፡ በላንት፡ ዘንድ፡ መልካም፡ እንደ ሆነ፡ልታዩነም፡ እንደ፡ ናፈቃችሁ፡ እኛ፡እላንትን፡እንደ፡ ናፈቅነ። *ዮሐዋ፡ ፲፰፡ ፭፡፡

፯፡ ስለዚህ፡ደሳለነ፡ ወንድሞች፡ ሆይ፡በላንት፡ ባዘናችን፡ ሁሉ፡ *በመከራችንም፡ ሁሉ፡ ስለ፡ ሃይማናታችሁ። *ም፡ ፪፡ ፪፡፡

፰፡ አሁን፡ እኛ፡ በሕይወት፡ እንኖራለንና፡ እላንት፡ በእግዚአብሔር፡ ብትቀሙ።

፱፡ ምን፡ያህልስ፡ምስጋና፡ ለእግዚአብሔር፡ እንሰጥ፡ዘንድ፡ይገባናል፡ ስለላንት፡ደስ፡ ባለነ፡ደስታ፡ ሁሉ፡ ስለላንት፡ ባምላካችን፡ ፊት።

፲፡ ሌትና፡ቀን፡ስንለምን፡ በብዙ፡ ልመና፡ ፊታችሁን፡ለማየት፡ከሃይማናታችሁ፡የጐደለውን፡እንሞላ፡ ዘንድ።

፲፩፡ እግዚአብሔርም፡ አባታችን፡ ጌታችንም፡ የሱስ፡ክርስቶስ፡ ወደላንት፡መንገዳችንን፡ ያቅና።

፲፪፡ ለላንትም፡ እግዚአብሕር፡ ፍቅር፡ ይጨምር፡ ያብዛላችሁም፡ እርስ፡ በርሳችሁ፡ ለሁሉም። እኛ፡ደግሞ፡ እላንተን፡ እንድንወዳችሁ።

፲፫፡ *ልባችሁን፡ ያጽና፡ ዘንድ፡ ያለ፡ †ነውር፡ በቅድስና፡ባባታችን፡ በእግዚአብሔር፡ ፊት፡ የሱስ፡ ክርስቶስ፡ በመጣ፡ ጊዜ፡ ከቅዱሳኑ፡ ሁሉ፡ ጋራ፡

*፪፡ ተሰ፡ ፪፡፲፯። †ፊል፡ ፩፡ ፲።

## ምዕራፍ፡ ፬፡

፩፡ በቀረውም፡ ወንድሞች፡ ሆይ፡ *እንለምናችኋለን፡ በጌታ፡ በየሱስም፡ እንመክራችኋለን፡ ከኛ፡ እንደ፡ተቀበላችሁ፡እንዴት፡እንዲገባ፡ †ትሔዱ፡ ዘንድ፡ እግዚአብሔርንም፡ ደስ፡ታሰኙ፡ ዘንድ፡ በዚያው፡ እንድትበዙ። *፪፡ ተሰ፡ ፫፡ ፲፪። †ኤፌ፡ ፬፡ ፩።

፪፡ በጌታ፡ በየሱስ፡ የሰጠናችኋቸውን፡ ትእዛዛት፡ ታውቃላችሁና።

፫፡ ይህ፡የእግዚአብሔር፡ፈቃድ፡ ነውና፡እርሱም፡ መቀደሳችሁ፡ ከዝሙት፡ ትርቁ፡ ዘንድ።

፬፡ ሁሉም፡ ኢያንዳንዳችሁ፡ *እቃውን፡ በመቀደስና፡ በክብር፡ይገዛ፡ ዘንድ፡ሊያወቅ።

*፩፡ ቆር፡ ፮፡ ፲፫፡ ፲፭፡

፭፡ *በዝሙት፡ሕማምም፡አይደለም፡እግዚአብሔርን፡ እንደማያውቁ፡ እንደ፡ አሕዛብ።

*ቆላ፡ ፫፡ ፭።

፮፡ ማንም፡ ወንድሙን፡ እንዳያታልው፡ ባንዳችም፡ግፍ፡ እንዳያደርግበት፡ እግዚአብሔር፡ በዚህ፡ ነገር፡ሁሉ፡ ይበቀላልና። ቀድሞ፡ እንደ፡ ነገርናችሁ፡ እንደ፡ መሰከርነም።

፯፡ እግዚአብሔር፡ ለርኩሰት፡ አልጸራነምና፡ *ለቅድስና፡እንጂ። *፪፡ ጢሞ፡ ፩፡ ፱።

፰፡ ስለዚህም፡ የሚጥል፡*ሰውን፡ የጣለ፡ አይደለም፡እግዚአብሔርን፡እንጂ፡ቅዱስ፡ መንፈሱን፡ ለላንት፡የሰጠውን። *ሉቃ፡ ፲፡ ፲፮።

፱፡ ወንድሞችን፡ ስለ፡ መውደድ፡ ግን፡ እጽፍላችሁ፡ ዘንድ፡ የምትሹ፡ አይደላችሁም፡ ከእግዚአብሔር፡ ተምራችኋልና፡ *እርስ፡ በርሳችሁ፡ ትዋደዱ፡ ዘንድ። ማር፡ ፲፪፡ ፴፩፡ ኤር፡ ፴፩፡ ፴፫፡ ፴፬።

፲፡ እንዲሁም፡ታደርጋላችሁ፡ *በመቄዶንያ፡ ባሉ፡ ወንድሞች፡ ሁሉ። እኛ፡ ግን፡ እንለምናችኋለን፡ ወንድሞቼ፡ ሆይ፡ በዚያው፡ †እጅግ፡ ትበዙ፡ ዘንድ።

*ም፡ ፩፡ ፯። †ም፡ ፬፡ ፩።

፲፩፡ *ትጥሩም፡ ዘንድ፡ በጸጥታ፡ ለመኖር፡ ስራችሁንም፡ ለመስራት፡ †በጃችሁ፡ ስትደክሙ፡ እንዳዘዝናችሁ። *፪፡ ተሰ፡ ፫፡ ፰፡ ፲፪። †ም፡ ፪፡ ፱።

፲፪፡ ትሔዱ፡ ዘንድ፡ ለመሔድ፡ *እንዲገባችሁ፡ በዉጪ፡ ሰዎች፡ ዘንድ፡ ከማንም፡ እንዳትሹ።

*ሮሜ፡ ፲፫፡ ፲፫።

፲፫፡ ነገር፡ግን፡ታውቁ፡ ዘንድ፡እወዳለሁ፡ ወንድሞቼ፡ሆይ፡ *ስላንቀላፉ፡ ሰዎች፡ እንዳታዝኑ፡ እንደ፡ ሌሎች፡†ተስፋ፡ እንደ፡ ሌላቸው። *፩፡ ቆር፡ ፲፭፡ ፳። †ኤፌ፡ ፪፡ ፲፪።

፲፬፡ የሱስ፡*ሙቶ፡ እንደ፡ ተነሣ፡ካመንን፡ እንዲሁም፡ በየሱስ፡ ያንቀላፉትን፡ እግዚአብሔር፡ ከርሱ፡ ጋራ፡ ያመጣቸዋልና። *ሮሜ፡ ፲፬፡ ፱።

፩፡ ቆር፡ ፲፭፡ ፫፡ ፬።

፲፭፡ በጌታ፡ ነገር፡ የምንላችሁ፡ ይህ፡ ነውና። እኛ፡ ሕያዋን፡ሁነን፡የምንቀር፡ጌታ፡ በመጣ፡ ጊዜ፡ ያንቀላፉትን፡ *እንደንቀድም። *፩፡ ቆር፡ ፲፭። ፳፫፡ ፶፩።

፲፮፡ እርሱ፡ ጌታ፡በእልልታ፡ በመላእክትም፡ አለቃ፡ድምጽ፡በእግዚአብሔርም፡ መለከት፡ ከሰማይ፡ ይወርዳል፡በክርስቶስም፡ የሞቱ፡ አስቀድመው፡ ይነሣሉ። ፩፡ ቆር፡ ፲፭፡ ፳፫፡ ፶፪።

፲፯፡ ከዚያም፡ በኋላ፡ እኛ፡ ሕያዋን፡ ሁነን፡ የቀረነው፡ ባንድ፡ *እንነጠቃለን፡ ከርሳቸው፡ ጋራ፡ በደመና፡ ጌታን፡ ለመቀበል፡ በአየር፡ እንዲሁም፡ ሁልጊዜ፡ †ከጌታ፡ጋራ፡ እንሆናለን። *ራእ፡ ፲፩፡ ፲፪።

†ዮሐ፡ ፲፪፡ ፳፮። ና፡ ፲፯፡ ፳፬።

፲፰፡ ስለዚህም፡ተጽናኑ፡እርስ፡ በርሳችሁ፡ በዚህ፡ ቃል።

## ምዕራፍ፡ ፭፡

፩፡ ስለ፡*ጊዜው፡ ግን፡ ስለ፡ ዘመኑም፡ ወንድሞቼ፡ ሆይ፡ የምትሹ፡ አይደላችሁም፡ እንጽፍላችሁ፡ ዘንድ። *ማቴ፡ ፳፬፡ ፴፮።

፪፡ እላንት፡ ፈጽማችሁ፡ ታውቃላችሁና፡ የጌታ፡ ቀን፡ እንዲመጣ፡ በሌት፡ እንዲገባ፡ *ሌባ።

*ማቴ፡ ፳፬፡ ፵፪፡—፵፬። ፪፡ ጴጥ፡ ፫፡ ፲።

ራእ፡ ፫፡ ፫። ና፡ ፲፮፡ ፲፭።

፫፡ በደህንነትም፡ *በጽናትም፡ አለነ፡ ባሉ፡ ጊዜ፡ የዚያን፡ ጊዜ፡ ጥፋት፡ በድንገት፡ ይደዛቸዋል፡ ምጥ፡ እርጉዝን፡ እንዲይዛት፡ አያመልጡምም።

*ኤር፡ ፮፡ ፲፬። ና፡ ፰፡ ፲፩።

፬፡ እላንት፡ግን፡ ወንድሞቼ፡ ሆይ፡ በጨለማ፡ አይደላችሁም፡ ያ፡ቀን፡ እላንተን፡ያገኛችሁ፡ ዘንድ፡ እንደ፡ሌባ። ኤፌ፡ ፭፡ ፰።

፭፡ እላንት፡ ሁላችሁ፡ *የብርሃን፡ ልጆች፡ ናችሁ፡ የቀንም፡ልጆች፡ናችሁ። የሌትና፡የጨለማ፡ ልጆች፡ አይደለነም። *ሮሜ፡ ፲፫፡ ፲፪። ኤፌ፡ ፭፡ ፱።

፮፡ አሁንም፡እንተኛ፡እንደ፡ ሌሎች፡ እንንቃ፡ እንትጋም፡እንጂ።

፯፡ የሚተኙ፡ በሌት፡ ይተኛሉና፡ የሚሰክሩም፡ በሌት፡ ይሰክራሉና።

፰፡ እኛ፡ ግን፡ *የቀን፡ ልጆች፡ ከሆነ፡ እንንቃ፡ የሃይማኖትና፡የፍቅር፡ †ጥሩር፡ ለብሰን፡ የደህንነትንም፡ ተስፋ፡ራስ፡ቁር። *ሮሜ፡ ፲፫፡ ፲፪። †ኢሳ፡ ፶፱፡ ፲፯።

ኤፌ፡ ፮፡ ፲፬፡ ፲፯።

፱፤ እግዚአብሔር፡ ለቍጣ፡ አላደረገነም፡ ለሕይወትና፡ ለደህንነት፡ እንጂ፡ ስለ፡ ጌታችን፡ ስለ፡ የሱስ፡ ክርስቶስ።

፲፤ በኛ፡ምክንያት፡ስለ፡ሞተው፡*ብንተጋ፡ብናንቀላፋም፡ †ከርሱ፡ጋራ፡ እንኖር፡ ዘንድ።

*ሮሜ፡ ፲፬፤ ፰፤ ፱። †ም፡ ፬፤ ፲፬።

፲፩፤ ስለዚህም፡ እርስ፡ በርሳችሁ፡ ተጽናኑ፡ ሁሉም፡ ኢያንዳንዱ፡ ባልንጀራውን፡ ይሰራ፡ እንድታደርጉ፡ደግሞ።
ዕብ፡ ፲፤ ፳፬፤ ፳፭።

፲፪፤ እንለምናችኋለን፡ግን፡ ወንድሞቼ፡ ሆይ፡ በላንት፡ *የሚደክሙትን፡ ታውቁ፡ ዘንድ፡ የሚቀሙላችሁንም፡ በጌታ፡ የሚያስተምርዋችሁንም።

*፩ ቆሮ፡ ፲፮፤ ፲፰።

፲፫፤ እጅግ፡ በብዙ፡ ፍቅርም፡ እንድታኖርዋቸው፡ ስለ፡ ስራቸው። እርሱ፡ በርሳችሁ፡ በሰላም፡ ሁኑ።

፲፬፤ እንለምናችሁማለን፡ እላንት፡ *ወንድሞች፡ ለሥርዓት፡ የማይገዙትን፡ ትቀጡ፡ ዘንድ፡ አፈራሞችንም፡ታጽኑ፡ዘንድ፡ደካሞችንም፡አቀናኑ፡በሰውም፡ ሁሉ፡ ታገሡ።
*፪ ተሰ፡ ፫፤ ፲፭።

፲፭፤ ተጠንቀቁ፡ ከላንት፡ *ማንም፡ ክፉን፡ በክፉ፡ እንዳይመልስ። መልካም፡ እኹ፡ እንጂ፡ ሁለጊዜ፡ እርሱ፡ በርሳችሁ፡ ለሁሉም።
*ምሳ፡ ፳፤ ፳፪።

ሮሜ፡ ፲፪፤ ፲፯። ፩ ጴጥ፡ ፫፤ ፱።

፲፮፤ ሁለጊዜ፡ ደስ፡ ይበላችሁ።
ሉቃ፡ ፲፤ ፳።

፲፯፤ ጸልዩ፡ሳታክቱ።
ሉቃ፡ ፲፰፤ ፩። ሮሜ፡ ፲፪፤ ፲፪።

ቆላ፡ ፬፤ ፪።

፲፰፤ እግዚአብሔርን፡*አመስግኑ፡በስራው፡ሁሉ። ይህ፡የእግዚአብሔር፡ፈቃድ፡ነውና፡ በክርስቶስ፡ የሱስ፡ስለላንት። *ኤፌ፡ ፭፤ ፳። ቆላ፡ ፪፤ ፯። ና፡ ፫፤ ፲፭።

፲፱፤ መንፈስን፡ አታጥፉ።
፩ ቆሮ ፲፬፤ ፴፤ ፴፪።

፳፤ ትንቢትን፡ አትናቁ።
፩ ቆሮ፡ ፲፬፤ ፩።

፳፩፤ ሁሉን፡ ፈትኑ፡ በመልካሙም፡ ተያዙ።

ሮሜ፡ ፪፤ ፲፰። ፩ ዮሐ፡ ፬፤ ፩።

፳፪፤ ክፉ፡ከሚመስል፡ ሁሉ፡ ሽሹ።

፳፫፤ *እግዚአብሔርም፡ራሱ፡ የሰላም፡ አምላክ፡ ሁላችሁን፡ ፈጽሞ፡ ይቀድሳችሁ። መንፈሳችሁም፡ ነፍሳችሁም፡ ሥጋችሁም፡ ሁለንትናው፡ ያለ፡ ነውር፡ ይጠበቅ፡ጌታችን፡ የሱስ፡ ክርስቶስ፡ በመጣ፡ጊዜ።

ሮሜ፡ ፲፭፤ ፴፫።

፳፬፤ እርሱም፡የጸራችሁ፡*እውነተኛ፡ነው፡እርሱም፡ይህነን፡ያደርገዋል።
*፩ ቆሮ፡ ፩፤ ፱። ና፡ ፲፤ ፲፫።

፪ ተሰ፡ ፫፤ ፫። ፪ ጢሞ፡ ፪፤ ፲፫።

፳፭፤ እላንት፡ ወንድሞች፡ ስለኛ፡ ጸልዩ።

ቆላ፡ ፬፤ ፫።

፳፮፤ ወንድሞችን፡ሁሉ፡እንዲት፡ ናችሁ፡በሉ፡በተቀደሰች፡መሳም።
ሮሜ፡ ፲፮፤ ፲፮።

፳፯፤ በእግዚአብሔር፡ አምያችኋለሁ፡ ይህች፡መልእክት፡ለቅዱሳን፡ወንድሞች፡ሁሉ፡ትነበብ፡ዘንድ።

፳፰፤ የጌታችን፡የየሱስ፡ ክርስቶስ፡ ጸጋ፡ከላንት፡ ጋራ፡ይሁን።አሜን። ሮሜ፡ ፲፮፤ ፳፤ ፳፬። ፊል፡ ፬፤ ፳፫።

መጀመርያይቱ፡ መልእክት፡ ወደ፡ ተሰሎንቄ፡ ሰዎች፡ በአቴና፡ አገር፡ ተጻፈች።

---

# የሐዋርያ ፡ የጳውሎስ ፡ መልእክት ፡ ሁለተኛይቱ ፡ ወደ ፡ ተሰሎንቄ ፡ ሰዎች ።

## ምዕራፍ፡ ፩፤

፩፡ ከጳውሎስ፡ ከሰልዋኖስም፡ ከጢሞቴዎስም። ወደ፡ተሰሎንቄ፡ሰዎች፡ቤተ፡ክርስቲያን፡በእግዚአብሔር፡ ባባታችን፡ በጌታችንም፡ በየሱስ፡ ክርስቶስ።

፪፤ *ጸጋ፡ይሁንላችሁ፡ሰላምም፡ከእግዚአብሔር፡ ካባታችን፡ ከጌታም፡ ከየሱስ፡ክርስቶስ።

*፩ ቆሮ፡ ፩፤ ፫። ቆላ፡ ፩፤ ፪።

፫፤ እግዚአብሔርን፡ሁለጊዜ፡ ስለላንት፡ እናመሰግን፡ ዘንድ፡ ይገባናል፡ ወንድሞቼ፡ ሆይ፡ አገቡብ፡ እንደሆነ፡ ሃይማኖታችሁ፡ እጅግ፡ ያድጋልና፡ ፍቅራችሁም፡ የሁላችሁ፡ ይበዛልና፡ ሁሉ፡ ኢያንዳንዱ፡ ለባልንጀራው።
ም፡ ፪፤ ፲፫። ፩ ተሰ፡ ፩፤ ፪።

፬፤ እኛ፡ ደግሞ፡ እንመካባችሁ፡ ዘንድ፡ በእግዚአብሔር፡አብያተ፡ ክርስቲያናት፡ በትዕግሥታችሁ፡ በሃይማኖታችሁም፡በገድላችሁ፡ሁሉ፡ በመከራችሁም፡ ሁሉ፡በምትቀበሉት።
፪ ቆሮ፡ ፯፤ ፲፬።

፭፤ እውነተኛው፡*የእግዚአብሔር፡ፍርድ፡በዚህ፡ ይገለጣልና፡የእግዚአብሔርን፡መንግሥት፡ትወርሱ፡ ዘንድ፡*እንዲገባችሁ፡ ስለርሱም፡ ብላችሁ፡ የምትደክሙ።
*ፊል፡ ፩፤ ፳፰። †ሉቃ፡ ፳፩፤ ፴፮።

፮፡ በእግዚአብሔር፡ ዘንድ፡ጽድቅ፡ነውና፡ዛሬ፡ የሚያስጨንቋችሁን፡ ጭንቀት፡ ይመልስላቸው፡ ዘንድ።
ራእ፡ ፲፭፤ ፮፤ ፯።

፯፤ ለላንትም፡ዛሬ፡ጭንቀት፡ ለምታዩት፡ዕረፍት፡ ይሰጣችኋል፡ከኛ፡ጋራ፡ የሱስ፡ጌታ፡ ከሰማይ፡ በተገለጠ፡ጊዜ፡ከኃይሉ፡*መላእክት፡ጋራ። *ማቴ፡ ፳፭፤ ፴፩።

፰፤ በሚቃጠል፡ እሳት፡ ተበቅሎ፡አምላክን፡ ከማያውቁ፡ለጌታችንም፡ ለየሱስ፡ ክርስቶስ፡ ወንጌል፡ ከማይታዘዙ።
ሮሜ፡ ፪፤ ፰።

፱፡ እለዚህም፡የዘላለም፡ ጥፋትን፡ ፍርድ፡ ይወስ
ዷሉ፡ከጌታ፡ፊት፡ከኃይሉም፡ክብር። ኢሳ፡ ፪፡ ፲፡፲፱።
፲፡ በቅዱሳኑ፡ሊመሰገን፡በመጣ፡ጊዜ፡ በሚያምኑ
በትም፡ሁሉ፡ይከብር፡ ዘንድ፡ በዚያ፡ቀን። ለላንተ፡ የ
መሰከርነውን፡ምስክር፡አምናችኋልና። ቈላ፡ ፫፡ ፬።
፲፩፡ ስለዚህም፡ሁለግዜ፡ ስለላንተ፡ እንጸልያለን፡
አምላካችን፡ ያደርጋችሁ፡ ዘንድ፡ ለመጽራቱ፡ እንዲ
ገባችሁ፡ እንደ፡ ፈቃዱም፡ መልካሙን፡ ሁሉ፡ ይፈጽ
ምባችሁ፡ ዘንድ፡ የሃይማኖትንም፡ ስራ፡ በኃይል።
፩፡ ተሰ፡ ፩፡ ፪።
፲፪፡ የየሱስ፡ክርስቶስ፡የጌታችን፡ስም፡ በላንት፡ ይ
መሰገን፡ዘንድ፡እላንትም፡በርሱ፡እንደ፡ ጌታችን፡እን
ደምላካችንም፡ እንደ፡ የሱስ፡ ክርስቶስ፡ ጸጋ።

## ምዕራፍ፡ ፪፡

፩፡ እኛ፡ግን፡እንለምናችኋለን፡ እላንት፡ወንድሞ
ች፡ስለ፡ ጌታችን፡ ስለ፡ የሱስ፡ክርስቶስ፡ መገለጥ፡ ወደ
ርሱም፡ስለ፡ መከማቻችን።
፪፡እንደትቸኩሉ፡በልቡናችሁም፡እንደትናወጡ፡
እንደትደነግጡም፡ በመንፈስም፡ ቢሆን፡ በነገርም፡
ቢሆን፡በመልእክትም፡ ከኛ፡ እንደ፡ ሆነች። የክርስቶ
ስ፡ ቀን፡ እንደ፡ ደረሰ፡ አሰባችሁ።
፫፡ *ማንም፡አያስታችሁ፡ በማናቸውም። ያ፡ ቀን፡
አይደርስምና፡ አስቀድሞ፡ ክሕደት፡ሳትመጣ፡ †የኃ
ጢአትም፡ ሰው፡ ሳይገለጥ፡ የጥፋት፡ልጅ።
*፩፡ ጢሞ፡ ፬፡ ፩። †፩፡ ዮሐ፡ ፪፡ ፲፰። ና፡ ፬፡ ፫።
፬፡ የሚቋቋም፡ ራሱንም፡ የሚያልቅ፡ አምላክ፡
ወይም፡መቅደስ፡በሚባል፡ሁሉ፡ላይ፡በእግዚአብሔ
ር፡መቅደስ፡እንደምላክ፡ እስኪቀመጥ፡ ድረስ፡ ራሱ
ንም፡የሚያሳይ፡አምላክ፡እንደሆነ። ዳን፡ ፲፩፡ ፴፯።
፭፡ አላሰባችሁምን፡ ይህነን፡ እንደ፡ ነገርኋችሁ፡ ከ
ላንት፡ዘንድ፡ሳለሁ።
፮፡ አሁንም፡ታውቃላችሁ፡የሚከለክለው፡ምን፡
እንደ፡ሆነ፡በጊዜው፡ እስኪገለጥ፡ድረስ።
፯፡ የኃጢአት፡ ምሥጢር፡ዛሬ፡ *ተጀምርዋልና፡ያ
ደርግ፡ዘንድ፡ብቻ፡የሚያቀመው፡ ከመካከል፡እስኪ
ሻር፡ ድረስ። *የሐዋ፡ ፳፡ ፳፱።
፰፡ የዚያን፡ ጊዜ፡ ያክፋ፡ ይገለጣል፡ ጌታችን፡ ባፉ፡
መንፈስ፡ የሚያጠፋው፡ በመምጣቱም፡ መገለጥ፡
ከንቱ፡ያደርገዋል። ኢሳ፡ ፲፩፡ ፬። ራእ፡ ፲፱፡ ፲፭፡ ፳።
፱፡ የዚያ፡ መምጣቱ፡ በሰይጣን፡ ስራ፡ ነው፡ በኃይ
ል፡ ሁሉ፡ በምልክትም፡ ባሰትም፡ ተአምራት።
ማቴ፡ ፳፬፡ ፳፬።
፲፡ በምታጠፋም፡በኃጢአት፡ስሕተት፡ሁሉ፡በሚ
ጠፉ፡ሰዎች።የውነትን፡ፍቅር፡ስላልተቀበሉ፡ይድኑበ
ት፡ዘንድ። ፪፡ ቆሮ፡ ፪፡ ፲፭። ና፡ ፬፡ ፫።
፲፩፡ ስለዚህም፡እግዚአብሔር፡የስሕተት፡መንፈ
ስ፡ ይሰድላቸዋል፡ ባሰት፡ ያምኑ፡ ዘንድ።
ሮሜ፡ ፩፡ ፳፬።
፲፪፡ ይኰነንባቸው፡ ዘንድ፡ *በውነት፡ በማያምኑ፡
ሁሉ፡ ነገር፡ግን፡ ኃጢአትን፡ ወደዱ።
*ሕዝ፡ ፳፡ ፳፬፡ ፳፭።
፲፫፡ እኛ፡ግን፡ይገባናል፡ እግዚአብሔርን፡ ሁለግዜ፡
*እናመሰግን፡ዘንድ፡ስለላንት፡ ወንድሞቼ፡ሆይ፡ከእ
ግዚአብሔር፡ የተወደዳችሁ። እግዚአብሔር፡ ከጥን
ቱ፡ለደህንነት፡ †እንደመረጻችሁ፡ በመንፈስ፡ቅዱስ፡
ቅድስና፡ እውነትንም፡ በማመን። *ም፡ ፩፡ ፫፡ ፬።
†ኤፌ፡ ፩፡ ፬።
፲፬፡ ወደዚህም፡ ጸራችሁ፡ በማስተማራችን፡ የጌ
ታችነን፡ የየሱስ፡ክርስቶስ፡ክብር፡ ትወርሱ፡ ዘንድ።
፲፭፡ አሁንም፡ ወንድሞቼ፡ ሆይ፡ጽኑ፡ የተማራች
ኋትንም፡ ትምህርት፡ በነገር፡ቢሆን፡ በመልእክታችን
ም፡ቢሆን፡ያዙ። ም፡ ፫፡ ፯።
፲፮፡ ራሱም፡ ጌታችን፡ የሱስ፡ ክርስቶስ፡ እግዚአብ
ሔርም፡ አባታችን፡ የወደደነ፡ የዘላለምም፡ ደስታ፡ የ
ሰጠነ፡ መልካምም፡ ተስፋ፡ በጸጋው።
፲፯፡ እርሱ፡ ልባችሁን፡ደስ፡ ያሰኝ፡ ያጽናም፡ መል
ካም፡በማድረግ፡ በመልካምም፡ ነገር፡ ሁሉ።
፩፡ ተሰ፡ ፫፡ ፲፫።

## ምዕራፍ፡ ፫፡

፩፡ አሁንም፡ ወንድሞቼ፡ ሆይ፡ ስለኛ፡ *ጸልዩ፡ የጌ
ታ፡ነገር፡እንዲዘረጋና፡እንዲመሰገን፡በላንት፡ ዘንድ፡
ደግሞ፡ እንደ፡ ተመሰገነ። *ቈላ፡ ፬፡ ፫።
፪፡ አእምሮ፡ከሌላቸውና፡ ከክፎች፡ ሰዎች፡እንድ
ን፡ ዘንድ። ሃይማኖት፡ ለሁሉ፡ አይደለችምና።
፫፡ እግዚአብሔር፡ ግን፡ እውነተኛ፡ ነው፡ የሚያጸ
ናችሁ፡ ከክፉም፡ የሚጠብቃችሁ። ፩፡ ቆሮ፡ ፩፡ ፱።
ና፡ ፲፡ ፲፫።
፬፡ ልባችንም፡ *አምንዋችኋል፡ በጌታ፡ ያዘዝናች
ሁን፡ አድርጋችኋልና፡ ደግሞም፡ ታደርጋላችሁ።
*፪፡ ቆሮ፡ ፯፡ ፲፮። ገላት፡ ፭፡ ፲።
፭፡ ጌታም፡ልባችሁን፡ ያቅናው፡ ለእግዚአብሔር፡
ፍቅር፡ ለክርስቶስም፡ ትዕግሥት።
፮፡ እናዛችኋለን፡ ግን፡ እላንት፡ወንድሞች፡ በጌታ
ችን፡በየሱስ፡ክርስቶስ፡ስም፡ *እንድትለዩ፡ ያለ፡ ሥር
ዓት፡ከሚሔድ፡ ወንድም፡ ሁሉ፡ እኛም፡ በሰጠነው፡
ትምህርት፡ አይደለም። *ማቴ፡ ፲፰፡ ፲፯።
ሮሜ፡ ፲፮፡ ፲፯። ቲጦ፡ ፫፡ ፲።
፯፡ እላንት፡ ታውቃላችሁና፡እንዴት፡ እንዲገባች
ሁ፡እኛን፡ትመስሉ፡ ዘንድ፡በላንት፡ መካከል፡ ትምህ
ርት፡የሚጣላ፡ነገር፡አላደረግነምና። ፩፡ ቆሮ፡ ፬፡ ፲፮።
፩፡ ተሰ፡ ፩፡ ፮።
፰፡ ከላንትም፡ካንዳችሁ፡በከንቱ፡ እንጀራ፡ አልበ
ላነም፡እንሰራ፡ነበርነ፡እንጂ፡ *በድካምና፡ በኃዘን፡ ሌ
ትና፡ ቀን፡ ከላንት፡ በማንም፡ እንዳናከብድ።
፩፡ ቆሮ፡ ፬፡ ፲፪።
፱፡ ለኛ፡ *የማይገባነ፡ ሆኖ፡ አይደለም። ነገር፡ ግን፡

ተምሳሌ፡እንሰጣችሁ፡ ዘንድ፡ ነው፡እኛን፡ ትመስሉ፡ ዘንድ። *ማቴ፡ ፲፡ ፲፡፡ †፩፡ ቆሮ፡ ፱፡ ፲፬፡፡

፲፡ ደግሞ፡ በላንት፡ ዘንድ፡ ሳለነ፡በዚህ፡ እናዛችሁ፡ ነበርነና። ስራ፡ መስራት፡ የማይወድ፡ አይብላ። ዘፍ፡ ፫፡ ፲፱፡፡

፲፩፡ እኛም፡ ሰምተናል፡ ከላንት፡ ሰዎች፡ እንደሉ፡ ያለ፡ ሥርዓት፡ የሚሔዱ፡ እንደችም፡ አያደርጉም፡ ከዙረት፡በቀር።

፲፪፡ እኛም፡እንደለዚህ፡ያሉትን፡ እናዛለን፡በጌታ ም፡ በየሱስ፡ ክርስቶስ፡ እንለምናቸዋለን፡ *በጸጥታ፡ ይሰሩ፡ ዘንድ፡እንጀራቸውንም፡ ይበሉ፡ ዘንድ። *፩፡ ተሰ፡ ፬፡ ፲፩፡፡

፲፫፡ እላንት፡ግን፡ ወንድሞቼ፡ ሆይ፡ መልካም፡ ማ ድረግ፡ አተው። ገላት፡ ፮፡ ፱፡፡

፲፬፡ ከላንትም፡አንድ፡ ሰው፡ ቢኖር፡በዚህ፡መልእ ክት፡ለጻፍነው፡ ነገር፡ የማይታዘዝ፡ከርሱ፡ራቁ፡ *አት ገናኙትም፡ ያፍር፡ ዘንድ። *ማቴ፡ ፲፰፡ ፲፯፡፡ ፩፡ ቆሮ፡ ፭፡ ፱፡ ፲፩፡፡

፲፭፡ ነገር፡ግን፡እንደ፡ ጸላት፡አትዩት፡ እንደ፡ ወንድ ም፡ገሥጹት፡እንጂ። ማቴ፡ ፲፰፡ ፲፭፡፡

፲፮፡ የሰላም፡ጌታም፡ሰላም፡ ይስጣችሁ፡ ሁለግዜ፡ በነገሩ፡ ሁሉ። እግዚአብሔር፡ ከላንት፡ ከሁላችሁ፡ ጋ ራ፡ይሁን። ሮሜ፡ ፲፭፡ ፴፫፡፡ ና፡ ፲፮፡ ፳፡፡

፲፯፡ ይህ፡ ሰላም፡እኔ፡ ጳውሎስ፡ በጄ፡ነው። እርሱ ም፡ ለኔ፡ ምልእክቴ፡ ነው፡ በመልእክቴ፡ ሁሉ፡ እንደ ሁ፡ እጽፋለሁ። ፩፡ ቆሮ፡ ፲፮፡ ፳፩፡፡

፲፰፡ የጌታችን፡ የየሱስ፡ ክርስቶስ፡ጸጋ፡ ከላንት፡ ከ ሁላችሁ፡ ጋራ፡ ትሁን። ፪፡ ጢሞ፡ ፬፡ ፳፪፡፡

ሁለተኛ፡ መልእክት፡ ወደ፡ ተሰሎንቄ፡ ሰዎች፡ በአቴና፡ አገር፡ ተጻፈች።

# የሐዋርያ ፡ የጳውሎስ ፡ መልእክት ፡ መጀመርያይቱ ፡ ወደ ፡ ጢሞቴዎስ ።

ምዕራፍ፡ ፩፡

፩፡ ከጳውሎስ፡የየሱስ፡ክርስቶስ፡ሐዋርያ፡በመድ ኃኒታችን፡ በእግዚአብሔር፡ትእዛዝ፡በተስፋችንም፡ በየሱስ፡ክርስቶስ። ቆላ፡ ፩፡ ፳፯፡፡

፪፡ ወደ፡ጢሞቴዎስ፡ወደ፡እውነተኛ፡*ልጅ፡ በሃይ ማኖት። ጸጋ፡ ምህረትም፡ ሰላምም ፡ ከእግዚአብሔ ር፡ካባታችን፡ ከየሱስ፡ ክርስቶስም፡ ከጌታችን። *ቲቶ፡ ፩፡ ፬፡፡

፫፡ እንደ፡ለመንሁህ፡ በኤፌሶን፡ትቀመጥ፡ ዘንድ፡ እኔ፡ወደ፡ *መቄዶንያ፡ በሔድሁ፡ጊዜ፡ ሰዎችን፡ ለማ ዘዝ፡ ሌላ፡ ትምህርት፡ እንዳያስተምሩ። *የሐዋ፡ ፳፡ ፩፡፡

፬፡ ወደ፡*ጨወታም፡እንዳያደምጹ፡ ፍጻሜ፡ወደ፡ ሌለው። ወደ፡ትውልድ፡ድብደቤ፡መለያየት፡ የሚያ ደርግ። የእግዚአብሔርን፡ ሥርዓት፡ በሃይማኖት፡ ያ ለውን፡ ከመሥራት፡ይልቅ፡አንተ፡እንደሁ፡አድርግ። *ምዕ፡ ፬፡ ፯፡፡

፭፡ የትእዛዝ፡*ፍጻሜ፡ግን፡ ፍቅር፡ ናት፡ ከንጹሕ፡ ልብ፡ ከመልካምም፡ ሕሊና፡ግብዝ፡ ከሌለበትም፡ ሃ ይማኖት። ሮሜ፡ ፲፪፡ ፱፡ ፲፡፡

፮፡ ከዚህ፡ነገር፡ ሰዎች፡*ራቁ፡ ወደ፡ ከንቱ፡ ነገርም፡ ተመለሱ። *ምዕ፡ ፮፡ ፬፡ ፳፡፡

፯፡ የሕግ፡ *መምህራን፡ ይሆኑ፡ ዘንድ፡ ወደዋልና፡ የሚሉትንም፡ የሚያጸኑትንም፡ †አያውቁም። *ዮሐ፡ ፫፡ ፲፡፡ †ምዕ፡ ፮፡ ፬፡ ፳፡፡

፰፡ እኛ፡ግን፡እናውቃለን፡ ኦሪት፡ መልካም፡እንደ ሆነች፡ሰው፡እንደ፡ ሕግ፡ አገባብ፡ ቢያረገው። ሮሜ፡ ፯፡ ፲፪፡፡

፱፡ ይህነን፡ሲያውቅ፡ሕግ፡ለጻድቅ፡እንዳልተሰራ፡ ለኃጢአተኞችና፡ ለዓመፀኞች፡ እንጂ፡ ለመናፍቃን፡ ለክፉ፡ ሰዎችም፡ ለርኩሳንም፡ ልባቸውም፡ ለከፋ፡ አባታቸውንና፡ እናታቸውን፡ ለሚመቱ። ሰዎችን፡ ለ ሚገሉ።

፲፡ ላመንዝሮች። ከወንድ፡ ጋራ፡ ለሚተኙ። *የሰ ው፡ ልጆችን፡ ለሚሸጡ። ላሰተኞች። ባሰት፡ ለሚም ሉ።እውነተኛንም፡ ትምህርት፡ †ለሚጣላ፡ ሁሉ። *ዘፀአ፡ ፳፩፡ ፲፮፡፡ †ምዕ፡ ፮፡ ፫፡፡

፲፩፡ እንደ፡ *ብሩክ፡ እግዚአብሔር፡እንደ፡ ተመሰ ገነው፡ ወንጌል፡እኔ፡ የታመንሁበት፡ *ምዕ፡ ፮፡ ፲፭፡፡

፲፪፡ እኔም፡አመሰግነዋለሁ፡ ክርስቶስ፡ የሱስ፡ጌታ ችነን፡ ያጠነከረኝ፡ *የታመነም፡ የቈጠረኝ፡ ለመልእ ክቱም፡ የመረጸኝ። *የሐዋ፡ ፱፡ ፲፭፡፡ ገላት፡ ፩፡ ፲፫፡፡

፲፫፡ እኔን፡ቀድሞ፡ ተሳዳቢ፡ የነበርሁትን፡ አሳዳጅ ም፡የሚጐዳን፡ነገርም፡ያደረግሁ። ነገር፡ግን፡ይቅር፡ተ ባልሁ፡ይህነን፡ባለማመን፡አደርግ፡ነበርሁና፡ሳላውቅ፡

፲፬፡ የጌታችንም፡ ጸጋ፡ በኔ፡ ላይ፡ በዛች፡ ከሃይማኖ ት፡ ጋራ፡ ከፍቅርም፡ በየሱስ፡ ክርሰቶሰ።

፲፭፡ ነገሪቱም፡እውነተኛ፡ ናት፡ እርስዋንም፡ መቀ በል፡የሚገባ፡ ነው፡ በፍጹም፡ መቀበል። ክርስቶስ፡ የ ሱስ፡*ወደ፡ዓለም፡እንደ፡ መጣ፡ ኃጢአተኞችን፡ ሊያ ድን፡እኔ፡መጀመርያቸው፡የምሆን። *ማቴ፡ ፲፰፡ ፲፩፡፡

፲፮፡ ነገር፡ግን፡ስለዚህ፡ምህረት፡ሆነልኝ፡ክርስቶስ፡ የሱስ፡የትዕግሥቱን፡ ርዝመት፡ ሁሉ፡ አስቀድሞ፡ በኔ፡ይገልጥ፡ዘንድ፡በርሱ፡ ለሚያምኑ፡ ምሳሌ፡ሁኜ፡ ለዘላለም፡ ሕይወት።

፲፯፡ አሁንም፡የዘላለም፡ንጉሥ፡ የማይጠፋ፡ የማይታይም፡ አንዱ፡ አምላክ፡ ክብር፡ ምስጋናም፡ ይገባዋል፡ ለዘላለም። አሜን።

፲፰፡ ይህችን፡ ትእዛዝ፡ አደራ፡ ሰጥቼሃለሁ፡ ልጄ፡ ሆይ፡ ጢሞቴዎስ፡ ስላንተ፡ አንደ፡ ተቀደመችው፡ ትንቢት፡ መልካም፡ *ገድል፡ ትጋደልባት፡ ዘንድ።

*ም፡ ፮፡ ፲፪፡፡

፲፱፡ በሃይማኖት፡በበጎም፡ ሕሊና፡ይህችን፡ሰዎች፡ ከርሳቸው፡ የጣልዋት፡ ከሃይማኖትም፡ የጠፉ።

ም፡ ፫፡ ፱፡፡

፳፡ ከርሳቸውም፡*ሄሜኔዎስና፡እስክንድሮስ፡†ለሰይጣን፡አሳልፌ፡የሰጠኋቸው፡እንዲሣቀዩ፡ደግሞ፡ እንደይሰድቡ። *፪፡ ጢሞ፡ ፪፡ ፲፯፡፡ †፩፡ ቆሮ፡ ፭፡ ፭፡፡

## ምዕራፍ፡ ፪፡

፩፡ እኔም፡እመክክራለሁ፡ከሁሉ፡ በፊት፡*ልመና፡ ጸሎትም፡ መማለድም፡ ምስጋናም፡ ስለ፡ ሰው፡ ሁሉ፡ እንዲደረግ። *ፊል፡ ፬፡ ፮፡

፪፡ ስለ፡ነገሥታት፡ስለ፡ ታላላቆችም፡ ሁሉ። በሕይወታችን፡እንኖር፡ዘንድ፡ በጸጥታና፡በሰላም፡ በመልካም፡አምልኮ፡ ሁሉ፡ በቅንነትም።

፫፡ ይህ፡ መልካም፡ ነውና፡ *በመድኃኒታችንም፡ በእግዚአብሔር፡ፊት፡የተቀበለ። *ም፡ ፩፡ ፩፡፡ ና፡ ፬፡፲፡፡

፬፡ ሰው፡*ሁሉ፡ይድን፡ ዘንድ፡የሚወድ፡እውነትንም፡ወደ፡ማወቅ፡ይመጡ፡ዘንድ። *ሕዝ፡ ፲፰፡ ፳፫፡፡

፪፡ ጴጥ፡ ፫፡ ፱፡፡

፭፡ እግዚአብሔር፡አንድ፡ነውና፡ በእግዚአብሔርም፡ መካከል፡ በሰውም፡ መካካል፡ ያለው፡ †አንድ፡ ነው፡ እርሱም፡ ሰው፡ ክርስቶስ፡ የሱስ።

ኢሳ፡ ዛ፭፡ ፳፩፡ ፳፪፡፡ ዮሐ፡ ፲፯፡ ፫፡፡ †ዕብ፡ ፲፪፡ ፳፬፡፡

፮፡ *ራሱን፡ የለወጠ፡ለሁሉ፡ ቤዛ። ምስክርነቱም፡ በጊዜዋ፡ የመጣች። ገላት፡ ፩፡ ፬፡፡ ና፡ ፪፡ ፳፡፡

ቲቶ፡ ፪፡ ፲፬፡፡

፯፡ እኔ፡ ጸሪ፡ *መለክተኛም፡ የሆንሁላት። እውነት፡ እላለሁ፡ አስትም፡ አልናገርም። እኔ፡ ለአሕዛብ፡ መምህር፡ ሆንሁ፡ በሃይማኖት፡ በእውነትም።

*የሐዋ፡ ፱፡ ፲፭፡፡ ፪፡ ጢሞ፡ ፩፡ ፲፩፡፡

፰፡ እኔም፡ እወደለሁ፡ወንዶች፡ ይጸልዩ፡ ዘንድ፡ በየስፍራው፡የተቀደሰም፡እጅ፡ወደ፡ላይ፡ ይዘረጉ፡ ዘንድ፡ ያለ፡ ቍጣና፡ ያለ፡ መጠራጠር።

፱፡ እንደሁም፡ሴቶች፡በማያስነውር፡ *ልብስ፡ በኀፍረትና፡በጥበብ፡ ራሳቸውን፡ያጌጹ፡ ራስ፡ በመሰራትም፡ አይደለም ። በወርቅም፡ አይደለም ። በዕንቍም፡በውድም፡ ልብስ፡ አይደለም።

*፩፡ ጴጥ፡ ፫፡ ፫፡—፭፡፡

፲፡ እግዚአብሔርን ፡ *ለሚፈሩት ፡ ሴቶች፡ እንደሚገባ፡እንጂ፡ መልካም፡ በመስራት። *ም፡ ፭፡ ፲፡፡

፲፩፡ ሴቲቱም፡በቀስታ፡በትሕትናም፡ የምትማር፡ ትሁን። ኤፌ፡ ፭፡ ፳፪፡፡

፲፪፡ ሴት፡ግን፡*ታስተምር፡ዘንድ፡ የማዝ፡ አደደሉሁም። †በወንድ፡ላይም፡ አትድፈር፡ ዝም፡ ትበል፡ እንጂ። *፩፡ ቆሮ፡ ፲፬፡ ፴፬፡፡ †ዘፍ፡ ፫፡ ፲፮፡፡

፲፫፡ አደም፡ በፊት፡ ተፈጥርዋልና፡ ኋላም፡ ሔዋ።

ዘፍ፡ ፩፡ ፳፯፡፡

፲፬፡ አደም፡ አልተታለለም፡ *ሴቲቱ፡ ተታላ፡ ወደ፡ መተላለፍ፡ ገባች፡ እንጂ። *ዘፍ፡ ፫፡ ፮፡፡

፪፡ ቆሮ፡ ፲፩፡ ፫፡፡

፲፭፡ ነገር፡ግን፡ ልጆችን፡ በመውለድ፡ ትድናለች፡ በሃይማኖት፡ ብትጸና፡ በፍቅርም፡ በቅድስናም፡ ከአኀብ፡ጋራ።

## ምዕራፍ፡ ፫፡

፩፡ ነገሩ፡እውነት፡ነው። *ማንም፡ጳጳስነውን፡ቢሻ፡ መልካም፡ ነገር፡ ይሻል። የሐዋ፡ ፳፡ ፳፰፡፡

፪፡ *ጳጳስም፡ነውር፡ እንዲደገኝበት፡ ይገባዋል። ያንዲት፡ ምሽትም፡ባል፡ ያለ። የሚተጋም፡ የንብረቱንም፡ልክ፡ የሚጠብቅ። ገገባብ፡ ያለ። እንግዶችንም፡ የሚወድ። አስተማሪም። ዘሌዋ፡ ፳፩፡ ፲፯፡፡

ቲቶ፡ ፩፡ ፮፡ ፯፡፡

፫፡ የጸጅም፡ ሰካሪ፡ ያደደለ። የማይማታም። የረከሰውንም፡ ረብ፡ የማይሻ። ታጋሽ፡ እንጅ። የማይጣላም። የብር፡ ወዳጅም፡ ያደደለ። *ዘሌዋ፡ ፲፡ ፰፡፡

ቲቶ፡ ፩፡ ፯፡፡

፬፡ የገዛ፡ ቤቱንም፡ ሥርዓት፡ ያሳመረ፡ *የታዘዙለትም፡ልጆች፡ ያሉት፡ በክብድና፡ ሁሉ።

፩፡ ሳሙኤ፡ ፪፡ ፲፪፡፡

፭፡ ሰው፡ ግን፡ የርሱን፡ ቤት፡ ለመግዛት፡ ባያውቅ፡ እንዴት፡ይቻለዋል፡የእግዚአብሔርን፡ ቤተ፡ ክርስቲያን፡ይጠብቅ፡ዘንድ።

፮፡ አዲስ፡ ተክልም፡ በሃይማኖት፡ አይሁን፡ ልቡ፡ እንደይታበይ፡ወደ፡ዲያብሎስ፡ ፍርድም፡ እንደይወድቅ።

፯፡ ደግሞም፡ *ደህና፡ ምስክር፡ †በሚደ፡ ሰዎች፡ ዘንድ፡የሆነለት፡ይሁን፡ ወደ፡ ስድብ፡ እንደይወድቅ፡ ወደ፡ዲያብሎስም፡ ወጽመድ። *ም፡ ፭፡ ፲፡፡

†፩፡ ቆሮ፡ ፭፡ ፲፪፡ ፲፫፡፡

፰፡ ዲያቆናትም፡ ደግሞ፡ የጸኑ፡ ይሁኑ። ባለ፡ ሁለት፡ነገርም፡ አይሁኑ። እጅግ፡ጸጅ፡ወደ፡ መጠጣትም፡ አይዘንበሉ። ርኩስ፡ ትርፍም፡ አይውደዱ።

ፊል፡ ፩፡ ፩፡፡ የሐዋ፡ ፮፡ ፫፡፡

፱፡ የሃይማኖት፡ ምሥጢር፡ ይሁንላቸው፡ በንጹሕ፡ሕሊና።

፲፡ እሌህም፡ አስቀድመው፡ ይፈተኑ፡ ከዚያ፡ በኋላም፡ ነውር፡ ከሌለባቸው፡ ያገልግሉ።

፲፩፤ *ሴቶችም፡ደግሞ፡ የጸኑ፡ይሁኑ፡ ሰደቦች፡ ያይ
ደሉ፡ለስካርና፡እጅግ፡ለመብላት፡ ያልተሰጡ፡ በሁሉ
ም፡የታመኑ። *ቲቶ፡ ፪፡ ፫፡፡
፲፪፤ ዲያቆናትም፡ *ያንዲት፡ ሴት፡ ባሎች፡ ይሁኑ፡
የልጆቻቸውንና፡ የቤታቸውን፡ ሥርዓት፡ ያሳመሩ።
*ቍ፡ ፪፡፡
፲፫፤ መልካሙን፡ ማገልገል፡ *የሚያገለግሉ፡ መል
ካሙን፡ መዓርግ፡ ለራሳቸው፡ ያደርጋሉና፡ ብዙ፡ †ድ
ፍረትንም፡ በክርስቶስ፡ የሱስ፡ ሃይማኖት።
*ማቴ፡ ፳፭፡ ፳፩፡፡ †፩፡ ዮሐ፡ ፫፡ ፳፩፡፡
፲፬፤ ይህነን፡ነገር፡ጻፍሁልህ፡እኔ፡ተስፋ፡ ሳደርግ፡ ወ
ደንተ፡ፈጥኜ፡እመጣ፡ዘንድ።
፲፭፤ የዘገየሁም፡ እንደ፡ ሆንሁ፡ አንተ፡ ታውቅ፡ ዘ
ንድ፡ እንዴት፡ እንዲገባህ፡ በእግዚአብሔር፡ *ቤት፡
እንድታደርግ፡ቤት፡ የሕያው፡ የእግዚአብሔር፡ቤተ፡
ክርስቲያን፡ የሚሆን፡ የጽድቅ፡ ዓምድ፡ የእውነት
ም፡መሠረት። *፪፡ ጢሞ፡ ፪፡ ፳፡፡
፲፮፤ በውነትም፡ ታላቅ፡ ነው፡ የአምልኮት፡ ምሥ
ጢር።*አምላክ፡በሥጋ፡ተገለጠ።በመንፈስ፡†ጸደቀ።
ለመላእክት፡ ታየ። በአሕዛብ፡ ተሰበከ። ከዓለም፡ታ
መነ። **በምስጋናም፡ ታረገ፡ ወጣ። *ዮሐ፡ ፩፡ ፲፬፡፡
†ዮሐ፡ ፲፮፡ ፲፡፡ ሮሜ፡ ፩፡ ፬፡፡ **ማር፡ ፲፮፡ ፲፱፡፡

ምዕራፍ፡ ፬፤

፩፤ መንፈስ፡ግን፡ በግልጥ፡ይላል፡*በኋለኛው፡ ዘመ
ን፡ ሰዎች፡ ከሃይማኖት፡ እንዲርቁ፡ የሚያስቱንም፡
አጋንንት፡ የሰይጣናትንም፡ ትምህርት፡ ሲከተሉ።
*ደን፡ ፯፡ ፳፭፡፡ ፪፡ ጢሞ፡ ፫፡ ፩፡፡ ፪፡ ጴጥ፡ ፫፡ ፫፡፡
፩፡ ዮሐ፡ ፪፡ ፲፰፡፡ ይሁ፡ ፲፰፡፡
፪፤ በማስመሳል፡ ባሰትም፡ ነገር። ሕሊናቸው፡ በጋ
ለ፡ብረት፡ የተቃጠለች፡ናት።
፫፤ መጋባትንም፡ ይከለክላሉ። መብልም፡ ያርማ
ሉ፡*እግዚአብሔር፡ የፈጠራትን፡ የሚያምኑ፡ እውነ
ትንም፡የሚያውቁ፡†በምስጋና፡ይቀበልዋት፡ዘንድ።
*ዘፍ፡ ፱፡ ፫፡፡ †፩፡ ቆሮ፡ ፲፡ ፴፡ ፴፩፡፡
፬፤ የእግዚአብሔር፡ፍጥረት፡ሁሉ፡ መልካም፡ነው
ና፡ከርሱም፡አንዳች፡ርኩስ፡ የለም፡ በምስጋና፡ ቢቀበ
ሉት። ዘፍ፡ ፩፡ ፴፩፡፡ የሐዋ፡ ፲፡ ፲፭፡፡
፭፤ በእግዚአብሔር፡ ነገር፡ በጸሎትም፡ ይቀደሳ
ልና።
፮፤ ይህነን፡ለወንድሞች፡ብታስተምር፡ የየሱስ፡ ክ
ርስቶስ፡ መልካም፡ አገልጋይ፡ ትሆናለህ፡ በሃይማኖት
ም፡ነገር፡በመልካምም፡በምትከተለው፡ትምህርት፡
*ታድጋለህ። ፪፡ ጢሞ፡ ፩፡ ፭፡፡
፯፤ ከርኩስ፡ ጨወታ፡ ግን፡ ከባልቴቶችም፡ *ተረት፡
ራቅ፡ ራስህንም፡ ባምልኮት፡ አስለምደው።
ም፡ ፩፡ ፬፡፡ ና፡ ፮፡ ፳፡፡ ፪፡ ጢሞ፡ ፪፡ ፲፮፡ ፳፫፡፡
ቲቶ፡ ፩፡ ፲፬፡፡ ና፡ ፫፡ ፱፡፡
፰፤ ሥጋዊ፡ ነገር፡ ማድረግ፡ ለጥቂት፡ ዘመን፡ ይጠቅ
ማልና፡*አምልኮት፡ግን፡ በሁሉ፡ይረባል፡ ለርሱም፡ ተ
ስፋ፡አለው፡ በዚህ፡ ዓለም፡ ሕይወት፡ በሚመጣው
ም፡ ደግሞ። *ም፡ ፮፡ ፮፡፡
፱፤ ነገሩ፡ እውነት፡ ነው፡ ለሁሉ፡ መቀበልም፡ ይገባ
ል። ም፡ ፩፡ ፲፭፡፡
፲፤ ስለዚህ፡ እንደክማለንና፡ እንሰደብማለንና፡
ሕያውን፡እግዚአብሔርን፡ ስላመነ፡ *ሰውን፡ ሁሉ፡ የ
ሚያድን፡ †ይልቁንም፡ የሚያምኑን።
*ቲቶ፡ ፪፡ ፲፡ ፲፩፡፡ †ኤፌ፡ ፭፡ ፳፫፡፡
፲፩፤ ይህነን፡እዘዝ፡አስተምርም።
፲፪፤ *ማንም፡ ሕፃንነትህን፡ አይናቀው፡ ነገር፡ ግን፡
ለምእመናን፡ምሳሌ፡ ሁን፡በነገር፡ ባካሄድ፡ በፍቅር፡
በመንፈስ፡በሃይማኖት፡ በንጽሕና። *ቲቶ፡ ፪፡ ፲፭፡፡
፲፫፤ እስክመጣ፡ ድረስ፡ አዘውትር፡ *በማንባብና፡
በምክር፡ በትምህርም። *ዮሐ፡ ፭፡ ፴፱፡፡
፲፬፤ በተሰጠችህ፡ጸጋ፡ በትንቢት፡ በቀሳውስትም፡
*እጅ፡ መጫን፡ ቸል፡ አትበል። *ም፡ ፭፡ ፳፪፡፡
የሐዋ፡ ፮፡ ፮፡፡ ና፡ ፰፡ ፲፯፡፡
፲፭፤ ይህችን፡ አስባት፡ አዘውትራትም። እድገት
ህ፡ ለሁሉ፡ ይገለጥ፡ ዘንድ።
፲፮፤ ለራስህ፡ ተጠንቀቅ፡ ለትምህርትህም፡ በርሰ
ዋም፡ጽና። ይህንም፡ ያደረግህ፡ እንደሆንህ፡ *ራስህ
ን፡ ታድናለህ፡ የሚሰሙህንም፡ ደግሞ።
*ሮሜ፡ ፲፩፡ ፲፬፡፡

ምዕራፍ፡ ፭፤

፩፤ *ሽማግሌውን፡ አትዘለፈው፡ እንደባት፡ ለምነ
ው፡ እንጂ። ጐበዛዝቱን፡ እንደ፡ ወንድሞች።
ዘሌዋ፡ ፲፱፡ ፴፪፡፡
፪፤ ሽማግሊት፡ ሴቶችን፡ *እንደናቶች። ቈነጃጅቶ
ን፡ ሴቶች፡ እንደ፡ እኅቶች፡ በንጽሕና፡ ሁሉ።
*ዮሐ፡ ፲፱፡ ፳፯፡፡
፫፤ ባልቴቶችን፡ አክብራቸው፡ በውነት፡ ባልቴቶች፡
የሆኑትን። ቍ፡ ፭፡፡
፬፤ ከርሳቸው፡ ግን፡ ባልቴት፡ ብትኖር፡ ልጆች፡ ያልዋ
ት፡ወይም፡ የልጅ፡ልጆች። አስቀድመው፡ ይማሩ፡ ቤ
ታቸውን፡ ያበጁ፡ ዘንድ፡ ለወላጆቻቸውም፡ ፍዳ፡ ይ
መልሱ፡ ዘንድ። ይህ፡ በእግዚአብሔር፡ ዘንድ፡ ያመ
ረ፡ የተቀበለም፡ ነውና።
፭፤ በውነት፡ግን፡ ባልቴት፡ የሆነች፡ ብቻዋንም፡ያለ
ች፡ ተስፋዋ፡ እግዚአብሔር፡ ነው፡ *በጸሎትም፡ በል
መናም፡ ትያዛለች፡ ሌትና፡ ቀን።
*ሉቃ፡ ፪፡ ፴፯፡፡ ና፡ ፲፰፡ ፩፡፡
፮፤ ቅምጥሊቱ፡ግን፡ ምንም፡ ባትሞት፡ ፈጽማ፡ የ
ሞተች፡ናት። ሮሜ፡ ፰፡ ፲፫፡፡
፯፤ ይህነን፡እዘዛቸው፡ነውር፡እንዳይገኝባቸው።
ም፡ ፬፡ ፲፩፡፡
፰፤ ለማንም፡ ሰዎች፡ ቢኖሩት፡ አንዳች፡ የሚኾ፡የ
ሚበጃቸውንም፡ ነገር፡ ባያስብላቸው፡ ይልቁንም፡

*ለቤቱ፡ ሰዎች፡ ሁሉ። ተሃይማኖቱን፡ የካደ፡ ከማያ
ምኑትም፡ የከፋ፡ ነው። *ገላ፡ ፮፡ ፲፡
†፪፡ ጢሞ፡ ፫፡ ፭፡፡

፱፡ ባልቴት፡ ለዲቁና፡ ብትመረጥ፡ ዕድሚዋ፡ ከስ
ድሳ፡አመት፡ያነሰ፡አይሁን፡ያንድ፡ወንድ፡ ምሽት፡ የነ
በረች።

፲፡ መልካም፡ነገር፡ በማድረግ፡ የተመሰከረላት፡ ል
ጆችዋን፡መልካም፡ አድርጋ፡ ካሳደገች፡ *እንግዶችን፡
ከተቀበለች፡ የቅዱሳንን፡ እግር፡ ካፀበች፡አዘንተኞች
ን፡ከረዳች። መልካምን፡ነገር፡ ሁሉ፡ የተከተለች፡ ከ
ሆነች። *ዕብ፡ ፲፫፡ ፪፡፡

፲፩፡ ቆነጃጅቱን፡ ባልቴቶች፡ ግን፡ ራቃቸው ። ለፍ
ትወት፡ይለቀቃሉና፡ክርስቶስን፡ ትተው፡ ሊያገቡም፡
ይወዳሉና።

፲፪፡ ፍርዳቸውም፡ ተዘጋጅቶባቸዋል፡ የቀደመው
ን፡ሃይማኖታቸውን፡ እንደ፡ ካዱ።

፲፫፡ ከዚያም፡ ጋራ፡ ተግባር፡ መፍታት፡ ይማራሉ፡
ቤት፡ ለቤትም፡ *ይዞራሉ። ተግባረ፡ ፍቾችም፡ ብቻ፡
አይደሉም፡ታውኳችና፡ ለገመኞች፡ ናቸው፡ እንጂ፡ የ
ማይገባም፡ ነገር፡ ይናገራሉ። *ምሳ፡ ፳፡ ፲፱፡፡

፲፬፡ እንግዲህም፡እወዳለሁ፡*ቆነጃጅቱ፡ ባልቴቶ
ች፡ ባል፡ እንዲያገቡ፡ ልጆችም፡ እንዲወልዱ፡ ቤታቸ
ውንም፡ እንዲሰሩ፡ ለጸላትም፡ አንድ፡ ምክንያት፡ሰ
ንኳ፡ለመሰደብ፡ እንዳይሰጡ። ፩፡ ቆሮ፡ ፯፡ ፱፡፡

፲፭፡ ከርሳቸው፡ ወገን፡ ከሰይጣን፡ በኋላ፡ የተከተ
ሉት፡ አሉና። ም፡ ፩፡ ፯፡፡

፲፮፡ ላመነ፡ሰው፡ወይም፡ ላመነች፡ ቤት፡ባልቴቶች፡
ቢኖሩት፡ በምግባቸው፡ ይቁሙላቸው። በቤተ፡ ክር
ስቲያንም፡ ላይ፡ አይክበዱባት፡ በውነት፡ ባልቴቶች፡
ለሚሆኑ፡ ይበቃቸው፡ ዘንድ።

፲፯፡ ቄሶች፡*ደህና፡ የሚቀሙ፡ ከሆኑ፡ ዕፅፍ፡ ክብ
ር፡ይገባቸዋል፡ ይልቁንም፡ በነገር፡ ለሚደክሙ፡ በማ
ስተማርም። *ሮሜ፡ ፲፪፡ ፰፡፡ ፍ፡ ፲፭፡ ፳፯፡፡

፲፰፡ መጽሐፍ፡ *ይላልና። የሚያርሰውን፡ በሬ፡ አ
ፋን፡ አትዝጋ። †ለሰራተኛም፡ ዋጋው፡ ይገባዋል።
*ዘዳግ፡ ፳፭፡ ፬፡፡ ፩፡ ቆሮ፡ ፱፡ ፱፡፡ †ሉቃ፡ ፲፡ ፯፡፡

፲፱፡ በቄስ፡ላይ፡ መክሰስ፡ አትቀበል፡ በሁለት፡ ም
ስክር፡ካልሆነ፡ወይም፡ በሦስት። ዮሐ፡ ፰፡ ፲፯፡፡

፳፡ ኃጢአት፡ የሚሰሩትን፡ ዘልፍ፡ *በሁሉ፡ ፊት፡
ሌሎች፡ደግሞ፡ እንዲፈሩ። *ኤፌ፡ ፭፡ ፲፪፡ ፲፫፡፡

፳፩፡ በእግዚአብሔር፡ፊት፡ አስመሰክርብሃለሁ፡
በጌታችንም፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስና፡ በተመረጹት ፡ በ
መላእክት፡ ፊት። ይህችን፡ ትእዛዝ፡ ትጠብቅ፡ ያለ፡
አሳብህ ፡ መዘንበል፡ አንዳችም ፤ በአድልዎ ፡ ሳታድ
ርግ።

፳፪፡ በማንም፡ ላይ፡ ፈጥነህ፡ *እጅህን፡ አትጫን፡
በሌሎችም፡ ኃጢአት፡አትግባ። ራስህን፡ ጠብቅ፡ በን
ጽሕና። *ዮሐዋ፡ ፯፡ ፯፡፡

፳፫፡ ደግሞ፡ውኃ፡ብቻ፡ አትጠጣ፡*ጥቂት፡ጸጅ፡ጠ
ጣ፡ እንጂ፡ ስለ፡ ሆድህ፡ ስለ፡ ደዌህም፡ ብዛት።
*መዝ፡ ፻፬፡ ፲፭፡፡

፳፬፡ ኃጢአታቸው፡ የታወቀች፡ ሰዎች፡ አሉ፡ ትቀ
ድማቸውማለች፡ ወደ፡ ፍርድ። ሌሎችንም፡ ኃጢአ
ታቸው፡ ትከተላቸዋለች።

፳፭፡ እንደዚሁም፡ መልካም፡ መሰራት፡ *የታወቀ
ች፡ናት። ሌሎችም፡ ደግሞ፡ አይሰወሩም።
ገላ፡ ፭፡ ፳፪፡፡

## ምዕራፍ፡ ፮፡

፩፡ ከቀምበር፡በታች፡ያሉ፡*ባሮች፡ ሁሉ፡በጌቶቻቸ
ው፡ ይያዙ፡ በክብር፡ ሁሉ፡ የእግዚአብሔር፡ ስም፡ ት
ምህርቱም፡እንዳይሰደቡ። *ኤፌ፡ ፮፡ ፭፡፡ ቲቶ፡ ፪፡ ፱፡፡

፪፡ ያመኑም፡ጌቶች፡እንደልዋቸው፡አይናቋቸው፡
ወንድሞቻቸው፡ ናቸውና። ነገር፡ግን፡ መገዛት፡ ይጨ
ምሩላቸው፡ያመኑ፡ ናቸውና፡ የተወደዱም፡ የእግዚ
አብሔርንም፡ በጉነት፡ ወሰዱ፡ ከርሳቸው፡ ጋራ። ይህ
ነን፡*አስተምር፡ገሥፅም። *ም፡ ፬፡ ፲፩፡፡ ቲቶ፡ ፫፡ ፰፡፡

፫፡ ማነም፡*ሌላ፡ትምህርት፡የሚያስተምር፡ ቢኖ
ር፡ተወደሚበጅ፡ትምህርትም፡የማይቀርብ፡ለጌታች
ን፡ ለየሱስ፡ ክርስቶስ፡ ወደሚሆን፡ ወደ፡ መልካም፡
አምልኮትም፡ ትምህርት። ገላ፡ ፩፡ ፮፡—፱፡፡
፪፡ ጢሞ፡ ፩፡ ፲፫፡፡

፬፡ ይህ፡ ልቡ፡ ይታበያል፡ አንዳች፡ ሳያውቅ ። እር
ሱ፡ ደካማ፡ ነው፡ እንጂ፡ በክርክር፡ በብዙ፡ ነገርም፡ በ
መመራመር፡ ቅናት፡ የሚሆንበት። ሐሜትም፡ ስድ
ብም፡ ክፉ፡አሳብም።

፭፡ መለያየትም፡ ልባቸውም፡ የጠፋ፡ሰዎች፡ ክፉ
ት፡ እውነትንም፡ ያጡ። መልካሚቱም፡ አምልኮ፡
እንደ፡ ንግድ፡ መሰለቻቸው። እንደዚህ፡ ካሉ፡ ራቅ።

፮፡ አምልኮ፡ ግን፡በቃኝ፡ ከማለት፡ *ረብ፡ ታላቅ፡ ረ
ብ፡ ነው። ተበቃኝ፡ ያሰኛል። *ም፡ ፬፡ ፰፡፡
†ፊል፡ ፬፡ ፲፩፡ ፲፪፡፡

፯፡ ወደ፡ዓለም፡ *አንዳች፡ ይዘን፡ አልገባነምና፡ ከ
ርስዋም፡አንዳች፡ ይዘን፡ ማውጣት፡ እንዳንችል፡ግል
ጥ፡ነው። *መክ፡ ፭፡ ፲፬፡፡

፰፡ ስለዚህም፡ *ምብልና፡ ልብስ፡ ካገኘነ፡ ይበቃ
ናል። ዘፍ፡ ፳፰፡ ፳፡፡ ምሳ፡ ፴፡ ፰፡፡

፱፡ ባለጠግነት፡ግን፡ *የሚወዱ፡ በፈተና፡ ይወድቃ
ሉ፡ በወጽመድም፡ በብዙም፡ ፍትወት፡ በምትጎዳ
ም፡ ሰንፍና፡ ሰውን፡ የምታሠጥም፡ በሞት፡ በጥፋት
ም። *ምሳ፡ ፳፫፡ ፬፡፡ ፍ፡ ፳፰፡ ፳፪፡፡

፲፡ የክፉ፡ ሁሉ፡ሥር፡ ኩብት፡ መውደድ፡ ነውና። ይ
ህነንም፡ ሰዎች፡ ሲወዱ፡ ከሃይማኖትም፡ ጠፉ፡ ራሳ
ቸውንም፡ ወደ፡ ብዙ፡ አዘን፡ አገቡ።
ሉቃ፡ ፲፪፡ ፲፭፡—፳፩፡፡ ኤፌ፡ ፭፡ ፭፡፡

፲፩፡ አንተ፡ግን፡ የእግዚአብሔር፡ ሰው፡ ሆይ፡ ከዚ
ህ፡ ሁሉ፡ ሽሽ፡ በጽድቅም፡ *ሩጥ፡ በአምልኮትም። በ

ሃይማኖትም፡ በፍቅርም፡ በትዕግሥትም፡ በየዋህትም። *፪፤ ጢሞ፡ ፪፤ ፳፪። ዕብ፡ ፲፪፤ ፲፬።

፲፪፤ መልካሙን፡ የሃይማኖትን፡ ገድል፡ *ተጋደል፡ ወደ፡ ዘላለሙም፡ ሕይወት፡ *ድረስ። ወደርሱዋ፡ ደግሞ፡ የተጸራህ፡ መልካሙም፡ ማመንም፡ አመንህ፡ በብዙ፡ ምስክሮች፡ ፊት። *፩፤ ቆር፡ ፱፤ ፳፭፤ ፳፮። ፊል፡ ፫፤ ፲፪—፲፬።

፲፫፤ አዝሃለሁ፡ ሁሉን፡ *በሚያድን፡ በእግዚአብሔር፡ ፊት፡ †በየሱስ፡ ክርስቶስም፡ በጴንጤኑ፡ በጲላጦስ፡ ፊት፡ በመልካም፡ ማመን፡ የመሰከረ። ዘዳግ፡ ፴፪፤ ፴፱። †ዮሐ፡ ፲፰፤ ፴፯። ና፡ ፲፱፤ ፲፩።

፲፬፤ ይህችን፡ ትእዛዝ፡ ትጠብቅ፡ ዘንድ፡ ያለ፡ ነውር፡ ያለ፡ ሐሜትም፡ የሱስ፡ ክርስቶስ፡ ጌታችን፡ እስኪገለጥ፡ ድረስ።

፲፭፤ በጊዜው፡ የሚገልጠው፡ የተመሰገነ፡ የሚሆን፡ ችሎት፡ ያለው፡ ብቻው። †የነገሥታት፡ ንጉሥ፡ **የጌቶችም፡ ጌታ። *ም፡ ፩፤ ፲፩። †ራእ፡ ፲፯፤ ፲፬። **ዘዳግ፡ ፲፤ ፲፯።

፲፮፤ አንድ፡ ብቻው፡ እርሱ፡ የማይሞት፡ በብርሃን፡ የሚኖር፡ ወደርሱ፡ ሰው፡ የማይቀርብ። ከሰውም፡ አንድ፡ *የማያየው፡ ደግሞም፡ ያየው፡ ዘንድ፡ የማይቻል። ክብር፡ ጽንዓትም፡ ያለው፡ ለዘላለም። አሜን። ዮሐ፡ ፩፤ ፲፰።

፲፯፤ የዚህን፡ ዓለም፡ ባለጠጎች፡ እዘዛቸው፡ ልባቸውን፡ እንዳያኰሩ፡ በሚያልፈውም፡ ባለጠግነት፡ እንዳይታመኑ፡ ሁሉን፡ ለምግብ፡ እንደ፡ ባለጠግነቱ፡ ልግሥና፡ በሰጠነ፡ በእግዚአብሔር፡ ላይ፡ ይታመኑ፡ እንጂ። መዝ፡ ፷፪፤ ፲፩። ሉቃ፡ ፲፪፤ ፳።

፲፰፤ መልካም፡ ስራ፡ ይሰሩ፡ ዘንድ፡ ባማረ፡ ስራ፡ ባለ፡ ጠጋ፡ ይሆኑ፡ ዘንድ፡ ለመለገስ፡ እንዲፈጥኑ፡ ከብታቸውንም፡ ለመክፈል።

፲፱፤ ለራሳቸው፡ መልካም፡ መሠረት፡ እንዲያከማቹ፡ ለሚመጣው፡ ዘመን። የዘላለም፡ ሕይወት፡ ይወስዱ፡ ዘንድ። ማቴ፡ ፮፤ ፳።

፳፤ ጢሞቴዎስ፡ ሆይ፡ ተጠበቅ፡ አደራ፡ በተቀበልሃው። ከርኩስና፡ ከምናምን፡ ነገር፡ በሐሰትም፡ እውቀት፡ ከሚባለው፡ ከመከራከር፡ ተራቅ። ፪፤ ጢሞ፡ ፩፤ ፲፬። †፩፡ ጢሞ፡ ፬፤ ፯።

፳፩፤ እርሱን፡ የሚሉ፡ ሰዎች፡ ከሃይማኖት፡ ጠፍተዋልና። ጸጋ፡ ካንተ፡ ጋራ፡ ትሁን። አሜን። ም፡ ፩፤ ፮። ፪፤ ጢሞ፡ ፪፤ ፲፰።

መልእክት፡ መጀመርያዪቱ፡ ወደ፡ ጢሞቴዎስ፡ ተጻፈች፡ በላዶቅያ፡ አገር፡ በቲቶስም፡ እጅ፡ ተላከች።

# የሐዋርያ ፡ የጳውሎስ ፡ መልእክት ፡ ሁለተኛዪቱ ፡ ወደ ፡ ጢሞቴዎስ ።

ምዕራፍ፡ ፩፤

፩፤ ከጳውሎስ፡ ከየሱስ፡ ክርስቶስ፡ ሐዋርያ፡ በእግዚአብሔር፡ ፈቃድ፡ በክርስቶስ፡ የሱስ፡ እንደምትሆን፡ እንደ፡ ሐይወት፡ ተስፋ። ዮሐ፡ ፩፤ ፬። ፩፤ ዮሐ፡ ፭፤ ፲፩—፲፫።

፪፤ ወደ፡ ጢሞቴዎስ፡ ወደ፡ የተወደደ፡ ልጄ። *ጸጋ፡ ምህረትም፡ ሰላምም፡ ከእግዚአብሔር፡ አብ፡ ከየሱስ፡ ክርስቶስም፡ ከጌታችን። *፩፤ ጢሞ፡ ፩፤ ፪። ቲቶ፡ ፩፤ ፬።

፫፤ እኔ፡ እግዚአብሔርን፡ አመሰግናለሁ፡ ካባቶቼ፡ የማገለግለውን፡ በንጹሕ፡ ሕሊና። በጸሎቴ፡ ሁልጊዜ፡ ሌትና፡ ቀን፡ አስብሃለሁና። የሐዋ፡ ፳፫፤ ፩። የሐዋ፡ ፳፬፤ ፲፮። ሮሜ፡ ፩፤ ፱።

፬፤ አንተንም፡ ለማየት፡ እናፍቃለሁ፡ እንባህን፡ ሳስብ፡ ደስታ፡ ይመላብኝ፡ ዘንድ።

፭፤ ተንኰል፡ የሌለባትን፡ ሃይማኖትህን፡ *አስባለሁና። አስቀድሞ፡ በአሚታህ፡ በሎይድ፡ ያደረች፡ በናትህም፡ በኤውኒቅያ። እኔም፡ ደግሞ፡ አምናለሁ፡ ባንተ፡ እንዳለች። *የሐዋ፡ ፲፮፤ ፩።

፮፤ ስለዚህም፡ አሳስብሃለሁ፡ የእግዚአብሔርን፡ የጸጋውን፡ ሕይወት፡ *ለማደስ። ይህች፡ ያደረችብህ፡ በተሰጠኸው፡ እጄን፡ በላይህ፡ በጫንሁብህ፡ ጊዜ። *፩፤ ተሰ፡ ፭፤ ፲፱። ፩፤ ጢሞ፡ ፬፤ ፲፬።

፯፤ እግዚአብሔር፡ የፍርሃት፡ መንፈስ፡ አልሰጠነምና፡ የኃይል፡ መንፈስ፡ እንጂ፡ የፍቅርም፡ የጥበብም። *ሮሜ፡ ፰፤ ፲፭።

፰፤ አንተም፡ በጌታችን፡ ምስክርነት፡ *አትፈር፡ በኔም፡ በታሠርሁለት፡ ደግሞ። ነገር፡ ግን፡ ስለ፡ ወንጌል፡ መከራ፡ ተቀበል፡ በእግዚአብሔር፡ ኃይል። *ሮሜ፡ ፩፤ ፲፮።

፱፤ እርሱም፡ ያዳነ፡ በተቀደሰች፡ መጽራትም፡ የጸራ፡ እንደ፡ ምግባራችን፡ አይደለም፡ አስቀድሞ፡ በመጽራቱ፡ እንጂ፡ በጸጋውም፡ ለኛ፡ በተሰጠችን፡ በክርስቶስ፡ የሱስ፡ ዓለም፡ ሳይፈጠር። ቲቶ፡ ፫፤ ፭።

፲፤ ዛሬ፡ ግን፡ ተገለጠች፡ ከየሱስ፡ ክርስቶስ፡ ከመድኃኒታችን፡ *መገለጥ፡ የተነሣ፡ †ሞትን፡ የሻረ፡ የማይጠፋንም፡ ሕይወት፡ ያወጣ፡ በወንጌል። ሮሜ፡ ፲፮፤ ፳፭። †፩፤ ቆር፡ ፲፭፤ ፶፭። ዕብ፡ ፪፤ ፲፬።

፲፩፥ እኔ፡ነጋሪ፡ በሆንሁለት፡ ሐዋርያም፡ አስተማሪ ም፡ ለአሕዛብ። ፩፥ ጢሞ፡ ፪፥ ፯።

፲፪፥ ስለዚህም፡ደግሞ፡ይህችን፡ መከራ፡ እሸከማ ለሁ፡ነገር፡ግን፡አላፍርም፡ በማን፡ እምኘለሁ፡ አውቃ ለሁና። ልቤም፡ ያምናል፡ *አደራ፡ የሰጠኋትን፡ ይጠ ብቅልኝ፡ ዘንድ፡ እንዲችል፡ እስከዚያ፡ ቀን፡ ድረስ። *ም፡ ፬፥ ፰።

፲፫፥ የእውነተኛውን፡ነገር፡ምሳሌ፡ከኔ፡የሰማሃው ን፡ጠብቅ፡በሃይማኖት፡በየሱስ፡ክርስቶስም፡ በሚሆ ን፡ ፍቅር። ፩፥ ጢሞ፡ ፯፥ ፫። ቲቶ፡ ፪፥ ፩።

፲፬፥ መልካሚቱን፡አደራ፡ ጠብቅ፡ በኛ፡ ባደረብን፡ በመንፈስ፡ቅዱስ። ቍ፡ ፲፪፥ ፩፥ ጢሞ፡ ፯፥ ፳።

፲፭፥ ይህነንም፡ ታውቃለህ፡ በእስያ፡ ያሉ፡ ሁሉ፡ ከ ኔ፡እንደ፡ ተመለሱ። ከርሳቸውም፡ ፊጊሉስ፡ ሔርሞ ጌኔስም።

፲፮፥ እግዚአብሔር፡ ለኦኔሲፎርስ፡ቤት፡ ምህረት፡ ይስጥ። ብዙ፡ጊዜ፡ አሳርፎኛልና፡ ሰንሰለቴንም፡ አላ ፈረም።

፲፯፥ ነገር፡ግን፡ *በሮምያ፡ ሳለ፡ ደግሞ፡ ፈለገኝ፡ እስ ኪያገኘኝ፡ ድረስ። የሐዋ፡ ፳፰፥ ፲፯።

፲፰፥ እግዚአብሔር፡ ይሰጠው፡ ከእግዚአብሔር፡ ምህረት፡ያገኝ፡ዘንድ፡በዚያ፡ ቀን። በኤፌሶንም፡ ያገ ለገለኝን፡ ማገልገል፡ ሁሉ፡ አንተ፡ ፈጽመህ፡ ታውቃ ለህ።

## ምዕራፍ፡ ፪፤

፩፥ አንተም፡ ልጄ፡ ሆይ፡ ጽና፡ በየሱስ፡ክርስቶስ፡ ጸጋ።

፪፥ ከኔም፡የሰማሃትን፡በብዙ፡ ምስክር፡ ፊት፡ይህ ችን፡*ለታመኑ፡ሰዎች፡አደራ፡ ስጥ፡ሌሎችን፡ያስተም ሩ፡ ዘንድ፡ ለሚችሉ። ፩፥ ጢሞ፡ ፫፥ ፪።

፫፥ አንተም፡ *መከራ፡ ተቀበል፡ እንደ፡ መልካም፡ ጭፍራ፡ ለየሱስ፡ ክርስቶስ። *ም፡ ፩፥ ፰። ና፡ ፬፥ ፭።

፬፥ ማንም፡ *ጭፍራ፡ሁኖ፡ የዚህን፡ ዓለም፡ ነገር፡ የ ሚያስብ፡ የለምና፡ ጭፍራ፡ ያደረገውን፡ ደስ፡ ያሰኝ፡ ዘንድ። *፩፥ ቆሮ፡ ፱፥ ፳፭።

፭፥ የሚጋደልም፡ ቢሆን፡ አክሊል፡ አይወስድም፡ እንደሚገባው፡ ካልተጋደለ። ም፡ ፬፥ ፰።

፮፥ ለሚደክም፡ አራሽ፡ ይገባዋል፡ አስቀድሞ፡ ከ ፍሬው፡ ይበላ፡ ዘንድ።

፯፥ ነገሬን፡ አስተውል፡ እግዚአብሔርም፡ ጥበብ፡ ይስጥህ፡ በሁሉ።

፰፥ ከሙታን፡*የተነሣውን፡የሱስ፡ክርስቶስን፡አሰ ብ፡እርሱ፡†ከዳዊት፡ ዘር፡የሚሆን፡ እንደ፡ ወንጌሌ። ፩፥ ቆሮ፡ ፲፭፥ ፬፥ ፳። †፪፡ ሳሙ፡ ፯፥ ፲፪።

፱፥ እኔ፡እንደ፡ክፉ፡ አድራጊ፡ *በመታሠር፡ መከራ፡ በተቀበልሁበት። ነገር፡ ግን፡ የእግዚአብሔር፡ †ቃል፡ አትታሠርም። *ኤፌ፡ ፫፥ ፩፥ ፲፫። ፊል፡ ፪፥ ፲፯። †ፊል፡ ፩፥ ፲፪።

፲፥ ስለዚህም፡ በሁሉ፡ እታገሣለሁ፡ ስለ፡ *ተመረ ጡት፡እርሳቸው፡ ደግሞ፡ መዳን፡ ይወስዱ፡ ዘንድ፡ በ የሱስ፡ ክርስቶስ፡ ከዘላለም፡ ክብር፡ጋራ። *ቆላ፡ ፩፥ ፳፬።

፲፩፥ ነገሩ፡እውነት፡ነው። ከርሱ፡ ጋራ፡ *ብንሞት፡ከ ርሱ፡ ጋራ፡ እንኖራለንና። ፪፥ ቆሮ፡ ፬፥ ፲፩። ፩፥ ጴጥ፡ ፬፥ ፲፫።

፲፪፥ *ብንታገሥ፡ ከርሱ፡ ጋራ፡ እንነግሣለን፡ ብንክ ደው፡ እርሱ፡ ደግሞ፡ ይክደናል። *ማቴ፡ ፲፥ ፴፫።

፲፫፥ *ባናምነው፡ እርሱ፡ በእውነቱ፡ †ጸንቶ፡ ይኖራ ል፡ራሱን፡ መካድ፡ አይቻለውም። *ሮሜ፡ ፫፥ ፫። †ዘኁ፡ ፳፫፥ ፲፱።

፲፬፥ ይህን፡ አሳስባቸው፡ በእግዚአብሔርም፡ ፊ ት፡ መስክርበት። *ጥቅም፡ በሌለበት፡ ነገር፡ እንዳይ ጣሉ፡ የሚሰሙት፡ እንዳይታወኩ። *፩፥ ጢሞ፡ ፮፥ ፬። ቲቶ፡ ፫፥ ፱።

፲፭፥ ራስህን፡ ለእግዚአብሔር፡ *የተፈተነ፡ አድርገ ህ፡ታቀም፡ ዘንድ፡ተጠንቀቅ፡ አድራጊም፡ ሁነህ፡ያለ፡ ኃፍረት፡ የውነትን፡ ነገር፡ በቅን፡ የሚቈርጥ። *፩፥ ጢሞ፡ ፬፥ ፮። ቲቶ፡ ፪፥ ፯፥ ፰።

፲፮፥ ከርኩስ፡ ግን፡ ከምናምንም፡ ነገር፡ ራቅ፡ ሰዎ ች፡ በርሳቸው፡ ጥርጣሬ፡ ይጨምራሉና። ፩፥ ጢሞ፡ ፬፥ ፯።

፲፯፥ ነገራቸውም፡እንደሚባላ፡ጭንኩር፡ነው። *ከ ርሳቸውም፡ ሔሜኔዎስ፡ ፊሌጦስም። ፩፥ ጢሞ፡ ፩፥ ፳።

፲፰፥ እሌህ፡ከውነት፡ ጠፉ። ትንሣኤ፡ አለፈች፡ ይ ላሉና፡ የሌሎችንም፡ ሃይማኖት፡ አወኩ።

፲፱፥ ነገር፡ ግን፡ የጸናው፡ የእግዚአብሔር፡ መሠረ ት፡ጸንቶ፡ቁሞዋል። በላዩም፡ ይህ፡ ማሕተም፡ አለበ ት።*እግዚአብሔር፡ ለርሱ፡ የሆኑትን፡ ያውቃል። በክ ርስቶስ፡ ስምም፡ የሚጸራ፡ ሁሉ፡ ከግፍ፡ ይራቅ። *ማቴ፡ ፯፥ ፳፫። ዮሐ፡ ፲፥ ፲፬።

፳፥ ነገር፡ግን፡በታላቅ፡ቤት፡ የወርቅና፡ የብር፡ እቃ፡ ብቻ፡ የሚኖርበት፡ አይደለም፡ የንጨትም፡ የሸክላ ም፡ እንጂ። እንዲም፡ ለክብር፡ ነው፡ እንዲም፡ ለነ ውር።

፳፩፥ አሁንም፡ ሰው፡ ራሱን፡ ከዚህ፡ ሁሉ፡ ነገር፡ ቢ ያነጻ፡ የክብር፡እቃ፡ይሆናል፡ የተቀደሰ፡ ለጌታው፡ ማ ገልገል፡ የሚበቃ፡ እርሱም፡ ለመልካም፡ ነገር፡ ሁሉ፡ የተዘጋጀ።

፳፪፥ ከብላቴንነትም፡ፍትወት፡ ራቅ። *ጽድቅንና፡ ሃይማኖትንም፡ ፍቅርንም፡ ሰላምንም፡ ለመሻት፡ ሩ ጥ፡ የጌታን፡ ስም፡ በንጹሕ፡ ልቡና፡ ከሚጸሩ፡ ጋራ። *፩፥ ጢሞ፡ ፮፥ ፲፩።

፳፫፥ ከስንፍና፡ *ክርክር፡ ግን፡ ተግሣጽ፡ የሌላት፡ ተጠንቀቅ፡ መጸላት፡ እንድትወልድ፡ ታውቃለህና። *፩፥ ጢሞ፡ ፬፥ ፯።

፳፬፤ የእግዚአብሔርም፡ *ባርያ፡ እንዲገባው፡ ሊ
ጣላ፡ ዘንድ። ነገር፡ ግን፡ ለሁሉ፡ ወደኛ፡ ይሁን፡ አስተ
ማሪ፡ ታጋሽም። *ቲቶ፡ ፩፤ ፯።
፳፭፤ ጸላቶችን፡ በየውሃት፡ የሚገሥጽ፡ ምናልባ
ት፡እግዚአብሔር፡ ንስሐ፡ ይሰጣቸው፡ እንደሆን፡ እ
ውነትን፡ ለማወቅ።
፳፮፤ ከሰይጣንም፡ ወጥመድ፡ ይድኑ፡ ዘንድ። እር
ሱ፡ፈጽሞ፡አጽምድዋቸዋልና፡ ወደ፡ ፈቃዱ፡ ለማሰ
ከተል።

ምዕራፍ፡ ፫፡

፩፤ ይህንም፡ ዕወቅ፡ በኋላ፡ ዘመን፡ ክፉ፡ ጊዜ፡ እን
ዲሆን። ፩፡ ጢሞ፡ ፬፡ ፩።
፪፤ ሰዎች፡ ራሳቸውን፡ የሚወዱ፡ ይሆኑበታልና፡
*ብር፡ ወዳጆች፡ ተመኳች፡ ዕቡዮች፡ ተሳደቦች፡ ላባቶ
ቻቸው፡ የማይታዘዙ፡ የማያመሰግኑ፡ ያልተቀደሱ።
*ሮሜ፡ ፩፡ ፳፱፡—፴፩።
፫፤ ፍቅር፡ የሌላቸው፡መሐላ፡ የሚያፈርሱ፡ ሐሜ
ተኞች፡ራሳቸውን፡ ከክፉ፡ የማይጠብቁ፡ ደስ፡ የማያ
ሰኙ፡ መልካም፡ የማይወዱ።
፬፤ በደለኞች፡ችኩሎች፡ ትቢተኞች፡ *ተድላ፡ የሚ
ወዱ፡እግዚአብሔርን፡ ከመውደድ፡ ይልቅ።
*ፊል፡ ፫፡ ፲፱።
፭፤ በርሳቸውም፡ የአምልኮት፡ መልክ፡ አለችባቸ
ው፡ ኃይልዋን፡ግን፡ የካዱ፡ ናቸው። እሌህንም፡ ሽሻ
ቸው። ማቴ፡ ፯፤ ፲፭፡ ፳፩። ቲቶ፡ ፩፡ ፲፮።
፮፤ ከለዚህ፡ *እሉና፡ ቤት፡ ለቤት፡ የሚዞሩ፡ ኃጢ
አት፡ የመላባቸውንም፡ ሴቶች፡ ይነታሉ። ወደ፡ ተላ
ለፈች፡ፍትወት፡የምቀደይደሙ። *ማቴ፡ ፳፫፡ ፲፬።
ቲቶ፡ ፩፡ ፲፩።
፯፤ ሁልጊዜም፡ ይማራሉ፡ ወደ፡ እውነትም፡ እው
ቀት፡ለመምጣት፡ከቶ፡ አይችሉም።
፰፤ ኢያኔስና፡ ኢያምብሬስም፡ *ሙሴን፡ እንደ፡
ተቃወሙት፡ እንደሁ፡ እሌህ፡ እውነትን፡ ይቃወማ
ሉ። አእምሮዋቸው፡ የጠፋ፡ ሰዎች፡ ከሃይማኖት፡ የ
ወጡ። *ዘፀአ፡ ፯፡ ፲፩፡ ፲፪።
፱፤ ነገር፡ ግን፡ ፈቀቅ፡ አይሉም። ስንፍናቸው፡ በሁ
ሉ፡ዘንድ፡ ትገለጣለችና፡ የለዚያ፡ ስንፍና፡ ደግሞ፡ እ
ንደ፡ተገለጠች።
፲፤ አንተ፡ ግን፡ ፈጽመህ፡ ትምህርቴን፡ ተከተልህ፡
አካሔዴንም፡ ፈቃዴንም፡ ሃይማኖቴንም፡ መቈየ
ቴንም፡ ፍቅሬንም፡ ትዕግሥቴንም።
፲፩፤ መሳደዴንም፡ *መከራዬንም፡ በአንጾኪያ፡ የ
ደረሰችብኝን፡ በኢቆኒዮምም፡ በልስትራም። ምን፡
ያህልስ፡ግድል፡ተጋደልሁ፡ ከዚህም፡ ሁሉ፡ እግዚአብ
ሔር፡አደነኝ። *የሐዋ፡ ፲፫፡ ፶፡ ፲፬፡ ፪፡ ፲፱፡ ፳፪።
መዝ፡ ፴፬፡ ፲፱።
፲፪፤የሱስ፡ክርስቶስንም፡በማምለክ፡ደናር፡ዘንድ፡
የሚወዱ፡ ሁሉ፡ ይሳደዳሉ። ማቴ፡ ፲፮፡ ፳፬።
የሐዋ፡ ፲፬፡ ፳፪።

፲፫፤ ክፉ፡ ሰዎች፡ ግን፡ አሳቶችም፡ ወደ፡ በለጠ፡ ክ
ፋት፡ ይደርሳሉ፡ ሲያጠፉ፡ ሲጠፉም።
፩፡ ጢሞ፡ ፬፡ ፩።
፲፬፤ አንተ፡ ግን፡ ጽና፡ በተማርኸው፡ ባወቅኸው፡
ም። ከማን፡ ተማርህ፡ ታውቃለህና። ም፡ ፪፡ ፪።
፲፭፤ ከሕፃንነትህ፡ ጀምረህ፡ የተቀደሱትን፡ መጽ
ሐፍ፡ ተምረሃልና፡ ለደህንነት፡ ታስተምርህ፡ ዘንድ፡
የምትችል፡ በየሱስ፡ ክርስቶስ፡ ሃይማኖት።
ዮሐ፡ ፭፡ ፴፱።
፲፮፤ መጽሐፍ፡ *ሁሉ፡ በእግዚአብሔር፡ መንፈስ፡
ተጻፈች፡ ለትምህርትም፡ ትረባለች፡ለዘለፋም፡ ለተ
ግሣጽም፡ ለማስተማርም፡ በጽድቅ።
፪፡ ጴጥ፡ ፩፡ ፲፱፡—፳፩።
፲፯፤ የእግዚአብሔር፡ *ሰው፡ ፍጹም፡ ይሆን፡ ዘን
ድ፡ ለመልካም፡ ስራ፡ †ሁሉ፡ የተዘጋጀ።
*፩፡ ጢሞ፡ ፮፡ ፲፩። †ም፡ ፪፡ ፳፩።

ምዕራፍ፡ ፬፡

፩፤ አሁንም፡ እኔ፡ አስመሰክርብሃለሁ፡ በእግዚአ
ብሔር፡ ፊት፡ በጌታም፡ በየሱስ፡ክርስቶስ፡ በሕያዋን
ና፡ በሙታን፡ የሚፈርድ፡ በመገለጡ፡ በመንግሥቱ
ም፡ጊዜ። *የሐዋ፡ ፲፡ ፵፪። ፪፡ ተሰ፡ ፩፡ ፯፡ ፰።
፩፡ ጴጥ፡ ፬፡ ፭።
፪፤ በነገር፡ *አስተምር፡ አንተ፡ ባለህበትም፡ ጽና፡
አየተጋደልህ፡ በጊዜው፡ ያለ፡ ጊዜውም። ሰነፎችን፡
†ዘልፍ፡ ገሥጽ፡ **በርኅራኄ፡ ሁሉ፡በትምህርትም።
*ኢሳ፡ ፶፰፡ ፩። †ቲቶ፡ ፩፡ ፱፡ ፲። **ም፡ ፪፡ ፳፬።
፫፡ ፲፡ ፲፯።
፫፤ እውነተኛ፡ ትምህርት፡ *የማይቀበሉበት፡ጊዜ፡
ይሆናልና፡ ነገር፡ ግን፡ እርሳቸው፡ በፈቃዳቸው፡ ለራሳ
ቸው፡ መምህራንን፡ ያከማቻሉ፡ ጆሮዋቸውን፡ ደስ፡
የሚያሰኙትን። *፩፡ ጢሞ፡ ፩፡ ፲፫። ፭፡ ፬፡ ፩።
፬፤ ጆሮዋቸውንም፡ ይመልሳሉ፡እውነትን፡ ከመስ
ማት፡ ወደ፡ ተረትም፡ ይመለሳሉ። ፩፡ ጢሞ፡ ፬፡ ፯።
፪፡ ተሰ፡ ፪፡ ፲፩።
፭፤ አንተ፡ ግን፡ በሁሉ፡ ንቃ። መከራ፡ ተቀበል። የ
ወንጌላዊን፡ ስራ፡ ስራ። መልክትህን፡ ፍጸም።
የሐዋ፡ ፳፩፡ ፰።
፮፤ እኔ፡ እነሆ፡እሠዋለሁና፡ የመሰናበቴም፡ ጊዜ፡
ደርሶዋል። ፊል፡ ፪፡ ፲፯።
፯፤ መልካሙን፡ ገድል፡ *ተጋደልሁ፡ †ሩጫዬንም፡
ጨረስሁ፡ ሃይማኖትንም፡ ጠበቅሁ።
፩*፡ ቆር፡ ፱፡ ፳፭። ፩፡ ጢሞ፡ ፮፡ ፲፪። †ፊል፡ ፫፡ ፲፬።
፰፤ እንግዲህም፡ የጽድቅ፡ *አክሊል፡ ተዘጋጅቶል
ኛል፡ እግዚአብሔር፡ የሚሰጠኝ፡ በዚያች፡ ቀን፡ ያ፡
ጻድቅ፡ ፈራጁ። ለኔም፡ ብቻ፡ አይደለም፡ መገለጡ
ን፡ ለሚወዱ፡ ሁሉ፡ እንጂ፡ ደግሞ። *ም፡ ፪፡ ፭።
፩፡ ጴጥ፡ ፭፡ ፬። ያዕ፡ ፩፡ ፲፪። ራእ፡ ፪፡ ፲።
፱፤ ተሉ፡ ወደኔ፡ ትመጣ፡ ዘንድ፡ ፍጠን። ቈ፡ ፳፩።

፲፡ *ደማስ፡ ትቶኛልና፡ ይህንም፡ †ዓለም፡ ወድዋልና፡ ወደ፡ ተሰሎንቄም፡ ሔደ። ቄሬስኪንስ፡ ወደ፡ ገላትያ፡ ቲቶስም፡ ወደ፡ ደልማጥያ። *ቈላ፡ ፬፡ ፲፬፡፡ †ም፡ ፩፡ ፲፭፡፡

፲፩፡ ሉቃስ፡ *ብቻ፡ ከኔ፡ ጋራ፡ ነው። ማርቆስን፡ ካንተ፡ ጋራ፡ ይዘኸው፡ ና፡ ለማገልገል፡ ይረባኛልና። *የሐዋ፡ ፲፭፡ ፴፯፡፡ ቈላ፡ ፬፡ ፲፡፡

፲፪፡ ቲቂኮስን፡ ግን፡ ወደ፡ ኤፌሶን፡ ላክሁ። የሐዋ፡ ፳፡ ፬፡፡ ኤፌ፡ ፮፡ ፳፩፡፡ ቈላ፡ ፬፡ ፯፡፡

፲፫፡ በጠራዋስ፡ ከከርጰስ፡ ዘንድ፡ የተውኋትን፡ ቡርኖስ፡ በመጣህ፡ ጊዜ፡ ይዘሃት፡ ና። መጻሕፍቱንም፡ ይልቁንም፡ በራናውን።

፲፬፡ እስክንድሮስ፡ የናስ፡ *አንጥረኛ፡ እጅግ፡ ክፉ፡ አደረገብኝ፡ *እግዚአብሔር፡ ይምልስለት፡ እንደ፡ ስራው። *፩፡ ጢሞ፡ ፩፡ ፳፡፡ †፪፡ ሳሙኤ፡ ፫፡ ፴፱፡፡ መዝ፡ ፳፰፡ ፬፡፡

፲፭፡ አንተም፡ ደግሞ፡ ከርሱ፡ ተጠንቀቅ፡ ነገራችንን፡ እጅግ፡ ተጠናውትዋልና።

፲፮፡ በቀደመው፡ ክርክሬ፡ ከኔ፡ ጋራ፡ ማንም፡ አልነበረም፡ ነገር፡ ግን፡ *ሁሉ፡ ተውኝ። ያነን፡ ኃጢአት፡ እግዚአብሔር፡ አያድርግባቸው። *ዮሐ፡ ፲፮፡ ፴፪፡፡ ፪፡ ጢሞ፡ ፩፡ ፲፭፡፡

፲፯፡ ነገር፡ግን፡እግዚአብሔር፡ *ቀመልኝ፡ረደኝም፡ የወንጌል፡ ትምህርት፡ በኔ፡ ትፈጸም፡ ዘንድ፡አሕዛብም፡ ሁሉ፡ ይሰሙ፡ ዘንድ። †ከአንበሳም፡ አፍ፡ ዳንሁ። *የሐዋ፡ ፳፫፡፲፩፡ ና፡ ፳፯፡፳፫፡፡ †የሐዋ፡ ፲፪፡፲፩፡፡

፲፰፡ እግዚአብሔርም፡ ከክፉ፡ ነገር፡ ሁሉ፡ ያወጣኛል፡ ወደ፡ ሰማያዊም፡መንግሥቱ፡አገባ፡ዘንድ፡ ያድነኛል፡ ለርሱም፡ *ምስጋና፡ ይገባዋል፡ ለዘላለም፡ አሜን። *ሮሜ፡ ፲፮፡ ፳፯፡፡ ገላት፡ ፩፡ ፭፡፡ ፩፡ ጢሞ፡ ፮፡ ፲፮፡፡

፲፱፡ ለጵሪስካና፡ *ለአኪላ፡ ሰላም፡ ስጥ፡ †ለኦኔሲፎርስም፡ ቤት። *የሐዋ፡ ፲፰፡ ፪፡፡ ሮሜ፡ ፲፮፡ ፫፡፡ †ም፡ ፩፡ ፲፮፡፡

፳፡ *ኤራስጦስ፡ በቆሮንቶስ፡ ቀረ፡ †ጠረፊሞስን፡ ግን፡ በሚሊጦስ፡ ታሞ፡ ተውሁት። *የሐዋ፡ ፲፱፡ ፳፪፡፡ †የሐዋ፡ ፳፡ ፬፡ ና፡ ፳፩፡ ፳፱፡፡

፳፩፡ ፍጠን፡ እንድትመጣ፡ ከክረምት፡ በፊት። እንደት፡ ነህ፡ ይልሃል፡ኤዎቡሉስ፡ ጱዴንስም፡ ሊኖስም፡ አክሎዲያም፡ ወንድሞችም፡ ሁሉ።

፳፪፡ ጌታ፡ የሱስ፡ ክርስቶስ፡ ከመንፈስህ፡ ጋራ፡ ይሁን። ጸጋ፡ ከላንተ፡ ጋራ፡ ይሁን። አሜን። ቲቶ፡ ፫፡ ፲፭፡፡

ተፈጸመች፡ ሁለተኛይቱ፡ መልእክት፡ ወደ፡ ጢሞቴዎስ፡ አስቀድሞ፡ በጳጳስነት፡ የተሾመ፡ በኤፌሶን፡ ሰዎች፡ ቤተ፡ ክርስቲያን፡ ላይ። በሮምያ፡ ተጻፈች፡ ጳውሎስ፡ በቄሣር፡ በኔሮን፡ ፊት፡ ሁለተኛ፡ በቆመ፡ ጊዜ።

# የሐዋርያ ፡ የጳውሎስ ፡ መልእክት ፡ ወደ ፡ ቲቶስ።

## ምዕራፍ፡ ፩፡

፩፡ ከጳውሎስ፡ ከእግዚአብሔር፡ ባርያ፡ ከየሱስ፡ ክርስቶስም፡ ሐዋርያ። እግዚአብሔር፡ በመረጣቸው፡ ሃይማኖት፡ እውነትንም፡ በማወቅ፡ እንደ፡ መልካም፡ አምልኮ፡ ያለች።

፪፡ ለዘላለም፡ ሕይወት፡ ተስፋ፡ በማድረግ። አስት፡ይናገር፡ ዘንድ፡ የማይችል፡አምላክ፡ተስፋ፡ የሰጠባት፡ዓለም፡ሳይፈጠር።

፫፡ ቃሉንም፡ *ገለጠ፡ በጊዜው፡ በስብከት፡እኔ፡ †በታመንሁባት፡ በመድኃኒታችን፡ በአምላክ፡ትእዛዝ። *ኤፌ፡ ፩፡ ፱፡ ፲፡፡ †፩፡ ጢሞ፡ ፩፡ ፩—፲፩፡፡

፬፡ ወደ፡ ቲቶስ፡ ወደ፡ እውነተኛ፡ *ልጄ፡ በሃይማኖት፡ አንድነት። ጸጋ፡ ምህረትም፡ ሰላምም፡ ከእግዚአብሔር፡ አብ፡ ከመድኃኒታችንም፡ ከጌታ፡ ከየሱስ፡ ክርስቶስ። *፩፡ ጢሞ፡ ፩፡ ፪፡፡

፭፡ ስለዚህ፡ በቀሬጢስ፡ ተውሁህ፡ የጐደለውን፡ ሁሉ፡ ታቀም፡ ዘንድ፡ ቀሳውስትም፡ ትሾም፡ ዘንድ፡ በያገሩ፡ እንዳዘዝሁህ።

፮፡ ሰውም፡ ነውር፡ የሌለበት፡ ቢሆን። ያንዲት፡ ምሽትም፡ ባል፡ ቢኖር፡ ያመኑም፡ ልጆች፡ ቢሆኑለት፡ በርኩሰት፡ የማይኖሩ፡ የማይታዘዙም፡ አይደሉ። ፩፡ ጢሞ፡ ፫፡ ፪፡፡ ፩፡ ጴጥ፡ ፭፡ ፫፡፡

፯፡ ለጳጳስ፡ ይገባዋልና፡ ነውር፡ የሌለበት፡ ይሆን፡ ዘንድ፡ እንደ፡ *እግዚአብሔር፡ መጋቢ። ፈቃዱን፡ የማይከተል፡ የማይቈጣ፡ የጸጅም፡ ዘካሪ፡ ያይደለ፡ የማይመታም፡ የረከሰውንም፡ ረብ፡ የማይሻ። *፩፡ ቆሮ፡ ፬፡ ፩፡፡ ፪፡ ጢሞ፡ ፪፡ ፳፬፡፡

፰፡ እንግዳችንም፡ የሚወድ፡ መልካምን፡ ነገር፡ የሚወድ፡ ትሑት፡ ጻድቅ። ቅዱስ። ራሱን፡ የጠበቀ።

፱፡ በታመነ፡ ነገር፡ *የነቃ፡ይሁን፡ እንደ፡ ትምህርቱ፡ ሌሎችን፡ ደግሞ፡ በውነተኛ፡ ትምህርት፡ ለማጽናት፡ ይችል፡ ዘንድ፡ የሚተላለፉትንም፡ ለመገሠፅ። *፪፡ ተሰ፡ ፪፡ ፲፭፡፡

፲፡ ብዙ፡ ሰዎች፡ አይታዘዙምና፡ ነገራቸውም፡ ከንቱ፡ ነውና፡ የሰውንም፡ ልብ፡ያጠፋሉ፡ይልቁንም፡ የግዝረት፡ ሰዎች።

፲፩፡ አሊያ፡አፋቸውን፡*ለመዝጋት፡የሚገባቸው።

ተቤቱን፡ ሁሉ፡ የሚያጠፉ፡ የማይገባውን፡ ሲያስተ ምሩ። የረከሰውንም፡ ረብ፡ ለመጠቀም።

*ማቴ፡ ፳፪፡ ፴፬፡፡ †፪፡ ጢሞ፡ ፫፡ ፮፡፡

፲፪፡ከርሳቸው፡አንዱ፡ይላል፡እርሱም፡ነቢያቸው። የቀሬጥስ፡ ሰዎች፡ አስተኞች፡ ሁለጊዜ። የከፉም፡ አ ራዊት። ሆዳሞች።

፲፫፡ ይህች፡ ምስክር፡ እውነተኛ፡ናት። ስለዚህም፡ ጽኑ፡ *ዘለፋ፡ ዝለፋቸው፡ በሃይማኖት፡ እንዲጸኑ።

፪፡ ጢሞ፡ ፬፡ ፪፡—፯፡፡

፲፬፡ ወደ፡ አይሁድም፡ ጨወታ፡ እንደያደምጹ፡ ከውነት፡ ወደ፡ ወጡም፡ ወደ፡ ሰዎች፡ ትእዛዝ።

፩፡ ጢሞ፡ ፬፡ ፯፡፡

፲፭፡ *ለንጹሓን፡ ነገር፡ ሁሉ፡ ንጹሕ፡ ነውና። ለርኩ ሳን፡ግን፡ለማያምኑም፡ንጹሕ፡የለባቸውም። እርሳ ቸው፡ ልባቸው፡ ሕሊናቸውም፡ ርኩስ፡ ነው፡ እንጂ።

*ማቴ፡ ፲፭፡ ፲፩፡፡ ሮሜ፡ ፲፬፡ ፳፡፡

፲፮፡ እግዚአብሔርን፡እንዲያውቁ፡ ይገለጣሉ፡ በ ስራቸው፡ ግን፡ ይክዱታል። እርሳቸውም፡ የተጠሉ፡ ያልታዘዙም፡በመልካምም፡ስራ፡ሁሉ፡ያልተፈተኑ።

፪፡ ጢሞ፡ ፫፡ ፭፡፡

ምዕራፍ፡ ፪፡

፩፡ አንተ፡ ግን፡ *ተናገር፡ ለእውነተኛ፡ ትምህርት፡ እንዲገባ። ፩፡ ጢሞ፡ ፮፡ ፫፡፡ ፪፡ ጢሞ፡ ፩፡ ፲፫፡፡

፪፡ሽማግሎች፡የነቁ፡ይሆኑ፡ዘንድ፡እንዲገባቸው። ራሳቸውን፡ የሚጠብቁ። አዋቆች፡ በሃይማኖት፡ የበ ረቱ፡ በፍቅር፡ በትዕግሥት። ፩፡ ጢሞ፡ ፭፡ ፩፡፡

፫፡ እንደሁም፡ ሽማግሊት፡ ሴቶች፡ በመልካም፡ ይሁኑ፡ ለንጽሕና፡ እንዲገባ። ሐሜተኞችም፡ አይሁ ኑ፡ ብዙ፡ጸጅም፡ለመጠጣት፡ የተገዙ። ነገር፡ ግን፡ መ ልካም፡ ነገር፡ የሚያሰተምሩ። ፩፡ ጢሞ፡ ፫፡ ፲፩፡፡

፬፡ ብላቴናዪቱን፡ ሴቶች፡ ያስተምሩ፡ ዘንድ፡ ባሎ ቻቸውን፡ እንዲወዱ፡ልጆቻቸውንም፡ የሚወዱ፡ እ ንዲሆኑ።

፭፡ የሚጠነቀቁ፡ ንጹሓንም፡ እንዲሆኑ። ቤታቸ ውን፡ በመልካም፡የሚሰሩ። በጎች። *ለባሎቻቸው፡ የሚገዙ። የእግዚአብሔርን፡ ነገር፡ ማንም፡ እንደይ ሰድብ። *ኤፌ፡ ፭፡ ፳፪፡፡

፮፡ ጐበዛዝቱም፡ ደግሞ፡ በልክ፡ ይኖሩ፡ ዘንድ፡ ም ክራቸው።

፯፡ ራስህንም፡ ለመልካም፡ ነገር፡ ሁሉ፡ ምሳሌ፡ አ ድርግላቸው። ትምህርትህ፡ የማያጠፋ፡ ይሆን።

፩፡ ጢሞ፡ ፬፡ ፲፪፡፡ ፩፡ ጴጥ፡ ፭፡ ፫፡፡

፰፡ በጥበብም፡ ተናገር፡ በመልካም፡ ነገር፡ ነውር፡ የሌለበት። ማንም፡ የሚጣላ፡ ቢሆን፡ ያፍር፡ ዘንድ፡ ክፉ፡ ነገር፡ ሰለላንት፡ ይል፡ ዘንድ፡ ባይችል።

፩፡ ጴጥ፡ ፪፡ ፲፭፡፡

፱፡ ባሮች፡ ለጌቶቻቸው፡ ይገዙ፡ በሁሉ፡ደስም፡ያሰ ኙዋቸው። ኤፌ፡ ፮፡ ፭፡፡ ፩፡ ጢሞ፡ ፮፡ ፩፡፡

፩፡ ጴጥ፡ ፪፡ ፲፰፡፡

፲፡ እምቢተኞችም፡ አይሁኑ፡ሌቦችም፡ሃይማኖታ ቸውን፡በምግባራቸው፡ ሁሉ፡ይግለጡ፡እንጂ። የመ ድኃኒታችነን፡ የእግዚአብሔርን፡ ትምህርት፡ በሁሉ፡ ያስጌጹ፡ ዘንድ። ም፡ ፩፡ ፫፡፡

፲፩፡ የእግዚአብሔር፡ ጸጋ፡ *የምታድን፡ ለሰው፡ ሁ ሉ፡ ተገልጣለችና። *ም፡ ፫፡ ፬፡፡ ፩፡ ዮሐ፡ ፬፡ ፱፡፡

፲፪፡ ልታስተምረነ፡መጠራጠርን፡ዓለማዊቱንም፡ ፍትወት፡ ሁሉ፡ እንክድ፡ ዘንድ። በጥበብና፡ በየውሃ ትም፡ በጽድቅም፡ *በመልካምም፡ አምልኮ፡በዚህ፡ ዓለም፡ እንኖር፡ ዘንድ። *ኤፌ፡ ፩፡ ፬፡፡

፲፫፡ የተመሰገነውንም፡ *ተስፋ፡ ስንጠብቅ፡ የታላ ቁ፡ አምላክ፡ የመድኃኒታችንም፡ የየሱስ፡ ክርስቶስ፡ ክብር፡ መገለጥ። *፩፡ ቆር፡ ፩፡ ፯፡፡ ፊል፡ ፫፡ ፳፡፡

፲፬፡ *ራሱን፡ ስለኛ፡ የለወጠ፡ ከኃጢአት፡ ሁሉ፡ ያ ድነነ፡ ዘንድ። ለራሱም፡ የተመረጸ፡ ወገን፡ ያነጸ፡ ዘን ድ፡ †ለመልካም፡ ነገር፡ የሚቀና። *ገላት፡ ፩፡ ፬፡፡

፩፡ ጢሞ፡ ፪፡ ፮፡፡ †ኤፌ፡ ፪፡ ፲፡፡

፲፭፡ በዚህ፡ ተናገር፡አጽናም፡በተሰጠህ፡ሥልጣነን፡ ሁሉ፡ አስተምርና፡ ገሥጽ፡ ማንም፡ አይናቅህ።

፩፡ ጢሞ፡ ፬፡ ፲፪፡፡

ምዕራፍ፡ ፫፡

፩፡ አሳስባቸው፡ ለነግሥታት፡ ለሠልጣናትም፡ ይገ ዙ፡ ዘንድ፡ ላለቆች፡ እንዲታዘዙ፡ መልካም፡ ነገር፡ ሁ ሉ፡ ለማድረግ፡ እንዲዘጋጁ። ፩፡ ጴጥ፡ ፪፡ ፲፫፡፡

፪፡ ማነን፡ እንዳይሰድቡ፡ የሚጣሉ፡ እንዳይሆኑ፡ የዋሃን፡ እንጂ። የውሃቱንም፡ ሁሉ፡ ለሰው፡ሁሉ፡ ይ ግለጡ። ፊል፡ ፬፡ ፭፡፡

፫፡ እኛ፡ ቀድሞ፡ ያለውቀት፡ ነበርነና፡ ያለ፡ መታዘ ዝም፡የጠፋነም፡ ነበርነ። ለተላለፈች፡ፈቃዶችን፡ ባሮ ች። በቅናት፡ በክፋም፡ የምንሔድ። የተጠላነ፡ እር ሱ፡ በርሳችነም፡ የምንጣለ። ፩፡ ቆር፡ ፮፡ ፲፩፡፡

ኤፌ፡ ፪፡ ፪፡፡ ና፡ ፬፡ ፲፯፡ ፲፰፡፡

፬፡ የእግዚአብሔር፡ ግን፡ የመድኃኒታችን፡ቸርነት፡ ምሀረቱም፡ በተገለጠ፡ ጊዜ። ም፡ ፪፡ ፲፩፡፡

፭፡ ጽድቅ፡ *በማድረግ፡ ያደረግናት፡አይደለም፡ በ ምሀረቱ፡ አደነነ፡ እንጂ። †ከሁለተኛ፡ ልደቱ፡ ጥም ቀት፡ በመንፈስ፡ ቅዱስም፡ መታደስ።

ኤፌ፡ ፪፡ ፰፡ ፱፡፡ †ዮሐ፡ ፫፡ ፭፡፡ ኤፌ፡ ፭፡ ፳፮፡፡

፮፡ በኛ፡ በመለገሰ፡ *ያፈሰሰው፡ በመድኃኒታችን፡ በየሱስ፡ክርስቶስ። *ኢዮብ፡ ፫፡ ፩፡፡ ሕዝ፡ ፴፯፡ ፴፭፡፡

፯፡ በጸጋው፡ *እንጸድቅ፡ ዘንድ፡ በተስፋም፡ የዘላ ለምን፡ ሕይወት፡ †ወራሾች፡ እንሆን፡ ዘንድ።

ሮሜ፡ ፭፡ ፩፡፡ †ሮሜ፡ ፰፡ ፲፯፡፡

፰፡ ይህ፡ ነገር፡ እውነት፡ ነው፡በዚህም፡ ነገር፡ትጸና፡ ዘንድ፡ እወደለሁ፡ በእግዚአብሔር፡ ያመኑ፡ ሁሉ፡ መልካም፡ ስራ፡ ለመስራት፡ ያስቡ፡ ዘንድ። ይህች፡ ያማረች፡ ለሰውም፡ የምትረባ፡ ናትና። ቍ፡ ፲፬፡፡

፱፡ የስንፍናን፡ ጥያቄ፡ግን፡ የነገርንም፡ ምላሽ፡ ጽል

ንም፡ በሕግም፡ መከራከርን፡ ራቃት። የማትረባ፡ ከንቱም፡ ናትና። ፩፡ ጢሞ፡ ፬፡ ፯።

፲፡ *ከሐዲን፡ ሰው፡ †አንደግዜ፡ ሁለተግዜም፡ ከመከርኸው፡ በኋላ፡ ባይመከርም፡ ተወው።
†፪፡ ዮሐ፡ ፲። †ማቴ፡ ፲፰፡ ፲፭።

፲፩፡ እንዲህ፡ ያለው፡ እርሱ፡ ጠማማ፡ ኃጢአተኛም፡ ነውና። እርሱም፡ በራሱ፡ የሚያስፈርድ፡ ይሆናል።
፩፡ ጢሞ፡ ፮፡ ፬፡ ፭።

፲፪፡ አርጤማስን፡ ወይም፡ ቲኪቆስን፡ በላክሁብህ፡ ጊዜ፡ ፈጥነህ፡ ወደኔ፡ ና፡ ወደ፡ ኒቆጶሊስ፡ አገር፡ ከዚያ፡ እክርም፡ ዘንድ፡ አስቢያለሁና። ፪፡ ጢሞ፡ ፬፡ ፲፪።

፲፫፡ ዜናስን፡ ሕጋዊን፡ *አጵሎስንም፡ ተሎ፡ ስደዳቸው፡ አንዳችም፡ የጐደላቸው፡ አይሁን።
*የሐዋ፡ ፲፰፡ ፳፬። ፩፡ ቆሮ፡ ፩፡ ፲፪።

፲፬፡ ወዳጆቻችንም፡ ደግሞ፡ ይማሩ፡ *መልካም፡ ነገር፡ ለማድረግ፡ እንዲያፀቡ፡ የምታገውንም፡ ነገር፡ ያጸኑ፡ ዘንድ፡ †ፍሬ፡ የሌለባቸው፡ እንዳይሆኑ።
*ኤፌ፡ ፪፡ ፲። †ማቴ፡ ፯፡ ፲፱።

፲፭፡ ከኔ፡ ጋራ፡ ያሉት፡ ሁሉ፡ እንዴት፡ ነህ፡ ይሉሃል። በሃይማኖት፡ የሚወዱነን፡ እንዴት፡ ናችሁ፡ በል። ጸጋ፡ ከሁላችሁ፡ ጋራ፡ ይሁን። አሜን። ገላት፡ ፭፡ ፮።

ወደ፡ ቲቶስ፡ ተጻፈች፡ ከጳጳሳት፡ አስቀድሞ፡ የተሾመ፡ በቀሬጢስ፡ ሰዎች፡ ቤተ፡ ክርስቲያን፡ ላይ፡ ከኒቆጶሊስ፡ ከመቄዶንያ፡ አገር።

# የሐዋርያ ፡ የጳውሎስ ፡ መልእክት ፡ ወደ ፡ ፊልሞን።

፩፡ ከጳውሎስ፡ ከየሱስ፡ ክርስቶስ፡ *እሥር፡ ከጢሞቴዎስም፡ ከወንድማችን። ወደ፡ ፊልሞን፡ ወዳጃችን፡ አጋዣችንም፡ በማድረግ። *ኤፌ፡ ፫፡ ፩።

፪፡ ወደ፡ ተወደደችም፡ ወደ፡ አጲያ። ወደ፡ አርኪጶስም፡ ከኛ፡ ጋራ፡ የሚጋደል። በቤትህም፡ ወዳለች፡ ቤተ፡ ክርስቲያን። ቆላ፡ ፬፡ ፲፯።

፫፡ ጸጋ፡ ለላንት፡ ሰላምም፡ ካባታችን፡ ከእግዚአብሔር፡ ከጌታችንም፡ ከየሱስ፡ ክርስቶስ።
ሮሜ፡ ፩፡ ፯።

፬፡ አምላኬን፡ አመሰግናለሁ፡ ሁለግዜ፡ በጸሎቴም፡ ሁሉ፡ አስብሃለሁ።

፭፡ ፍቅርህን፡ ሃይማኖትህንም፡ ከሰማሁ፡ ጀምሬ፡ ለየሱስ፡ ክርስቶስ፡ ለቅዱሳንም፡ ሁሉ፡ ያለችህን።

፮፡ የሃይማኖትህ፡ አንድነት፡ የምታደርግ፡ ትሆን፡ ዘንድ፡ መልካም፡ ነገር፡ ሁሉ፡ በማስታወቅ፡ በላንት፡ ያለችውን፡ በክርስቶስ፡ የሱስ። ፊል፡ ፩፡ ፱።

፯፡ አጅግ፡ ደስታ፡ አለንና፡ መጽናናትም፡ በፍቅርህ። የቅዱሳን፡ ልብ፡ ባንተ፡ አርፈዋልና፡ ወንድሜ፡ ሆይ። ፪፡ ቆሮ፡ ፯፡ ፬።

፰፡ ስለዚህም፡ በክርስቶስ፡ አጅግ፡ ድፍረት፡ ቢሆንልኝ፡ በሚገባው፡ አዝህ፡ ዘንድ።

፱፡ ስለ፡ ፍቅር፡ ግን፡ ይልቁን፡ እለምንሃለሁ። እንደዚህ፡ ያለሁ፡ ትሆን፡ እኔ፡ ጳውሎስ፡ እኔ፡ ሽማግሌ፡ ዛሬም፡ የታሠርሁ፡ ስለ፡ የሱስ፡ ክርስቶስ።

፲፡ እለምንሃለሁ፡ ስለ፡ *ልጄ፡ ስለ፡ ኦኔሲሞስ፡ በግዞቴ፡ *የወለድሁት። *ቆላ፡ ፬፡ ፱። †፩፡ ቆሮ፡ ፬፡ ፲፭።
ገላት፡ ፬፡ ፲፱።

፲፩፡ እርሱ፡ ቀድሞ፡ ያልረባህ፡ ዛሬ፡ ግን፡ አጅግ፡ ይረባል፡ ላንተ፡ ለኔም።

፲፪፡ ያስመለስሁት፡ አንተ፡ ግን፡ እንደ፡ ነፍሴን፡ ተቀበለው።

፲፫፡ አወድም፡ ነበርሁ፡ ወደኔ፡ አስቀረው፡ ዘንድ፡ *ባንተ፡ ለውጥ፡ ያገለግለኝ፡ ዘንድ፡ ስለ፡ ወንጌል፡ በመታሠሬ። *፩፡ ቆሮ፡ ፲፮፡ ፲፯። ፊል፡ ፪፡ ፴።

፲፬፡ ነገር፡ ግን፡ ያለ፡ ፈቃድህ፡ አንዳች፡ አደርግ፡ ዘንድ፡ አልወደድሁም፡ መስጠትህ፡ በግድ፡ እንዳይሆን፡ *በፍቃድ፡ እንጂ። *፪፡ ቆሮ፡ ፱፡ ፯።

፲፭፡ ምናልባት፡ ስለዚህ፡ አንድ፡ ወራት፡ ተለይቶህ፡ እንደ፡ ሆነ፡ ለዘላለሙ፡ እንድትዘው።
ዘፍ፡ ፵፭፡ ፭።

፲፮፡ እንደ፡ ባርያ፡ ደግሞ፡ አይደለም፡ እንደ፡ *ተወደደ፡ ወንድም፡ እንጂ። ከባርያ፡ የሚሻል። ለኔም፡ የተወደደ፡ ወንድም፡ ከሆነኝ፡ ለንትስ፡ እንዴት፡ ይሆን፡ በሥጋም፡ በጌታም። *ማቴ፡ ፳፫፡ ፰። ፩፡ ጢሞ፡ ፮፡ ፪።

፲፯፡ አሁንም፡ ባልንጀራዬ፡ ትለኝ፡ እንደሆንህ፡ እንደኔ፡ ተቀበለው።

፲፰፡ በምንም፡ በድሎህ፡ እንደሆን፡ ወይም፡ አንዳች፡ ወስዶብህ፡ እንደሆን፡ በኔ፡ ላይ፡ ቍጠረው።

፲፱፡ እኔ፡ ጳውሎስ፡ በጄ፡ ጻፍሁ። ስለርሱ፡ እኔ፡ እመልሳለሁ። እንዳልልህ፡ አንተ፡ ስለ፡ ነፍስህ፡ ባለዳዬ፡ እንድትሆን።

፳፡ አዎን፡ ወንድሜ፡ ሆይ። እኔን፡ ባንተ፡ ደስ፡ ይለኝ፡ ዘንድ፡ በእግዚአብሔር። ልቤን፡ አሳርፈው፡ በእግዚአብሔር። ቍ፡ ፯።

፳፩፡ እኔ፡ በመታዘዝህ፡ አምኜለሁና፡ ጻፍሁልህ። ካልሁህ፡ አብልጠህ፡ እንድታደርግ፡ አውቄ።
፪፡ ቆሮ፡ ፯፡ ፲፭፡ ፲፮።

፳፪፡ ከዚህም፡ ጋራ፡ ቤት፡ አዘጋጅልኝ፡ ተስፋ፡ አደርጋለሁና፡ በጸሎታችሁ፡ *እሰጣችሁ፡ ዘንድ።
*ፊል፡ ፩፡ ፳፭።

፳፫፡ እንደ፡ ትእ፡ ነህ፡ ይልሃል፡ ኤጳፍራስ፡ ከኔ፡ ጋራ፡ የታሠረው፡ በክርስቶስ፡ የሱስ። ቆላ፡ ፩፡ ፯፡፡ ፬፡ ፲፪፡፡

፳፬፡ ማርቆስ፡ አርስጠርኮስ፡ ዴማስ፡ ሉቃስ፡ የሚ ያግዙኝ። ቆላ፡ ፬፡ ፲፡ ፲፬፡፡

፳፭፡ የጌታችን፡ የየሱስ፡ ክርስቶስ፡ ጸጋ፡ ከመንፈ ሳችሁ፡ ጋራ፡ ይሁን። አሜን።

ለፊልሞን፡ ከሮምያ፡ ተጻፈች። በኦኔሲሞስ፡ በባርያውም፡ እጅ፡ ተላከች።

# የሐዋርያ ፡ የጳውሎስ ፡ መልእክት ፡ ወደ ፡ ዕብራውያን።

## ምዕራፍ፡ ፩፡

፩፡ እግዚአብሔር፡ አስቀድሞ፡ በብዙ፡ ነገር፡ በል ዩ፡ ልዩ፡ አይነትም፡ ላባቶቻችን፡ *በነቢያት፡ አፍ፡ ከተ ናገረ፡ በኋላ። *ዘኍል፡ ፲፪፡ ፮፡ ፰፡፡ ሮሜ፡ ፫፡ ፪፡፡ ፪፡ ጢሞ፡ ፫፡ ፲፮፡፡

፪፡ እርሱ፡ በዚህ፡ በኋለኛው፡ ዘመን፡ በልጁ፡ ነገረን፡ ሁሉን፡ *ወራሽ፡ ባደረገው። ዓለሙንም፡ በርሱ፡ የፈ ጠረ። *መዝ፡ ፪፡ ፰፡፡ ዮሐ፡ ፩፡ ፫፡ ቆላ፡ ፩፡ ፲፮፡፡

፫፡ እርሱም፡ *የክብሩ፡ ብርሃን፡ የአካሉም፡ ምሳ ሌ፡ ሁሉንም፡ የያዘ፡ በችሎቱ፡ ቃል። እርሱም፡ የኃጢአ ታችነን፡ ተማንጸት፡ በራሱ፡ ካደረገ፡ በኋላ፡ በታላቅነት፡ ቀኝ፡ በከፍታ፡ **ተቀመጠ። *፪፡ ቆሮ፡ ፬፡ ፬፡፡ ቆላ፡ ፩፡ ፲፭፡፡ †ም፡ ፱፡ ፲፬፡ ፳፮፡፡ **ማቴ፡ ፳፮፡ ፷፬፡፡

፬፡ ይህም፡ ከመላእክት፡ ይበልጣል፡ እርሱ፡ የወረ ሰው፡ ስም፡ ከርሳቸው፡ በበለጠ፡ መጠን። ፊል፡ ፪፡ ፱፡፡

፭፡ ማንን፡ ነው፡ ከመላእክት፡ *ያለው፡ ከቶ። አን ተ፡ ልጄ፡ ነህ። እኔ፡ ዛሬ፡ ወለድሁህ። ደግሞስ፡ ማን ን፡ አለ። እኔ፡ ተአባት፡ እሆነዋለሁ፡ እርሱም፡ ልጄ፡ ይ ሆናል። *መዝ፡ ፪፡ ፯፡፡ †፪፡ ሳሙኤ፡ ፯፡ ፲፬፡፡

፮፡ ደግሞም፡ *በኩር፡ ወደ፡ ዓለም፡ ባገባ፡ ጊዜ፡ አ ለ። የእግዚአብሔር፡ ተመላእክት፡ ሁሉ፡ ለርሱ፡ ይሰ ግዱ። *ሮሜ፡ ፰፡ ፳፱፡፡ †መዝ፡ ፺፯፡ ፯፡፡

፯፡ ስለ፡ መላእክትም፡ አለ። *መላእክቱን፡ ንፋሳት ን፡ ያደረገ፡ አገልጋዮቹንም፡ የእሳት፡ ነበልባሎች። መዝ፡ ፻፬፡ ፬፡፡

፰፡ ስለ፡ *ልጁ፡ ግን፡ አለ፡ ዙፋንህ፡ አምላክ፡ ለዘላ ለም፡ ነው። የመንግሥትህ፡ በትር፡ የቅንነት፡ በትር፡ ነው። *መዝ፡ ፵፭፡ ፯፡ ፰፡፡

፱፡ ጽድቅን፡ ወደድህ፡ ዓመፃንም፡ ጠላህ። ስለዚ ህም፡ እግዚአብሔር፡ አምላክህ፡ የደስታ፡ ቅቤ፡ *ቀ ባህ፡ ከባልንጀሮችህ፡ ይልቅ። *ኢሳ፡ ፷፬፡ ፩፡፡ የሐዋ፡ ፲፡ ፴፰፡፡

፲፡ ደግሞም፡ አለ። አንተ፡ አቤቱ፡ በጥንት፡ ምድ ርን፡ መሠረትህ፡ ሰማዮችም፡ *የጁህ፡ ስራ፡ ናቸው። *መዝ፡ ፻፪፡ ፳፮፡—፳፰፡፡

፲፩፡ እርሳቸው፡ ይጠፋሉ፡ አንተ፡ ግን፡ ትኖራለህ። ሁሉም፡ እንደ፡ ልብስ፡ ያረጃሉ።

፲፪፡ እንደ፡ መጐናጸፊያም፡ ትጠቀላቸዋለህ፡ *ይ ለውጡማል። አንተ፡ ግን፡ አንተ፡ ነህ፡ ዘመንህም፡ *አያልቅም። *ኢሳ፡ ፶፬፡ ፬፡፡ ራእ፡ ፮፡ ፲፬፡፡ †ም፡ ፲፫፡ ፰፡፡

፲፫፡ ከመላእክትስ፡ ማንን፡ አለ። *በቀኜ፡ ተቀመ ጥ፡ ጸላቶችህን፡ ከግርህ፡ ጫማ፡ በታች፡ እስክጥል፡ ድ ረስ። *መዝ፡ ፻፲፡ ፩፡፡

፲፬፡ እሌህ፡ ሁሉ፡ ለማገልገል፡ መናፍስት፡ አይደሉ ምን፡ *ለማገልገል፡ የሚላኩ፡ መዳንን፡ ይወርሱ፡ ዘን ድ፡ ላላቸው። *ዘፍ.ጥ፡ ፴፬፡ ፯፡፡ መዝ፡ ፴፬፡ ፰፡፡ ፺፩፡ ፲፩፡፡

## ምዕራፍ፡ ፪፡

፩፡ ስለዚህም፡ ይገባናል፡ የሰማነውን፡ ሁሉ፡ አብ ዝተን፡ እንጠብቅ፡ ዘንድ፡ እንዳንወድቅ።

፪፡ *በመላእክት፡ የተነገራት፡ ነገር፡ የጸናች፡ ከሆነ ች፡ መተላለፍና፡ አለመታዘዝ፡ ሁሉም፡ ባገባብ፡ ፍር ድ፡ ከተቀበለች። *የሐዋ፡ ፯፡ ፶፫፡፡ ገላት፡ ፫፡ ፲፱፡፡

፫፡ እኛ፡ እንዴት፡ *እናመልጣለን፡ ይህነን፡ ታላቅ፡ መድኃኒት፡ ቸል፡ ብንል፡ ከሆነ። ይህ፡ ጌታችን፡ በር ሱ፡ መናገር፡ የጀመረ፡ ከሰሙትም፡ ወደኛ፡ ጸና። *ም፡ ፲፡ ፳፱፡፡ ፍ፡ ፲፪፡ ፳፭፡፡ ዮሐ፡ ፩፡ ፩፡ ፪፡፡

፬፡ እግዚአብሔር፡ *ሲመሰክርላቸው፡ በምልእክ ት፡ በተአምራትም፡ በልዩ፡ ልዩ፡ ኃይልም፡ የመንፈስ፡ ቅዱስንም፡ ክፍል፡ በመስጠት፡ እንደ፡ ፈቃዱ። *ማር፡ ፲፮፡ ፳፡፡ ፩፡ ቆሮ፡ ፲፪፡ ፬፡ ፲፩፡፡

፭፡ ያነን፡ የሚመጣውን፡ ዓለም፡ ስለርሱ፡ የተናገ ርነ፡ ለመላእክት፡ አላስገዛምና።

፮፡ ነገር፡ ግን፡ አንዱ፡ ባንድ፡ ስፍራ፡ መሰከረ፡ እን ደህ፡ ሲል። ምንድር፡ ነው፡ ሰው፡ ታስበው፡ ዘንድ። ወይስ፡ የሰው፡ ልጅ፡ ትጐበኘው፡ ዘንድ። *መዝ፡ ፰፡ ፭፡፡

፯፡ ከመላእክት፡ ጥቂት፡ አሳነስኸው። ክብርን፡ ምስጋናንም፡ አክሊል፡ አደረግህለት፡ በጁህም፡ ስራ፡ ሁሉ፡ ላይ፡ ሾምኸው።

፰፡ ሁሉን፡ አስገዛህለት፡ ከግሩ፡ በታች። ሁሉንም፡ ለርሱ፡ በማስገዛቱ፡ አንዳች፡ አልተውም፡ ተገዛለት፡ እንጂ። ዛሬ፡ ግን፡ ሁሉ፡ ለርሱ፡ እንደ፡ ተገዛለት፡ አና ይም። ቆላ፡ ፫፡ ፫፡ ፬፡፡

፱፡ ከመላእክት፡ ግን፡ ጥቂት፡ የተዋረደውን፡ እናያለን፡ እርሱም፡ የሱስ፡ ስለ፡ ሞቱ፡ ሕማም፡ ክብርን፡ ምስጋናንም፡ *አክሊል፡ ያደረገለት። በእግዚአብሔር፡ ጸጋ፡ ሞት፡ ይቀምስ፡ ዘንድ፡ስለ፡ ሰው፡ †ሁሉ።
*ፊል፡ ፪፡ ፰፡ ፱። †፪፡ ቆር፡ ፭፡ ፲፬። ፩፡ ዮሐ፡ ፪፡ ፪።

፲፡ ይገባልና፡ ስለርሱ፡ ሁሉ፡ የሆነ፡ ሁሉም፡ *በጂ፡ የተሰራ፡ ብዙ፡ ልጆች፡ ወደ፡ ክብር፡ያገባ፡የመድኃኒታቸውን፡ †አለቃ፡ **በሕማም፡ ይፈጽም፡ ዘንድ።
*ሮሜ፡ ፲፩፡ ፴፮። †ሚካ፡ ፪፡ ፲፫። **ም፡ ፭፡ ፰፡ ፱።

፲፩፡ የቀደሰው፡ የተቀደሱትም፡ ሁሉ፡ *ካንድ፡ ናቸውና። ስለዚህም፡አያፍርም፡ †ወንድሞች፡ ይላቸው፡ ዘንድ።
*ሉቃ፡ ፫፡ ፴፰። ዮሐ፡ ፲፯፡ ፲፱።
†ማር፡ ፫፡ ፴፬። ዮሐ፡ ፳፡ ፲፯።

፲፪፡ ሲል፡ *ለወንድሞቼ፡ስምህን፡ እነግራለሁ። በሕዝብ፡መካከል፡አመሰግንሃለሁ። *መዝ፡ ፳፪፡ ፳፫።

፲፫፡ ደግሞም፡ ይላል። *እኔ፡ በርሱ፡ የታመንሁ፡ እሆናለሁ። ደግሞም፡ ይላል። †እነሆኝ፡ እኔ፡ እግዚአብሔርም፡ ያሰጠኝ፡ ልጆች።
*ኢሳ፡ ፰፡ ፲፯።
†ኢሳ፡ ፰፡ ፲፰።

፲፬፡ ልጆችም፡ በሥጋና፡ በደም፡ ተገናኝተውታልና፡ እርሱም፡ ደግሞ፡ በዚህ፡ *ተገናኛቸው፡ †በሞቱ፡ የሞት፡ ሥልጣን፡ ያለውን፡ ይሽር፡ ዘንድ፡ እርሱም፡ **ሰይጣን።
*ሮሜ፡ ፰፡ ፫። †፪፡ ጢሞ፡ ፩፡ ፲።
**ዮሐ፡ ፲፪፡ ፴፩።

፲፭፡ እሊያንም፡ *ይፈታ፡ ዘንድ፡ ከሞት፡ ፍርሃት፡ የተነሣ፡ ለባርነት፡ ተዋርደው፡የነበሩትን፡ ዕድሜያቸውን፡ ሁሉ።
*ሉቃ፡ ፩፡ ፸፬። ገላት፡ ፬፡ ፲፭።

፲፮፡ የመላእክትን፡ አካል፡ የወሰደ፡ አይደለም፡ የአብርሃምን፡ አካል፡ ዘር፡ ወሰደ፡ እንጂ።

፲፯፡ ስለዚህም፡ ይገባዋል፡ *ወንድሞቹን፡ በሁሉ፡ ይመስል፡ ዘንድ፡ ይቅር፡ ባይ፡ ወደ፡እግዚአብሔር፡ በሚደርስ፡ ነገር፡ በታመነም፡ የካህናት፡ አለቃ፡ ይሆንና፡ የሕዝቡን፡ ኃጢአት፡ ያስተሰርይ፡ ዘንድ።
*ም፡ ፬፡ ፲፭። ፊል፡ ፪፡ ፯።

፲፰፡ ሕማማት፡ በተቀበለበትና፡ በተፈተነበት፡ ነገር፡ እርሱ፡ የተፈተኑትን፡ ያግዝ፡ ዘንድ፡ ይችላልና።

## ምዕራፍ፡ ፫፡

፩፡ ስለዚህም፡ *ቅዱሳን፡ወንድሞቼ፡ሆይ፡ ከሰማይ፡ በመጣችው፡ መጸራት፡ ባልንጀሮቼ፡ ይህነን፡ የሃይማኖታችነን፡ †ሐዋርያ፡የካህናት፡ አለቃንም፡ ተመልከቱ፡የሱስ፡ክርስቶስን። *ም፡ ፪፡ ፲፩። †ም፡ ፬፡ ፲፬።

፪፡ የታመነ፡ የሆነ፡ በሾመው፡ዘንድ፡ ሙሴ፡ደግሞ፡ የታመነ፡ እንደ፡ ሆነ፡ በቤቱ፡ ሁሉ። ዘኁል፡ ፲፪፡ ፯።

፫፡ ስለዚህም፡ ክብር፡ ይገባዋል፡ እጅግ፡ ከሙሴ፡ ይልቅ፡ ቤትን፡ ለሚሠራ፡ እጅግ፡ ክብር፡ ስላለው፡ ከቤቱ፡ ይልቅ።

፬፡ ቤቱ፡ ሁሉ፡አንድ፡ ሰው፡ይሰራልና፡ ሁሉን፡ግን፡ የሰራ፡ እርሱ፡እግዚአብሔር፡ ነው።

፭፡ ሙሴ፡ በቤቱ፡ ሁሉ፡ የታመነ፡ ሁንዋልና፡ እንደ፡ ሎሌ፡ ለምስክር፡ ኋላ፡ ይነገር፡ ዘንድ፡ ባለው፡ ነገር።

፮፡ ክርስቶስ፡ ግን፡ እንደ፡ ልጅ፡ በቤቱ፡ ላይ። *ቤቱም፡ እኛ፡ ነን፡በድፍረት፡በተስፋውም፡ †ትምክሕት፡ ብንያዝ፡እስከ፡ፍጻሜ። *ኤፌ፡ ፪፡ ፳፪። †ም፡ ፮፡ ፲፩።

፯፡ ስለዚህም፡ መንፈስ፡ ቅዱስ፡ እንዲል። *ዛሬ፡ እላንት፡ ድምጹን፡ ከሰማችሁ፡ ልባችሁን፡ አታጽኑ።
*መዝ፡ ፺፭፡ ፯—፱።

፰፡ በቍጣ፡ እንደ፡ሆነ፡ በፈተናም፡ቀን፡ በምድረ፡ በዳ።

፱፡ አባቶቻችሁ፡ በፈተኑኝ፡ ጊዜ። ፈተኑኝ፡ስራዬንም፡ አዩ፡ አርባ፡ አመት። ዘፀአ፡ ፲፯፡ ፯።

፲፡ ስለዚህም፡ ያነን፡ ትውልድ፡ ተቈጣሁ፡ አልሁም፡ ሁለጊዜ፡ በልባቸው፡ ይስታሉ፡ መንገዴንም፡ አላወቁም።

፲፩፡ በቍጣዬ፡ እንደ፡ ማልሁ፡ ወደ፡ዕረፍቴ፡ አይገቡም፡ ብዬ።

፲፪፡ ተጠንቀቁ፡ ወንድሞቼ፡ ሆይ፡ ባንደኛችሁ፡ክፉ፡ ልብ፡ እንዳይሆን፡ ሃይማኖት፡ የሌለው፡ ከሕያው፡ እግዚአብሔር፡ በመራቅ። ም፡ ፲፡ ፴፩።

፲፫፡ እርሱ፡በርሳችሁ፡ራሳችሁን፡ *ተመካከሩ፡ እንጂ፡ ዛሬ፡ በሚባልበቱ፡ ቀን፡ ሁሉ፡ ከላንት፡ ማንም፡ በኃጢአት፡ †ስሕተት፡ እንዳይጸና።
*፩፡ ተሰ፡ ፭፡ ፲፩። †ዘፍ፡ ፫፡ ፲፫። ሮሜ፡ ፯፡ ፲፩።

፲፬፡ እኛ፡ ከክርስቶስ፡ ጋራ፡ አንድ፡ ሁነናልንና፡ በሃይማኖታችን፡ መጀመርያ፡ እስከ፡ *ፍጻሜ፡ ጸንተን፡ ብንይዝ። *ም፡ ፮፡ ፲፬።

፲፭፡ በማለቱ፡ ዛሬ፡ ድምጹን፡ ከሰማችሁ፡ ልባችሁን፡ አታጽኑ፡ እንደ፡ በማስመረርያው።

፲፮፡ አለማን፡ናቸው፡ ሰምተው፡ያስመረሩት፡ከሊዚያ፡ በሙሴ፡ እጅ፡ ከምሥር፡ ከወጡት፡ በቀር።

፲፯፡ በማንንስ፡ ተቈጣ፡ አርባ፡ አመት። ኃጢአት፡ የሰሩትን፡ አይደለምን፡ *ሬሳቸው፡ በምድረ፡ በዳ፡ የወደቀ። *ዘኁል፡ ፲፬፡ ፳፱። ፩፡ ቆር፡ ፲፡ ፲።

፲፰፡ በማንስ፡ማለ፡ ወደ፡ ዕረፍቱ፡ እንዳይገቡ፡ ከማያምኑ፡ ሰዎች፡ በቀር።

፲፱፡ እንግዲህ፡ አይተናል፡ እንዳልተቻላቸው፡ ይገቡ፡ ዘንድ፡ ሃይማኖት፡ ስላልኖራቸው።
ዘኁል፡ ፳፡ ፲፪።

## ምዕራፍ፡ ፬፡

፩፡ አሁንም፡ እንፍራ፡ ተስፋ፡ ቀርትዋልንና፡ ወደ፡ ዕረፍቱ፡ ለመግባት፡ እንጂ፡ ከላንት፡ አንዱ፡ እንደይመስል፡ የማይገባበት፡ እንደ፡ ሆነ።

፪፡ ለኛ፡ ወንጌል፡ ተነግሮልናልና፡ ለለዚያ፡ እንደ፡ ተነገረላቸው፡ ነገር፡ ግን፡ የሰሙት፡ ነገር፡ለለዚያ፡ አልረባቸውም፡ በሃይማኖት፡አልተቀላቀለምና፡ በሰሙት፡ ሰዎች፡ ዘንድ።

፫፡ እኛ፡ ያመነው፡ ወደ፡ ዕረፍቱ፡ እንገባለንና፡ እን

ጀለ። እንደ፡ ማልሁ፡ በቍጣዬ፡ ወደ፡ ዕረፍቴ፡ አይገቡም፡ ብዬ። ምንስ፡ ስራው፡ ተፈጽማ፡ ስለ፡ ነበረች፡ በዓለም፡ ፍጥረት፡ ጀምሮ። ም፡ ፫፡ ፲፩።

፬፡ እንዲህ፡ ብልዋልና፡ ባንድ፡ ስፍራ፡ ስለ፡ ሰባተኛው፡ ቀን። በሰባተኛውም፡ ቀን፡ እግዚአብሔር፡ ከስራው፡ ሁሉ፡ አረፈ። ዘፍጥ፡ ፪፡ ፪።

፭፡ በዚህም፡ ስፍራ፡ ደግሞ፡ አለ። ወደ፡ ዕረፍቴ፡ አይገቡም።

፮፡ አሁንም፡ ሲቀር፡ ሰዎች፡ እንዲገቡባት፡ ቀድሞ፡ የተነገረላቸውም፡እንደልገቡባት፡አላመኑምና።

፯፡ ደግሞም፡ አንዲት፡ ቀን፡ ወሰነ፡ ዛሬ፡በማለቱ፡ በዳዊት፡ እንደ፡ አለ፡ ይህን፡ ከሚያህል፡ ዘመን፡ በኋላ። ዛሬ፡ ድምጹን፡በሰማችሁ፡ጊዜ፡ልባችሁን፡ አታጽኑ። ም፡ ፫፡ ፯።

፰፡ *ኢያሱም፡ የነዌ፡ ልጅ፡ አሳርፎዋቸው፡ቢሆን፡ ስለ፡ ሌላ፡ቀን፡ ባልተናገረም፡ ከዚያ፡ በኋላ። *ዘዳግ፡ ፴፩፡ ፯።

፱፡ እንግዲህ፡ የሰንበት፡ ዕረፍት፡ ለእግዚአብሔር፡ ወገን፡ ቀርትዋል።

፲፡ ወደ፡ ዕረፍቱ፡ የገባ፡ እርሱ፡ ደግሞ፡ ከስራው፡ አርፍዋልና፡ እግዚአብሔር፡ ከስራው፡ እንደረፈ። ራእ፡ ፲፬፡ ፲፫።

፲፩፡ አሁንም፡ እንጋደል፡ወደዚያች፡ዕረፍት፡ ለመግባት፡ ማንም፡ እንደይወድቅ፡እንደለዚያ፡ እንደላመኑት፡ ምሳሌ።

፲፪፡ የእግዚአብሔር፡ *ቃል፡ ሕያው፡ አድራጊም፡ ነውና፡ ለመቍረጥም፡ †የተሳለ፡ ሁለት፡ ልሳን፡ ካለው፡ ሰይፍ፡ ይልቅ። ይጠልቅማል፡ **በነፍስና፡ በመንፈስ፡ መካከል፡ ለመለየት፡ በጅማትም፡ ባጥንትም። ††የልብንም፡ አሳብ፡ ምክሩንም፡ ይመረምራል። *ኤር፡ ፳፫፡ ፳፱። †ራእ፡ ፩፡ ፲፮። **፩፡ ተሰ፡ ፭፡ ፳፫። ††፩፡ ቆር፡ ፲፬፡ ፳፭።

፲፫፡ ከፍጥረትም፡እንደች፡ከርሱ፡ *የሚሰወረው፡ የለም። ሁሉ፡ግን፡የተከፈተ፡የተገለጠም፡ ነው፡ ባይኑ፡ ፊት። ከርሱም፡ጋራ፡ ነው፡ ነገር፡ ያለነ። *ምሳ፡ ፲፭፡ ፫። ኤር፡ ፲፯፡ ፲፯።

፲፬፡ *ታላቅ፡ የካህናት፡ አለቃም፡ ሳለነ፡ ወደ፡ †ሰማይ፡ የወጣ፡የሱስ፡የእግዚአብሔር፡ልጅ። እርሱን፡ **በማመን፡እንያስ። *ም፡ ፫፡ ፩። †ም፡ ፯፡ ፳፮። **ም፡ ፲፡ ፳፫።

፲፭፡ የካህናት፡ አለቃ፡ የለነምና፡ የማይችል፡ ከድካማችን፡ጋራ፡*ይራራ፡ዘንድ። በሁሉ፡ †እንደኛ፡የተፈተነ፡ ነው፡ እንጂ፡ያለ፡**ኃጢአት፡ከመሆኑ፡ በቀር። *ም፡ ፭፡ ፪። †ም፡ ፪፡ ፲፯፡ ፲፰። **ም፡ ፯፡ ፳፮።

፲፮፡ አሁንም፡ ያለ፡ ፍርሃት፡ *በጸጋው፡ ዙፋን፡ ፊት፡ እንቅረብ፡ ምህረት፡ እንድንወስድ፡ ጸጋም፡ እንድናገኝ፡ ትረዳነ፡ ዘንድ፡ †በመከራ፡ ጊዜ። *ዘፀአ፡ ፳፭፡ ፲፯። †መዝ፡ ፵፪፡ ፭፡ ፮።

## ምዕራፍ፡ ፭፡

፩፡ ከሰዎች፡ የሚወሰድ፡ የካህናት፡ አለቃ፡ ሁሉ፡ ስለ፡ ሰው፡ ይሾማልና፡ ለእግዚአብሔር፡ የሚደርስ፡ ነገር፡ ስጦታንና፡ መሥዋዕትን፡ ያቀርብ፡ ዘንድ፡ ስለ፡ ኃጢአት። ም፡ ፰፡ ፫።

፪፡ ሊራራ፡ የሚችል፡ ከሚጠፉ፡ከሚስቱም፡ጋራ፡ እርሱ፡ ደግሞ፡ ከድካም፡ ተቀብዋልና። ም፡ ፬፡ ፲፭።

፫፡ ስለዚህም፡ ይገባዋል፡ ስለ፡ ሕዝቡ፡ እንዲያቀርብ፡ እንደሁ፡ ስለ፡ *ራሱ፡ ኃጢአት፡ ሊሠዋ። *ዘሌዋ፡ ፱፡ ፯፡ ፲፮።

፬፡ ማንም፡ይህችን፡ ክብር፡ ለራሱ፡ አይወስድም፡ ነገር፡ ግን፡ እግዚአብሔር፡ የጸራው፡ ነው፡ ሐሮንን፡ እንደ፡ ጸራ። ዘፀአ፡ ፳፰፡ ፩።

፭፡ እንደሁም፡ ክርስቶስ፡ ራሱን፡ አላመሰገነም፡ የካህናት፡ አለቃ፡ ይሆን፡ ዘንድ። እርሱን፡ አመሰገነው፡ እንጂ፡ ያለውን። አንተ፡ ልጄ፡ ነህ፡ እኔ፡ ዛሬ፡ ወለድሁህ። መዝ፡ ፪፡ ፯።

፮፡ ደግሞ፡ በሌላው፡ ስፍራ፡እንዲል። አንተ፡ ካህን፡ ነህ፡ ለዘላለም፡ እንደ፡ መልከ፡ ጼዴቅ፡ ሹመት። ዘፍጥ፡ ፲፬፡ ፲፰። መዝ፡ ፻፲፡ ፬።

፯፡ እርሱ፡ ሥጋ፡ በለበሰ፡ ጊዜ፡ ልመና፡ ያቀረበ፡ መማጸንም፡ ከሞት፡ ያድነው፡ ዘንድ፡ ወደሚችል፡በብርቱ፡ *ጩኸትና፡ በእንባ፡ ከፍርሃቱም፡ ተሰማት። *ሉቃ፡ ፳፪፡ ፵፬።

፰፡ ልጅም፡ ቢሆን፡ እርሱ፡ መታዘዝን፡ ተማረ፡ በተቀበለው፡ መከራ። ፊል፡ ፪፡ ፰።

፱፡ በተፈጸመም፡ ጊዜ፤ *ለሚታዘዙት፡ሁሉ፡ የዘላለም፡ ሕይወት፡ †ምክንያት፡ ሆነ። *ሮሜ፡ ፩፡ ፭። †ም፡ ፯፡ ፳፭።

፲፡ ከእግዚአብሔርም፡ የካህናት፡ አለቃ፡ ተባለ፡ እንደ፡ መልከ፡ ጼዴቅ፡ ሹመቱ።

፲፩፡ ይህም፡ ስለርሱ፡ ለኛ፡ እጅግ፡ ነገር፡ አለነ፡ ትርጓሚውም፡ ጭንቅ፡ ነው፡ በመስማታችሁ፡ ደክማችኋልና።

፲፪፡ መምህራን፡ትሆኑ፡ ዘንድ፡ይገባ፡ ነበርና። ረጅም፡ዘመን፡ ስለሆናችሁ። ዛሬ፡ ግን፡ ትሻላችሁ፡ የእግዚአብሔርን፡ የነገሩን፡ መጀመርያ፡ ትህማሩ፡ ዘንድ። *ወተትም፡ የምትሹ፡ ሆናችሁ፡ ጽኑ፡ መብልም፡ አይደለም። *፩፡ ቆሮ፡ ፫፡ ፩፡ ፪።

፲፫፡ ምግቡ፡ወተት፡ የሆነ፡ ሁሉ፡ የውነት፡ ነገር፡ አያውቅምና፡ ገና፡ ሕፃን፡ ነውና። ኤፌ፡ ፬፡ ፲፬።

፲፬፡ ጽኑ፡ መብል፡ግን፡ ለፍጹማን፡ነው፡ ልቦናቸውን፡መልካሙንና፡ክፉውን፡ለመለያየት፡ያስለመደ።

## ምዕራፍ፡ ፮፡

፩፡ ስለዚህም፡የክርስቶስን፡የነገሩን፡ መጀመርያ፡ እንተው፡ወደ፡ፍጹሚም፡እንሒድ። ደግመንም፡ መ

ሠረት፡ አንጣል፡ ከሞተች፡ ስራ፡ *ለመመለስ፡ በእግ
ዚአብሔርም፡ ለማመን። *ማቴ፡ ፬፡ ፲፯።
፪፡ *ጥምቀትንም፡ ለመማር። እጅንም፡ ስለ፡ መ
ጫን።ከሙታንም፡ስለ፡†መነሣት። ስለ፡ዘላለሙም፡
ፍርድ። *ዮሐ፡ ፫፡ ፳፭። †ዘኁል፡ ፳፯፡ ፲፰።
፫፡ ይህነንም፡እናደርገዋለን፡እግዚአብሔር፡ ቢፈ
ቅድልን። የሐዋ፡ ፲፰፡ ፳፩።
፬፡ አይቻልምና፡እንደግዜ፡ብርሃን፡ *ለወሰዱ፡የሰ
ማይንም፡ †ስጦታ፡ የቀመሱ። ከመንፈስ፡ ቅዱስ፡
ጋራም፡አንድ፡የሆኑ። *ም፡ ፲፡ ፴፪። †፩፡ ጴጥ፡ ፪፡ ፫።
፭፡ የእግዚአብሔርንም፡ ነገር፡ መልካሚቱን፡ የ
ምትመጣውንም፡ የዓለምን፡ ኃይል፡ የቀመሱ።
ም፡ ፪፡ ፬።
፮፡ ደግሞ፡ ቢወድቁ፡ *ለንስሐ፡ ለመታደስ፡ የእግ
ዚአብሔርን፡ ልጅ፡ ለራሳቸው፡ ሁለተኛ፡ ይሰቅሉታ
ልና፡በግልጥም፡ያጎሩታል። *ም፡ ፲፡ ፳፱።
፪፡ ጴጥ፡ ፪፡ ፳፡ ፳፩።
፯፡ ምድርም፡ ብዙ፡ ጊዜ፡ በርሷ፡ የወረደውን፡ዝ
ናም፡ከጠጣች፡ መልካም፡ ፍሬ፡ ለደከሙባት፡ ላረሷ
ዋትም፡ብታበቅል፡ከእግዚአብሔር፡ ዘንድ፡ በረከት፡
ትቀበላለች።
፰፡ *እሾህና፡ አሜከላ፡ ግን፡ ያበቀለች፡ እንደሆነ፡ የ
ማትረባ፡ ትሆናለች፡ ለመረገምም፡ ትቀርባለች፡ ፍጻ
ሜዋም፡መቃጠል፡ይሆናል። *ዘፍ፡ ፫፡ ፲፰።
፱፡ በላንት፡ ግን፡ ወንድሞቼ፡ ሆይ፡ ልባችን፡ በመል
ካም፡ተስፋ፡ታመነ፡ ወደ፡ሕይወት፡ የምታቀርብ። ይ
ህነን፡ ብንናገር።
፲፡ እርሱ፡እግዚአብሔር፡ ግፈኛ፡ አይደለውምና፡
ስራችሁን፡ *ደረሳ፡ ዘንድ፡ በፍቅርም፡ ድካማችሁን፡
የገለጣችሁት፡ በስሙ፡ ቅዱሳንን፡ ባለፈው፡ ባገልገላ
ችሁ፡ ጊዜ፡ አሁንም፡ ስታገለግልዋቸው።
*ም፡ ፲፡ ፴፪፡—፴፬።
፲፩፡ እንወድማለን፡ ከላንት፡ኢያንዳንዱ፡ይህነን፡
ጥረት፡ ይገልጥ፡ ዘንድ፡ ተስፋችሁ፡ ይጸና፡ ዘንድ፡ እስ
ከ፡ ፍጻሜ። ፊል፡ ፩፡ ፮።
፲፪፡ እንዳታክቱ፡እርሳቸውን፡ ትመስሉ፡ ዘንድ፡እ
ንጂ፡ *ተስፋ፡ የወረሱትን፡ በሃይማኖትና፡ በትዕግ
ሥት። *ም፡ ፲፩፡ ፲፫።
፲፫፡ እግዚአብሔር፡ ግን፡ ለአብርሃም፡ ተስፋ፡ በሰ
ጠው፡ጊዜ፡ ከርሱ፡ የበለጠ፡ባይኖር፡ በሚምልበት፡ በ
ራሱ፡ማለ፡አለም። ዘፍ፡ ፳፪፡ ፲፮፡ ፲፯።
፲፬፡ እኔ፡ በረከት፡ እባርክሃለሁ፡ ብዛትም፡ አበዛ
ሃለሁ።
፲፭፡ እንዲህም፡ ታግሦ፡ ተስፋውን፡ ተቀበለ።
፲፮፡ ሰዎች፡ከርሳቸው፡በሚበልጠው፡ይምላሉና፡
የሙግትም፡ ሁሉ፡ ፍጻሜ፡ *በመሐላ፡ ትጸናለች።
ዘፀአ፡ ፳፪፡ ፲፩።
፲፯፡ ስለዚህም፡ እግዚአብሔር፡ ተስፋ፡ የሚወር
ሱን፡በብዙ፡ምሳሌ፡ያስተምር፡ ዘንድ፡ በወደደ፡ ጊዜ፡
ምክሩ፡ እንደ፡ይናወጥ፡ እርሱ፡ በመካከል፡ ገባ፡ *በመ
ሐላ። *ዘፍ፡ ፳፪፡ ፲፮፡ ፲፯።
፲፰፡ በሁለት፡ በማይለወጥ፡ ነገር፡ እግዚአብሔር፡
ሊዋሽ፡ አይችልም። በሚሆንበት፡ ጽኑ፡ ደስታ፡ ይሆን
ልን፡ዘንድ፡ወደርሱ፡ የሸሸን፡ የተሰጠችን፡ ተስፋ፡ ለመ
ያዝ።
፲፱፡ እርሱም፡ ለነፍሳችን፡ እንደ፡ አውታችን፡ ጽ
ኑ፡ ወደ፡ መጋረጃው፡ ውሥጥም፡ የሚገባ፡ መልሕቅ፡
ያለ። ዘፀአ፡ ፳፮፡ ፴፩፡—፴፫።
፳፡ የሱስ፡ *ቀድሞ፡ ስለኛ፡ ወደ፡ ገባበት፡ †የካህና
ት፡አለቃ፡ለዘላለም፡ የሚሆን፡እንደ፡መልከ፡ጼዴቅ፡
ሹመት። *ም፡ ፲፡ ፳። †ም፡ ፭፡ ፮።

## ምዕራፍ፡ ፯፡

፩፡ ይህም፡ *መልከ፡ ጼዴቅ፡ የሳሌም፡ ንጉሥ፡ የል
ዑል፡ የእግዚአብሔር፡ ካህን፡ ነው። አብርሃምንም፡
የተገናኘው፡ እርሱ፡ ነገሥታትን፡ ወግቶ፡ በተመለሰ፡
ጊዜ፡ባረከውም። *ዘፍ፡ ፲፬፡ ፲፰።
፪፡ አብርሃም፡ ከያዘው፡ ሁሉ፡ ካሥር፡ አንድ፡ ሰጠ
ው። የፊተኛውም፡ የስሙ፡ ትርጓሜ፡ *የጽድቅ፡ንጉ
ሥ፡ ነው። ከዚያ፡በኋላም፡ የሳሌም፡ ንጉሥ፡ ማለት፡
†የሰላም፡ንጉሥ፡ነው። *ም፡ ፩፡ ፱። መዝ፡ ፷፱፡ ፱።
†መዝ፡ ፸፪፡ ፫። ኢሳ፡ ፱፡ ፮፡ ፯።
፫፡ አባትም፡ የለውም፡ እናትም፡ የለችውም፡ ት
ውልዱም፡ አይቈጠርም። ለዘመኑም፡ መጀመርያ፡
የለውም፡ ለሕይወቱም፡ ፍጻሜ፡ የለውም። ነገር፡ ግ
ን፡ ለእግዚአብሔር፡ ልጅ፡ ተመስሉ፡ ለዘላለም፡ ካህ
ን፡ ሁኖ፡ ይኖራል።
፬፡ እዩ፡ እስኪ፡ ምን፡ ያህላል፡ መጠኑ፡ ይህ፡አብር
ሃም፡ ያባቶች፡ አለቃ፡ *ካሥር፡ አንድ፡ የሰጠው።
*ዘፍ፡ ፲፬፡ ፳።
፭፡ እርሳቸውም፡የሌዊ፡ልጆች፡ክህነት፡የተሰጣቸ
ው፡*ታዘው፡ነበሩ፡ከሕዝብ፡ካሥር፡ አንድ፡ ይወስዱ፡
ዘንድ። በኦሪት፡እንደለ፡ ይህም፡ ከወንድሞቻቸው፡
ነው፡ ምንስ፡ በአብርሃም፡ †ወገብ፡ የወጡ፡ ቢሆኑ።
*ዘዳግ፡ ፲፬፡ ፳፯፡ ፳፱። †ዘፍ፡ ፴፭፡ ፲፩።
፮፡ ይህ፡ ግን፡ ከወገናቸው፡ ያይደለ፡ ከአብርሃ
ም፡ካሥር፡አንድ፡ ወሰደ፡ተስፋ፡ የተሰጠውንም፡ *ባ
ረከው። *ዘፍ፡ ፲፪፡ ፫። ፍ፡ ፲፬፡ ፲፱፡ ፳።
፯፡ ያለ፡መጠራጠርም፡ታናሹ፡በረከት፡ይወስዳል፡
ከሚበልጠው።
፰፡ ከዚህም፡ የሚሞቱ፡ ሰዎች፡ ካሥር፡አንድ፡ ይ
ወስዳሉ። ከዚያ፡ግን፡ይወስዳታል፡ሕያው፡እንደሆነ፡
የተመሰከረለት።
፱፡ እንደ፡ ተነገረውም፡ ነገር፡ ሌዊም፡ደግሞ፡ ካሥ
ር፡አንድ፡ የሚወሰደው፡ በአብርሃም፡ካሥር፡ አንድ፡
ሰጠ።
፲፡ እርሱ፡ገና፡ባባቱ፡ ወገብ፡ ነበርና፡መልከ፡ ጼዴቅ፡
ባገኘው፡ ጊዜ።

፲፩፤ ፍጻሜስ፡ በሌዊ፡ ክህነት፡ *ቢሆን፡ የኦሪት፡ ሕግ፡ለሕዝብ፡ የተደረገባት፡ አንዳችም፡ ባላሻም፡ ነበር፡ ሌላ፡ ካህን፡ ይነሣ፡ ዘንድ፡ በመልከ፡ ጼዴቅ፡ ሹመት፡ በአሮንም፡ ሹመት፡ የማይባል። *ቍ፡ ፲፰፡ ፲፱፡፡

፲፪፤ ክህነትም፡ የተሻረ፡ ከሆነ፡ የግድ፡ የኦሪት፡ ሽረት፡ ደግሞ፡ ይሆናል።

፲፫፤ ይህች፡ ስለርሱ፡ የተነገረችለት፡ ከሌላ፡ ወገን፡ ነበርና፡ ማንም፡ ከርሱ፡ መሠውያን፡ ያላገለገለ።

፲፬፤ ጌታችን፡ከይሁዳ፡እንደ፡ወጣ፡ የተገለጠ፡ ነውና። ለዚህም፡ ነገድ፡ ሙሴ፡እንዳች፡ አልተናገረም፡ ከክህነት። ዘፍ.ጥ፡ ፵፱፡ ፲፡፡ ኢሳ፡ ፲፩፡ ፩፡፡ ሚክ፡ ፭፡ ፩፡፡

፲፭፤ ደግሞም፡ ይህ፡ ነገር፡አብዝቶ፡ ተገልጦዋል፡ በመልከ፡ ጼዴቅ፡ ምሳሌ፡ሌላ፡ ካህን፡ ቢነሣ።

፲፮፤ በሥጋዊ፡ በኦሪት፡ ትእዛዝ፡ ሥርዓት፡ ያልሆነ፡ በማትፈታው፡ በሕይወት፡ ኃይል፡ እንጂ። ቍ፡ ፳፭፡—፳፰፡፡

፲፯፤ ይመሰክርለታልና፡ እንዲህ፡ ሲል። *አንተ፡ ካህን፡ ነህ፡ ለዘላለም፡ እንደ፡ መልከ፡ ጼዴቅ፡ ሹመት። *ም፡ ፭፡ ፮፡፡

፲፰፤ የቀደመዪቱ፡ትእዛዝ፡ ሽረት፡ሆንዋልና፡ስለ፡ ድካምዋ፡ረብም፡ ስላልኖራት።

፲፱፤ ኦሪት፡ አንዳችም፡ *አልፈጸመችምና፡ የሚበልጠው፡የተሰፋው፡መግቢያ፡ግን፡ ወደ፡ እግዚአብሔር፡ የምንቀርብበት፡ ሆነ። *ቍ፡ ፲፩፡፡

፳፤ እርሱም፡ ያለ፡ መሐላ፡ካህን፡ አልሆነም። እለዚያ፡ ካህናት፡ ያለ፡ መሐላ፡ ሁነዋልና።

፳፩፤ ይህ፡ ግን፡ በመሐላ፡ ነው፡ በሚለው፡ ቃል። እግዚአብሔር፡ማለ፡አያዝንም። አንተ፡ ለዘላለም፡ካህን፡ሆንህ፡በመልከ፡ጼዴቅ፡ ሹመት። መዝ፡ ፻፲፡ ፬፡፡

፳፪፤ እንዲሁም፡ የሱስ፡ የሚበልጠውን፡ ኪዳን፡ መድኅን፡ ሆነ። ም፡ ፰፡ ፮፡፡ ና፡ ፲፪፡ ፳፬፡፡

፳፫፤ እለዚያም፡እጅግ፡ካህናት፡ ነበሩ፡ በሞት፡ ተከለከሉ፡ እንዳይኖሩ።

፳፬፤ ይህ፡ ግን፡ ለዘላለም፡ ይኖራልና፡ የማይለውጥ፡ ክህነት፡ አለው።

፳፭፤ ስለዚህም፡ ይቻለዋል፡ ወደ፡ *እግዚአብሔር፡በርሱ፡የሚመጡን፡ †ፈጽሞ፡ ያድን፡ ዘንድ። ሁለ ጊዜ፡ ሕያው፡ ነውና፡ **ጸሎት፡ ስለርሳቸው፡ ያሳርግ፡ ዘንድ። *ዮሐ፡ ፲፬፡ ፮፡፡ †ም፡ ፲፡ ፲፬፡፡ **ኢሳ፡ ፶፫፡ ፲፩፡፡

፳፮፤ እንዲህ፡ያለ፡ የካህናት፡አለቃ፡ ይገባልናልና፡ ቅዱስ፡የሚሆን፡ክፋትና፡ርኵሰት፡የሌለበት፡ከኃጢአተኞች፡ የራቀ፡ ከሰማያትም፡ ከፍ፡ ከፍ፡ ያለ። ም፡ ፩፡ ፫፡ ፬፡፡ ኤፌ፡ ፬፡ ፲፡፡

፳፯፤ እርሱ፡ የግድ፡ የሌለበት፡ *ዕለት፡ ዕለት፡ እንደለዚያ፡ካህናት፡አለቆች፡ መሥዋዕት፡ ያቀርብ፡ ዘንድ፡ አስቀድሞ፡ ስለ፡ ኃጢአቱ፡ከዚያ፡ በኋላም፡ ስለ፡ ሕዝቡ፡ ኃጢአት። እርሱም፡ ይህችን፡ አንደጊዜ፡ አደረጋት፡ †ራሱን፡ ባቀረበ፡ ጊዜ። *ዘሌዋ፡ ፲፮፡ ፮፡ ፲፭፡ ፳፬፡፡ †ም፡ ፱፡ ፲፪፡ ፳፮፡

፳፰፤ የኦሪት፡ *ሕግ፡ የካህናት፡ አለቆች፡ ታደርጋለችና፡ ድካም፡ ያለባቸውን፡ ሰዎች። የመሐላዪቱ፡ ቃል፡ግን፡ ከኦሪት፡ በኋላ፡ የሆነችው፡ ልጁን፡ አስነሣች፡ ለዘላለም፡ ፍጹም፡ የሚሆነውን። ም፡ ፭፡ ፩፡ ፪፡፡ ና፡ ፭፡ ፱፡፡

## ምዕራፍ፡ ፰፤

፩፤ ከተባለውም፡ አይነተኛው፡ ነገር፡ይህ፡ ነው። እንዲህ፡ያለ፡ የካህናት፡ አለቃ፡ አለን፡ በታላቅነት፡ ዙፋን፡ቀኝ፡ በሰማያት፡ የተቀመጠ። ም፡ ፬፡ ፲፬፡፡

፪፤ መቅደስን፡ የሚያገለግል፡ እውነተኛዪቱንም፡ ድንኳን፡ እግዚአብሔር፡ የተከላት፡ ሰውም፡ አይደለም። ቍ፡ ፭፡፡

፫፤ የካህናት፡ አለቃ፡ ሁሉ፡ ስጦታንና፡ መሥዋዕትን፡ ያቀርብ፡ ዘንድ፡ ይመደባልና። ስለዚህም፡ ይገባዋል፡ ለዚህም፡ ደግሞ፡ አንዳች፡ የሚያቀርበው፡ ይኖረው፡ ዘንድ። ም፡ ፭፡ ፩፡፡

፬፤ በምድርስ፡ የሚኖር፡ ቢሆን፡ ካህን፡ ባልሆነም። ካህናት፡ አሉዋቸውና፡ መሥዋዕት፡ የሚያቀርቡ፡ እንደ፡ ሕጉ።

፭፤ እለዚያ፡ የሚያገለግሉ፡ በሰማይ፡ እንደለው፡ ነገር፡ *ምሳሌና፡ ጥላ። ለሙሴ፡ እንደተባለ፡ ድንኳኒቱን፡ ይሰራ፡ ዘንድ፡ ባዘዘው፡ ጊዜ፡ አለውም። አሁንም፡ ተመልከት፡ በተራራ፡ ላይ፡ †በተሳየህ፡ ምሳሌ፡ ሁሉ፡እንድታደርግ። *ቈላ፡ ፪፡ ፲፯፡፡ †ዘፀአ፡ ፳፭፡ ፵፡፡

፮፤ ዛሬ፡ግን፡እርሱ፡የምትበልጥ፡ ማገልገል፡ አገኘ፡ *ለምትበልጥ፡ ሥርዓት፡ መካከለኛ፡ ሆንዋልና። በተሻለ፡ተስፋ፡ላይ፡ተመሠርታለችና። *ም፡ ፯፡ ፳፪፡፡ ፪፡ ቆሮ፡ ፫፡ ፮፡፡

፯፤ የፊተኛዪቱስ፡ባትነወር፡ለሁለተኛዪቱ፡ስፍራ፡ ባልተፈለገም።

፰፤ እርስዋን፡ ነቅፎ፡ ይላቸዋልና። *እነሆ፡ ወራት፡ ትመጣለች፡ይላል፡ እግዚአብሔር። በእሥራኤል፡ ቤትና፡ በይሁዳም፡ ቤት፡ አዲስ፡ ኪዳን፡ አፈጽምባታለሁ። *ኤር፡ ፴፩፡ ፴፩፡—፴፬፡፡

፱፤ ላባቶቻቸው፡ እንደ፡ ሰጠሁት፡ *ኪዳን፡ አይደለም። እጃቸውን፡ ባያዝኋቸው፡ ጊዜ፡ ከምድረ፡ ግብጽ፡ አወጣቸው፡ ዘንድ። በኪዳኔ፡ አልጸኑምና። እኔም፡ ቸል፡ አልኋቸው፡ †እግዚአብሔር፡ አለ። *ዘፀአ፡ ፲፱፡ ፭፡፡ †ኤር፡ ፲፭፡ ፩፡፡

፲፤ ይህ፡ግን፡ኪዳን፡ ነው፡ ለእሥራኤል፡ ቤት፡ የምሰጠው፡ከዚያች፡ወራት፡በኋላ፡እግዚአብሔር፡አለ። ሕጌን፡በሕሊናቸው፡አደርጋለሁ፡ በልባቸውም፡ እጽፈዋለሁ። እኔም፡ አምላካቸው፡እሆናለሁ። እርሳቸውም፡ ወገኖቼ፡ ይሆናሉ። ኢሳ፡ ፶፬፡ ፲፫፤

፲፩፤ ሁሉም፡ ኢያንዳንዱ፡ ባልንጀራውን፡ አያስተምርም፡ ሁሉም፡ ኢያንዳንዱ፡ ወንድሙን፡ እንዲህ፡ሲል። እግዚአብሔርን፡ እወቅ፡ሁሉ፡ያውቁኛልና፡ ከታናሾች፡ ጀምሮ፡ እስከ፡ ታላቆች። ኤር፡ ፱፡ ፳፬፡፡

፲፪፡ ክፉታቸውን፡ የምበርድ፡ እሆናለሁና፡ ደግሞም፡ ኃጢአታቸውንና፡ በደላቸውን፡ አላስብም።

፲፫፡ አዲስ፡ ሲል፡ የፊተኛዪቱን፡ ሥርዓት፡ በለ፡ አስረጀት፡ነው። የቀደመውም፡ ነገር፡ ያረጀውም፡ ለጥፋት፡የቀረበ፡ነው።

## ምዕራፍ፡ ፱፡

፩፡ የቀደመችውም፡ ድንኳን፡ የማገልገል፡ ሥርዓት፡ ነበራት፡ ምድራዊም፡ መቅደስ።

፪፡ የፊተኛዪቱ፡ድንኳን፡የተደረገችው፡ነበረችና፡ *መቅረዝ፡የነበረባት፡ማዕድም፡የቍርባንም፡እንጀራ፡ †መቅደስም፡ ትባል፡ ነበረች።

*ዘፀአ፡ ፳፭፡ ፳፫፡ ፴፩፡፡ †ዘፀአ፡ ፳፱፡ ፴፡፡

፫፡ ከሁለተኛው፡ መጋረጃ፡ ግን፡ በኋላ፡ ያለችው፡ ድንኳን፡*ቅድስተ፡ ቅዱሳን፡ ትባል፡ነበረች።

*ዘፀአ፡ ፳፮፡ ፴፫፡፡

፬፡ የወርቅም፡ *ማዕጠንት፡ ነበረባት። †የኪዳኑም፡ታቦት፡ሁለንትናው፡በወርቅ፡የተለበጠ፡ነበረባት፡ የወርቅ፡ **ሣፅን፡ መናም፡ የነበረባት፡ ††የአሮንም፡ በትር፡ የበቀለች። ኪዳኑም፡ የተጻፈባቸው፡ ጽላት።

*ዘፀአ፡ ፴፡ ፴፬—፴፮፡፡ †ዘፀአ፡ ፳፭፡ ፲፡፡
**ዘፀአ፡ ፲፮፡ ፴፫፡፡ ††ዘኍል፡ ፲፯፡ ፲፡፡

፭፡ በላዩም፡ የክብር፡ ኪሩቤል፡ ማስተስረያውን፡ የሚሸፍኑ። ይህም፡ ጊዜው፡ አይደለም፡ ዛሬ፡ ሁሉን፡እንናገር፡ ዘንድ፡ በየተርታው።

ዘፀአ፡ ፳፭፡ ፲፯፡ ፲፰፡፡ ና፡ ፳፮፡ ፴፬፡፡

፮፡ ይህ፡ሁሉ፡ግን፡ እንዲሁ፡ በተዘጋጀ፡ጊዜ፡ የፊተኛዪቱ፡ ድንኳን፡ ካህናት፡ ሁለጊዜ፡ ይገቡባት፡ ነበር፡ ማገልገላቸውን፡ ሲፈጽሙ። ዘኍል፡ ፲፰፡ ፫፡፡

፯፡ ሁለተኛዪቱ፡ ግን፡ ድንኳን፡ አንደግዜ፡ ባመት፡ ይገባታል፡ የካህናት፡ አለቃ፡ ለብቻው። በዚያ፡ ደም፡ ስለ፡ ራሱ፡ የሚያቀርበው፡ ስለ፡ ሕዝቡም፡ ስንፍና።

ዘፀአ፡ ፴፡ ፲፡፡

፰፡ በዚህም፡ አስታወቀ፡ መንፈስ፡ ቅዱስ፡ የቅድስተ፡ቅዱሳን፡መንገድ፡ በዚያን፡ ጊዜ፡ገና፡ ተገልጣ፡ እንዳልነበረች፡የቀደመችው፡ ድንኳን፡ ቁማ፡በነበረች፡ ጊዜ።

፱፡ ይህችም፡ ለዚያ፡ ዘመን፡ ምሳሌ፡ ነበረች፡ ስጦታና፡ መሥዋዕት፡ ለቀረቡበት፡ የሚያገለግላቸውን፡ ሕሊና፡ ይፈጽሙ፡ ዘንድ፡ የማይችሉ።

፲፡ ብቻ፡ *በመብልና፡ በመጠጥ፡ የሆኑ። በተለያየችም፡ †ጥምቀት። እርስዋ፡ የሥጋ፡ ሥርዓት፡ የምትሆን፡ እስከ፡ **መቀናት፡ ዘመን፡ ድረስ።

*ዘሌዋ፡ ፲፩፡ ፲፡፡ †ዘፀአ፡ ፳፱፡ ፫፡፡ **፩፡ ጴጥ፡ ፫፡ ፳፩፡፡

፲፩፡ ክርስቶስ፡ ግን፡ ይመጣ፡ ዘንድ፡ ላለው፡ በጎ፡ነገር፡የካህናት፡*አለቃ፡ ሁኖ፡በመጣ፡ጊዜ፡ወደ፡ታላቂቱ፡ ወደ፡ ተፈጸመችውም፡ በእጅም፡ ወደልተሰራች፡ እርሱም፡ማለቱ፡ከዚህ፡ፍጥረት፡ ወደይደለች፡ †ድንኳን፡ገባ። *ም፡ ፮፡ ፳፡፡ ና፡ ፲፡ ፩፡፡ †ም፡ ፰፡ ፪፡፡

፲፪፡ የፍየልና፡*የላም፡ደም፡ደዛም፡ አልገባም፡ ነገር፡ግን፡†በራሱ፡ ደም፡ አንደግዜ፡ ወደ፡ መቅደስ፡ ገባ፡ ስለኛ፡ **የዘላለምን፡መድኃኒት፡ ባገኘ፡ ጊዜ።

*ዘሌዋ፡ ፲፮፡ ፫፡ ፲፬፡፡ †ም፡ ፲፫፡ ፳፡፡ የሐዋ፡ ፳፡ ፳፰፡፡
**ኢሳ፡ ፵፮፡ ፲፯፡፡

፲፫፡ የፍየልና፡የበሬ፡ ደምስ፡ የላምም፡ አመድ፡ በረከሱት፡ላይ፡ቢረጭ፡ሥጋቸውን፡ ለማንጻት፡ የሚቀድሳቸው፡ ከሆነ። ዘኍል፡ ፲፱፡ ፱፡፡

፲፬፡ እንዴት፡ ይልቁን፡ የክርስቶስ፡ ደም፡ ለዘላለም፡ በሚኖር፡ መንፈስ፡ ራሱን፡ ያቀረበ፡ ያለ፡ *ነውር፡ ለእግዚአብሔር፡ሕሊናችሁን፡†ያነጻል፡ከሞት፡ስራ፡ ሕያው፡ እግዚአብሔርን፡ **ታገለግሉ፡ ዘንድ።

*ዘሌዋ፡ ፳፪፡ ፲፱፡ ፳፡፡ ፩፡ጴጥ፡ ፩፡ ፲፱፡፡
†ም፡ ፲፡ ፪፡ ፳፪፡፡ **፩፡ ተሰ፡ ፩፡ ፱፡፡ ፩፡ ዮሐ፡ ፩፡ ፯፡፡

፲፭፡ ስለዚህም፡ እርሱ፡ *ለአዲስ፡ ኪዳን፡ ማእከላዊ፡ሆነ። በሞቱ፡ መድኃኒት፡ ይሆን፡ ዘንድ፡ ከፊተኛ፡ ኪዳን፡ በታች፡ ከሆነ፡ †መተላለፍ፡ ለዘላለም፡ **ርስትም፡ የተጸሩት፡ ተስፋውን፡ ያገኙ፡ ዘንድ።

ም፡ ፲፪፡ ፳፬፡፡ ፩፡ ጢሞ፡ ፪፡ ፭፡፡ †ሮሜ፡ ፫፡ ፳፭፡፡
**የሐዋ፡ ፳፮፡ ፲፰፡፡

፲፮፡ ሥርዓትም፡ወደለች፡የሠራት፡ሞት፡ይመጣ፡ ዘንድ፡ በግድ፡ይፈለጋል።

፲፯፡ ሥርዓት፡በሞቱ፡ሰዎች፡ጸንታለችና፡ትረገም፡ ዘንድ፡አይቻላትም፡በሠራት፡ሕይወት፡ሁሉ።

፲፰፡ ስለዚህም፡ የፊተኛዪቱ፡ደግሞ፡ ያለ፡ ደም፡ አልተገረከችም።

፲፱፡ ሙሴም፡ የኦሪትን፡ ትእዛዝ፡ሁሉ፡ ለሕዝብ፡ ሁሉ፡ከተናገረ፡ በኋላ፡ የበሬና፡የፍየል፡ ደም፡ ወስደ፡ ውኃም፡ ቀይ፡ ጸጕርም፡ ስምዕዛም፡ በመጽሐፉም፡ ረጨው፡ በሕዝቡም፡ ሁሉ፡ላይ።

፳፡ እንዲህ፡ ሲል። *ይህ፡ ነው፡ የኪዳኑ፡ደም፡ እግዚአብሔር፡ ያዘዛችሁት። ዘፀአ፡ ፳፬፡ ፮፡—፰፡፡

፳፩፡ እንዲሁም፡ድንኳኑን፡የማገልገልንም፡እቃ፡ ሁሉ፡ በደም፡ ረጨችው። ዘሌዋ፡ ፰፡ ፲፡ ፲፭፡ ፲፱፡፡

፳፪፡ በኦሪት፡*ሕግም፡ሁሉ፡ በደም፡ይነጻልና፡ደምም፡ሳይፈስ፡†ስርየት፡የለም። *ዘሌዋ፡ ፲፯፡ ፲፩፡፡
†ኤፌ፡ ፩፡ ፯፡፡

፳፫፡ የግድም፡የሰማያዊት፡ነገር፡ *ምሳሌ፡ በዚህ፡ ትነጻ፡ዘንድ፡ይገባ፡ነበር፡ ሰማያዊቱ፡ ግን፡ከዚህ፡ በምትበልጠው፡ መሥዋዕት። *ም፡ ፰፡ ፭፡፡

፳፬፡ ክርስቶስ፡በእጅ፡ወደ፡ተሰራው፡መቅደስ፡የውነተኛው፡ምሳሌ፡ወደ፡ሆነው፡ የገባ፡ አይደለውምና። ወደርስዋ፡ወደ፡ ሰማይ፡ገባ፡እንጅ፡ዛሬ፡ በእግዚአብሔር፡ፊት፡ስለኛ፡*ይታይልን፡ዘንድ። *ቈ፡ ፲፩፡ ፲፪፡፡
፩፡ ዮሐ፡ ፪፡ ፩፡፡

፳፭፡ ራሱንም፡ ብዙ፡ ጊዜ፡ የሚያቀርብ፡ እንደይሆን፡የካህናት፡ አለቃ፡ወደ፡ መቅደስ፡እንዲገባ፡ ባመት፡ ባመት፡ በሌላው፡ *ደም። *ዘፀአ፡ ፴፡ ፲፡፡

፳፮፡ ያስ፡ባይሆን፡ብዙ፡ጊዜ፡ ሕማማት፡ ይቀበል፡

ዘንድ፡ይገባው፡ ነበረ፡ ዓለም፡ ከተፈጠረ፡ ጀምሮ። ነገር፡ግን፡ ዛሬ፡ *በኋለኛው፡ ዘመን፡ አንድ ግዜ፡ ተገለጠ፡ ኃጢአትን፡ ይሽር፡ ዘንድ፡ በራሱ፡ መሥዋዕት።
*ም፡ ፩፤ ፪፡፡ ፩፤ ቀር፡ ፲፤ ፲፩፡፡

፳፯፤ በሰዎችም፡ ላይ፡ አንድ፡ ተሠራ፡ *አንድ ግዜ፡ ይሞቱ፡ ዘንድ፡ ከሞቱ፡ በኋላም፡ ፍርድ፡ እንዲለባቸው፡ ዘፍ፡ ፫፤ ፲፱፡፡

፳፰፤ እንደሁም፡ ክርስቶስ፡ ራሱን፡ *አንድ ግዜ፡ አቅርቦ፡ የብዙ፡ ሰዎችን፡ ኃጢአት፡ ያስወግድ፡ ዘንድ፡ ተሁለተኛ፡ጊዜ፡ያለ፡ኃጢአት፡ይታያል፡ ደጅ፡ለሚጸኑ ት፡ **ለመድኀኒት። *ም፡ ፲፤ ፲፪፡፡ †ኢሳ፡ ፶፫፤ ፲፪፡፡
**፩፤ ተሰ፡ ፩፤ ፲፡፡

ምዕራፍ፡ ፲፤

፩፤ ኦሪት፡የሚመጣው፡የበጎ፡ ነገር፡ጽላል፡አላትና፡ የነገሩ፡አይነተኛ፡*ሥእል፡ ግን፡አይደላትም። ስለዚህም፡ ባመት፡ ባመት፡ ይገመው፡ በሚያቀርብዋቸው፡ በማይጨርሱም፡ መሥዋዕቶች፡ እሊያን፡ የሚቀርቡትን፡ ተትፈጽም፡ ዘንድ፡ከቶ፡ አይቻላትም።
*ቈላ፡ ፪፤ ፲፯፤ ፲፯፡፡ †ም፡ ፱፤ ፳፯፡፡

፪፤ ተፈጽመውስ፡ቢሆኑ፡ ከማቅረብን፡ባላረፉን። የሚያቀርብዋቸው፡ ሕሊናቸው፡ ከኃጢአት፡ ስለ፡ ነጻች፡ እርሳቸው፡ አንድ ግዜ፡ ከነጹ።

፫፤ ነገር፡ግን፡በልያ፡ መሥዋዕቶች። ባመት፡ ባመት፡ *የኃጢአት፡ መታሰቢያ፡ ነው። *ዘሌዋ፡ ፲፮፡ ፳፩፡፡
ኢያ፡ ፴፤ ፲፫፡፡

፬፤ የበሬና፡ የፍየል፡ ደም፡ ኃጢአትን፡ ይደመስስ፡ ዘንድ፡ አይችልምና። መዝ፡ ፶፤ ፯፡፡

፭፤ ስለዚህም፡ ወደ፡ ዓለም፡ሲገባ፡ እንደህ ፡ ይላል።ቍርባንን፡ መሥዋዕትንም፡ አልሻህም፡ነገር፡ ግን፡ ሥጋዬን፡ አዘጋጀህልኝ።

፮፤ የሚቃጠልና፡ የኃጢአት፡ መሥዋዕት፡ አልሻህም። ሚክ፡ ፮፤ ፯፡፡

፯፤ የዚያን፡ጊዜ፡አልሁ። እነሆኝ፡እኔ፡እመጣለሁ። (በመጽሐፍ፡ ጥቅልል፡ስለኔ፡ ተጽፎዋል)፡ ፈቃድህን፡ አደርግ፡ ዘንድ፡ አቤቱ።

፰፤ ከዚህም፡በላይ፡ ሲል። የእርድ፡ መሥዋዕትንና፡ የእህል፡ ቍርባን፡ የሚቃጠልና፡ የኃጢአት፡ መሥዋዕት፡ አልሻህም፡ አልወደድህም። (እሌህ፡በኦሪት፡ ሥርዓት፡ ይቀረባሉ።) የዚያን፡ ጊዜ፡ አለ።

፱፤ እነሆ፡ እኔ፡ እመጣለሁ፡ ፈቃድህን፡ አደርግ፡ ዘንድ፡ አቤቱ። የፊተኛውን፡ ነቀለ፡ የኋለኛውን፡ ሊያቆም።

፲፤ በዚችም፡ ፈቃድ፡ እኛ፡ የተቀደስነ፡ ነነ፡ በየሱስ፡ ክርስቶስ፡ በሥጋው፡ ቍርባን፡ *አንድ ግዜ፡ በሆነው።
*ም፡ ፱፤ ፲፪፤ ፳፰፡፡ ቈላ፡ ፩፤ ፪፡፡ ፩፤ጴጥ፡ ፪፤ ፳፬፡፡

፲፩፤ ካህንም፡ ሁሉ፡ ዕለት፡ ዕለት፡ አገልጋይ፡ ሁኖ፡ ይቆማል፡ ብዙ፡ ጊዜም፡ እልያን፡ መሥዋዕቶች፡ ደግሞ፡ያቀርባል፡ ኃጢአት፡ ያስወግዱ፡ ዘንድ፡ ከቶ፡የማይቻላቸውን። ቍ፡ ፩፤ ፯፤ ፲፩፡፡

፲፪፤ እርሱ፡ ግን፡ስለ፡ ኃጢአት፡ *አንዲት፡ መሥዋዕት፡ባቀረበ፡ጊዜ፡ ለዘላለም፡ በእግዚአብሔር፡ቀኝ፡ ተቀመጠ። *ቍ፡ ፲፤ ፲፬፡፡ ም፡ ፩፤ ፲፫፡፡

፲፫፤ ከዚያም፡ ይጠብቃል፡ጸላቶቹ፡ ለእግሩ፡ ድጋ፡ እስኪጣሉ፡ ድረስ። መዝ፡ ፻፲፤ ፩፡፡

፲፬፤ *ባንዲት ፡ ቍርባን ፡ የሚቀደሱትን ፡ ለዘላለም፡ፈጽሞዋልና። ቍ፡ ፲፪፡፡ ም፡ ፱፤ ፳፮፡፡

፲፭፤ መንፈስ፡ ቅዱስም፡ ደግሞ፡ መሰከረልነ። አስቀድሞ፡ ብልዋልና።

፲፮፤ ይህች፡ሥርዓቴ፡ ናት፡ የምሠራላቸው፡ ከዚያች፡ ቀን፡ በኋላ፡ ይላል፡ እግዚአብሔር፡ ሕጋቴን፡ በልባቸው፡ እኖራለሁ፡ በሕሊናቸውም፡ *እጽፈዋለሁ።
*ኤር፡ ፴፩፤ ፴፫፤ ፴፬፡፡

፲፯፤ ደግሞም፡ኃጢአታቸውን፡ በደላቸውንም፡ደግሞ፡ አላስብም።

፲፰፤ የርሳቸውም ፡ ስርየት ፡ ሳለች ፡ ደግሞ፡ ወደ፡ ቍርባን፡ስለ፡ኃጢአት፡አያሻም። ኢሳ፡ ፵፫፤ ፳፭፡፡

፲፱፤ አሁንም፡ ወንድሞቼ፡ ሆይ፡ ለኛ፡ ድፍረት፡ ሳለነ፡ ወደ፡ *መቅደስ፡ መግቢያ፡ በየሱስ፡ ክርስቶስ፡ ተደም። *፪፤ ጴጥ፡ ፩፤ ፲፩፡፡ †ኤፌ፡ ፪፤ ፲፰፡፡ ፫፡ ፫፤ ፲፪፡፡

፳፤ ላዲስና፡ ለሕያው፡ *መንገድ፡ የቀደሰልነ፡ በመጋረጃ። ይህ፡ማለት፡ ተበሥጋው። *ም፡ ፱፤ ፰፡፡
†ዮሐ፡ ፪፤ ፳፩፡፡

፳፩፤ ታላቅ፡ካህንም፡ሳለነ፡በእግዚአብሔር፡ቤት፡ ላይ። ም፡ ፬፤ ፲፬፤ ፲፭፡፡

፳፪፤ እንቅረብ፡ *በውነተኛ፡ ልብ፡ በፍጹምም፡ ሃይማኖት። ልባችነንም፡ ከክፉ፡ ሕሊና፡ ተረጭተን፡ ሥጋችነንም፡ በጽሩ፡ ተውኃ፡ ታፅበን። *ም፡ ፬፤ ፲፮፡፡
†ሕዝቅ፡ ፴፯፤ ፳፭፡፡ ቲቶ፡ ፫፤ ፭፡፡

፳፫፤ ተስፋችነንም፡ በመግለጽ፡ እንጸና፡ ሳንዘነብል፡ተስፋ፡የሰጠነ፡እርሱ፡ የታመነ፡ነውና።
ም፡ ፬፤ ፲፬፡፡ ፲፩፤ ፲፩፡፡

፳፬፤ እርሱ፡በርሳችንም፡እንጠባበቅ፡ ለፍቅር፡ *ለመልካም፡ነገር፡እናሰቀና፡ዘንድ። *ም፡ ፲፫፤ ፩፤ ፳፩፡፡
ዮሐ፡ ፲፫፤ ፴፬፡፡

፳፭፤ መከማቻችነንም፡ አንተው፡ አያሌ፡ ሰዎች፡ ልማድ፡ እንደደረጉ፡ እርሱ፡ በርሳችሁ፡ ተጸናኑ፡ እንጂ። ይህነን፡በሚያህል፡ ጨምራችሁ፡ ያ፡ ቀን፡ እንደ፡ ተቀረበ፡ አይታችሁ። *ቍ፡ ፴፯፡፡ ፩፤ ተሰ፡ ፭፤ ፪፤ ፬፡፡

፳፮፤ ማንም፡ ኃጢአት፡ *በፈቃዱ፡ ቢሰራ፡ የእውነትን፡እውቀት፡ ከተቀበለ፡ በኋላ፡ ስለ፡ ኃጢአት፡ መሥዋዕት፡አይሆንምና። *ም፡ ፮፤ ፮፡፡
ዘኍል፡ ፲፭፤ ፴፤ ፴፩፡፡

፳፯፤ የሚያስፈራ፡ ፍርድ፡ *ተዘጋጅቶለታል፡ እንጂ፡ የሳትም፡ ቅንዓት፡ ጸላቶችን፡ ተየምትበላ።
*ም፡ ፱፤ ፳፯፡፡ †ዘደግ፡ ፴፪፤ ፳፪። ኢሳ፡ ፳፮፤ ፲፩፡፡
ሰፎን፡ ፩፤ ፲፰፡፡ ፫፤ ፰፡፡

፳፰፤ የሙሴን፡ ኦሪት፡ የተላለፈ፡ ሁለት፡ ሰዎች፡

ወይም፡ሶስት፡*በመሰከሩበት፡ጊዜ፡ያለ፡ምሕረት፡ይ
ሞታል። *ዘኍ፡ ፲፭፡ ፴:: ዘዳግ፡ ፲፯፡ ፮::

፳፱፡ *ስንት፡ከፋ፡ሥቃይ፡እጅግ፡የሚገባው፡ይመ
ስላችኋል፡ የእግዚአብሔርን፡ ልጅ፡ †የረገጠ። የተቀ
ደሰበቱንም፡ የኪዳኑን፡ ደም፡ **ያረከሰ። የጸጋውን
ም፡መንፈስ፡ ††የሰደበ። *ም፡ ፪፡ ፪፡ ፫::
†ዮሐ፡ ፲፫፡ ፲፰:: **፩፡ ቆሮ፡ ፲፩፡ ፳፭፡ ፳፱::
††ማቴ፡ ፲፪፡ ፴፩::

፴፡ እኛም፡ እናውቃለን፡ ያለውን ። *በቀል፡ ለኔ፡
ነው፡እኔ፡ ፍዳ፡ እሰጣለሁ። ደግሞም፡ አለ። እግዚአ
ብሔር፡ በሕዝቡ፡ ይፈርዳል። *ዘዳግ ፴፪፡ ፴፭፡ ፴፮፡
መዝ፡ ፶፡ ፬::

፴፩፡ እጅግ፡ ያስፈራል፡ ያስገርምማል፡ በሕያው፡
እግዚአብሔር፡እጅ፡መውደቅ።

፴፪፡ ነገር፡ግን፡ ብርሃን፡ የተቀበላችሁባትን፡ የፊተ
ኛዪቱን፡ቀን፡አስቡ። *የሕማማትን፡ታላቅ፡ገድል፡እ
ንደ፡ ተጋደላችሁ። *ፊል፡ ፩፡ ፳፱::
፩፡ ተሰ፡ ፪፡ ፲፬::

፴፫፡ እላንትም፡ ራሳችሁ፡ በስድብ ፡ በመከራም፡
ለሰዎች፡ማላገጫ፡ ሆናችሁ። ደግሞም፡አንድ፡ ሆናች
ሁ፡ በዚህ፡ መንገድ፡ ከሔዱት፡ ጋራ።

፴፬፡ በግዞቴም፡ ደግሞ፡ከኔ፡ ጋራ፡መከራ፡ ተቀበላ
ችሁና፡ የከብታችሁንም፡ ምርኮ፡ በደስታ፡ታገሣችሁ፡
*በሰማይ፡ የተሻለና፡የጸና፡ገንዘብ፡ እንዳላችሁ፡ታው
ቃላችሁና። *ማቴ፡ ፮፡ ፳:: ሉቃ፡ ፲፪፡ ፴፫::

፴፭፡ እንግዲህም፡ መታመናችሁን፡ አትጣሉ፡ ታ
ላቅ፡ ዋጋ፡ ያለውን። ም፡ ፲፩፡ ፳፮::

፴፮፡ ትዕግሥት፡ይገባችኋልና፡ የእግዚአብሔርን፡
ፈቃድ፡ ታደርጉ፡ ዘንድ፡ *ተስፋም፡ ትወሰዱ፡ ዘንድ።
*ሉቃ፡ ፳፩፡ ፲፱::

፴፯፡ ቀሊል፡ ነውና፡ ጥቂትም፡ የሚመጣው፡ እስ
ኪመጣ፡ድረስ፡አይዘገይምም። ኢሳ፡ ፳፮፡ ፳::
አንባ፡ ፪፡ ፫፡ ፬::

፴፰፡ ጻድቅም፡ *በሃይማኖት፡ ይድናል። ማንም፡
ቢታክት፡ ግን፡ ነፍሴ፡ አትወደውም። *አንባ፡ ፪፡ ፬::

፴፱፡ እኛ፡ግን፡ለጥፋት፡ከሚርቁት፡*አይደለነም፡
ነፍሳቸውን፡ †ለማደን፡ ከሚያምኑት፡ እንጂ።
*ኢሳ፡ ፳፰፡ ፲፮:: †፩፡ ጴጥ፡ ፩፡ ፱::

ምዕራፍ፡ ፲፩፡

፩፡ *ሃይማኖትም፡ ማመን፡ ነው፡ ተስፋ፡ በተደረገ
ችው፡ነገር።†የማትታየውንም፡ነገር፡ማየት።
*ም፡ ፲፡ ፴፰:: †ዮሐ፡ ፳፡ ፳፱:: ሮሜ፡ ፬፡ ፲፰::

፪፡ በዚህም፡ ለሽማግሌች፡ ተመሰከረላቸው።

፫፡ በሃይማኖት፡እናውቃለን፡ ዓለሞች፡ በእግዚአ
ብሔር፡ ቃል፡ እንደ፡ ተዘጋጁ፡ ከማይታየውም፡ነገር፡
የሚታየው፡እንደ፡ ሆነ። ም፡ ፩፡ ፪::መዝ፡ ፴፫፡ ፮::

፬፡ በሃይማኖት፡*አቤል፡ መሥዋዕት፡ ለእግዚአብ
ሔር፡አቀረበ፡ ከቃየል፡ መሥዋዕት፡ የሚሻል። በርሱ
ም፡ተመሰከረለት፡ ጻድቅ፡ እንደ፡ ሆነ። እግዚአብሔ
ር፡ ለቍርባኑ፡ ሲመሰከረለት። በዚህም፡እርሱ፡ ከሞ
ተ፡በኋላ፡ዛሬ፡†ይናገርበታል። *ዘፍ፡ ፬፡ ፬፡ ፭፡ ፲::
†ም፡ ፲፪፡ ፳፬::

፭፡ በሃይማኖት፡ሄኖክ፡ ከዚህ፡ ዓለም፡ ወጣ፡ *ሞ
ትንም፡አላየም።ከዚያም፡ በኋላ፡ አልተገኘም፡ እግ
ዚአብሔር፡ አውጥቶታልና ። ሳያወጣው፡ ተመሰከ
ረለት፡ ነበርና፡ እግዚአብሔርን፡ እንደ፡ሰመረ።
*ዘፍ፡ ፭፡ ፳፬:: ዮሐ፡ ፳፡ ፶፩::

፮፡ ያለ፡ሃይማኖት፡ ግን፡ አይቻልም፡ እግዚአብሔ
ርን፡ *ያሰምሩት፡ ዘንድ። ወደ፡ እግዚአብሔር፡ የሚ
መጣ፡ይገባዋልና፡ያምን፡ ዘንድ፡ እርሱ፡ እንዳለ፡ በጽ
ኑ፡ ለሚሹትም፡ †ዋጋቸውን፡ እንዲሰጥ።
*ኤር፡ ፳፱፡ ፫:: ሮሜ፡ ፲፬፡ ፳፫:: †ዓሞ፡ ፳፡ ፬::
መልክ፡ ፫፡ ፲፬፡ ፲፯::

፯፡ በሃይማኖት፡ *ኖህ፡ገና፡ የማይታየውን፡ ነገር፡ ጉ
ወቀ፡ ጊዜ፡ ፈራ፡ መርከብም፡ አበጀ፡ የቤቱን፡ሰዎች፡
ለማደን። በዚያውም፡ ዓለምን፡ አስኰነነበት፡ በሃይ
ማኖት፡ የሚገኘውንም፡ †ጽድቅ፡ ወራሽ፡ ሆነ።
*ዘፍ፡ ፯፡ ፳:: †ሮሜ፡ ፫፡ ፳፪፡ ፳፬:: ና፡ ፬፡ ፳::

፰፡ በሃይማኖት፡ አብርሃም፡ በተጸራ፡ ጊዜ፡ ታዘዘ፡
ለርስት፡ ወደሚወርሰው፡ ስፍራ፡ ይወጣ፡ ዘንድ። ወ
ዴት፡ የሚደርስበትንም፡ ሳያውቅ፡ ወጣ።
ዘፍ፡ ፲፪፡ ፩—፬::

፱፡ በሃይማኖት፡ተቀመጠ፡ ተስፋ፡ በተሰጠው፡ም
ድር፡ እንደ፡ ስደተኛ፡ በድንኳንም፡ ተቀመጠ፡ የዚያ
ችን፡ የተስፋውን፡ ርስት፡ ከሚወርሱ፡ ከይስሐቅና፡
ከያዕቆብ፡ጋራ። ዘፍ፡ ፲፪፡ ፰:: ና፡ ፲፬፡ ፲፱::

፲፡ መሠረት፡ያላትን፡አገር፡ተስፋ፡ያደርግ፡ ነበረና።
ሠሪዋ፡ አድራጊዋም፡እግዚአብሔር፡ የሚሆን።
ም፡ ፲፪፡ ፳፪:: ኢሳ፡ ፴፫፡ ፳::

፲፩፡ በሃይማኖት፡ደግሞ፡ መካን፡ የነበረች፡ ሳራ፡ ኃ
ይል፡ አገኘች፡ ዘር፡ ለመቀበል፡ በማትወልድበትም፡
ጊዜ፡ ወለደች፡ ተስፋ፡ የሰጣት፡ የታመነ፡ እንደ፡ ሆነ፡
ስላመነች። ዘፍ፡ ፳፩፡ ፪::

፲፪፡ እንደዚሁም፡*ካንዱ፡ ተወለዱ፡ እርሱም፡ ሥጋ
ው፡ከሞተው። ብዛታቸው፡ እንደ፡ሰማይ፡†ከዋክብ
ት፡ የሆኑ፡ሰዎች፡ እንደማይቈጠርም፡ በባሕር፡ ዳር፡
እንዳለ፡አሸዋ። *ሮሜ፡ ፬፡ ፲፱:: †ዘፍ፡ ፲፭፡ ፭::
ና፡ ፳፪፡ ፲፯::

፲፫፡ እሊያ፡ ሁሉ፡ በሃይማኖት፡ ሞቱ፡ *ተስፋ፡ የተ
ሰጣቸውንም፡ አልወሰዱም፡ ነገር፡ ግን፡ †ከሩቅ፡ አዩ
ዋት፡ በደስታም፡ ተመለከትዋት፡ ስደተኞች፡ መጻተ
ኞችም፡ **በምድር፡ ላይ፡ እንደ፡ሆኑ፡አመኑ።
*ቍ፡ ፴፱:: †ዘኍ፡ ፳፬፡ ፲፯::
**ዘፍ፡ ፳፫፡ ፬:: ፵፯፡ ፱:: መዝ፡ ፴፱፡ ፲፫::

፲፬፡ ይህነን፡ እንዲህ፡ የሚሉ፡ ያስታውቃሉና፡ አገ
ራቸውን፡ እንዲሹ።

፲፭፤ ከርስዋ፡ የወጡባትንስ፡ አገር፡ አስበው፡ ቢሆ
ኑ፡ ይመለሱባት፡ ጊዜ፡ ነበራቸው።
፲፮፤ አሁን፡ግን፡እርሳቸው፡ ከርስዋ፡ወደ፡ተሻለች፡
ማለት፡ ወደ፡ሰማያዊት፡ አገር፡ ይናፍቃሉ። ስለዚህ
ም፡እግዚአብሔር፡ አያፍርም፡ *አምላካቸው፡ ይባ
ል፡ ዘንድ፡ ከተማ፡†አዘጋጅቶላቸዋልና።
*ማቴ፡ ፳፪፡ ፴፩፡ ፴፪። †ቈ፡ ፲፡
፲፯፤ በሃይማኖት፤ አብርሃም፡ ይስሐቅን፡ አቀረበ
ው፡ በተፈተነ፡ጊዜ። አንድዬ፡ንልጁንም፡ አሳረገው፡ተ
ስፋ፡ የተቀበለበቱን።　ዘፍ፡ ፳፪፡ ፪፡ ፲።
፲፰፤ የተባለለትን፡ *በይስሐቅ፡ ዘር፡ ይጸራልሃል።
*ዘፍ፡ ፳፩፡ ፲፪።
፲፱፤ እግዚአብሔር፡ከሙታን፡ደግሞ፡ ያስነሣ፡ዘን
ድ፡ እንዲችል፡ አስቦ። በምሳሌም፡ ከዚያ፡ ተመልሶ፡
ወሰደው።　ሮሜ፡ ፬፡ ፲፯።
፳፤ በሃይማኖት፡ ይስሐቅ፡ ያዕቆብንና፡ ዔሳውን፡
ባረከ፡ ስለሚመጣው፡ ነገር።　ዘፍ፡ ፳፯፡ ፳፰።
፳፩፤ በሃይማኖት፡ ያዕቆብ፡ ሞቱ፡ በቀረበ፡ ጊዜ፡ የ
ዮሴፍን፡ *ልጆች፡ ኢያንዳንዱ፡ ባረከ፡ †በበትሩ፡ ጫ
ፍም፡ ጠግቶ፡ ሰገደ።　*ዘፍ፡ ፵፰፡ ፲፭።
†ዘፍ፡ ፵፯፡ ፴፩።
፳፪፤ በሃይማኖት፡ ዮሴፍ፡ ሲሞት፡ የእሥራኤል
ን፡ልጆች፡መውጣት፡አሰበ፡ ስለ፡ አጽንቱም፡ አዘዛቸ
ው።　ዘፍ፡ ፶፡ ፳፬፡ ፳፭።
፳፫፤ በሃይማኖት፡ ሙሴ፡ በተወለደ፡ ጊዜ፡ ከወላ
ጆቹ፡ሦስት፡ወር፡ተሸሸገ፡ ሕፃኑ፡ ውብ፡ እንደሆነ፡ አይ
ተዋልና፡ የንጉሡንም፡ ትእዛዝ፡ አልፈሩም።
ዘፀአ፡ ፩፡ ፳፪፡ ፳፫። ፍ፡ ፪፡ ፪።
፳፬፤ በሃይማኖት፡ ሙሴ፡ ባደገ፡ ጊዜ፡ካደ፡ የፈርዖ
ን፡ የልጁ፡ ልጅ፡ እንደ፡ ይባል።　ዘፀአ፡ ፪፡ ፲፡—፲፪።
፳፭፤ መከራም፡ይቀበል፡ዘንድ፡ከእግዚአብሔር፡
ወገን፡ጋራ፡ወደደ፡ በኃጢአት፡ጥቂት፡ ዘመን፡ ደስ፡ ኪ
ለው፡ ይልቅ።
፳፮፤ የክርስቶስን፡*ስድብ፡ በርሱ፡ ዘንድ፡ የሚበል
ጥ፡ ባለጠግነት፡ አድርጓልና፡ ከምሥር፡ ከብት፡ ሁሉ፡
ይልቅ። †የዋጋውን፡ መልካምነት፡ ተመልክቶ፡ ነበ
ረና።　*ም፡ ፲፫፡ ፲፫። ዘፀአ፡ ፬፡ ፳፪። †ም፡ ፲፡ ፴፭።
፳፯፤ በሃይማኖት፡ የምሥርን፡አገር፡ተወ፡ የንጉሠ
ንም፡*ቍጣ፡ አልፈራም፡ የማያየውም፡ †እንደሚ
ያየው፡ ስለ፡ ሆነለት፡ ታገሠ።　*ዘፀአ፡ ፲፡ ፲፩፡ ፳፰።
†ዘፀአ ፫፡ ፯።
፳፰፤ በሃይማኖት፡ ፋሲካ፡ አደረገ፡ ደምም፡ ረጨ፡
የበኵሩ፡ አጥፊ፡ እርሳቸውን፡ እንዳይነካ።
ዘፀአ፡ ፲፪፡ ፲፪፡ ፲፰።
፳፱፤ በሃይማኖት፡ የእሥራኤል፡ልጆች*የኤርትራ
ን፡ ባሕር፡ ተሻገሩ፡ በደረቅ፡ ምድር፡ እንደሚያልፉ።
የምሥር፡ ሰዎች፡ግን፡ይከተሉዋቸው፡ ዘንድ፡ ሲሞክ
ሩ፡ ተሠጠሙ።　*ዘፀአ፡ ፲፬፡ ፳፪።

፴፤ በሃይማኖት፤ የዪሪኮ፡*ቅጥሮች፡ ወደቁ፡ሰባት፡
ቀን፡ በከበብዋቸው፡ጊዜ።　*ኢያ፡ ፯፡ ፳።
፴፩፤ በሃይማኖት፡ ረሓብ፡ ጋለሞታ፡ ከማያምኑ፡
ጋራ፡ አልጠፋችም፡ ጕበኞችን፡ በደኅንነት፡ ስለተቀበ
ለች።　ኢያ፡ ፪፡ ፲፰። ፯፡ ፲፫፡ ፳፫። ያዕ፡ ፪፡ ፳፭።
፴፪፤ ደግሞም፡ምን፡ እላለሁ። ጊዜው፡ ያጥርብኛ
ልና፡ ልናገር፡ ብሻ፡ ከጌደዎን፡ ከባራቅም፡ ከሰምሶን
ም፡ ከዮፍታሔንም፡ ከዳዊትም፡ ከሳሙኤልም፡ ከነ
ቢያትም።　መሳ፡ ፯፡ ፲፩። መሳ፡ ፬፡ ፯። ፍ፡ ፲፭፡ ፳።
መሳ፡ ፲፪፡ ፫። ፪፡ ሳሙ፡ ፪፡ ፬።
፴፫፤ በሃይማኖት፡ *መንግሥታትን፡ ያሸነፉ፡ ጽድ
ቅ፡አደረጉ። ተስፋ፡ የተሰጣቸውን፡ ተቀበሉ። †የአና
ብስትን፡ አፍ፡ ዘጉ።　*፪፡ ሳሙ፡ ፰፡ ፩፡ ፲፬።
†ዳን፡ ፯፡ ፳፪።
፴፬፤ የሳቱን፡ኃይል፡አጠፉ። ከሰይፍ፡ ስለት፡ዳኑ።
ከድካም፡ በረቱ፡ በመጋደል፡ጐለመሱ። የአሕዛብን፡
ጭፍራ፡አሸሹ።　ዳን፡ ፫፡ ፳፫።
፴፭፤ ሴቶች፡ሙታናቸውን፡ተቀበሉ፡ከሞት፡በመ
ነሣት፡ሌሎችም፡ተሣቀዩ፡ መዳንም፡ አልወደዱም፡
የሚበልጥ፡ትንሣኤ፡ ይቀበሉ፡ ዘንድ።
፩፡ ነገሥ፡ ፲፯፡ ፳፫። ፪፡ ነገሥ፡ ፬፡ ፴፯።
፴፮፤ ሌሎችም፡ በልግጥ፡ተፈተኑ፡ በግርፋትም፡ደ
ግሞም፡ በግዞት፡ በመታሠርም።　ኤር፡ ፳፡ ፪።
፴፯፤ በድንጊያ፡*ተወገሩ። በመጋዝ፡ተሰነጠቁ። መ
ከራ፡ተቀበሉ። †በሰይፍ፡በመቈረጥ፡ሞቱ። ማቅም፡
በግና፡ የፍየል፡ ለምድ፡ ለብሰው፡ ዞሩ፡ ታርዘው፡ ተቸ
ግረውም፡ ጐስቍለውም።　*የሐዋ፡ ፫፡ ፶፪።
†፩፡ ሳሙ፡ ፳፪፡ ፲፰።
፴፰፤ አሌህ፡ ዓለም፡ የማይገባቸው። ጠፍተው፡
ነበሩ፡ በበረሃ፡ በተራራም፡ በዋሻው፡ በምድርም፡ ጕ
ድጓድ።　፩፡ ነገሥ፡ ፲፰፡ ፬።
፴፱፤ እሌህም፡ ሁሉ፡ በሃይማኖታቸው፡ የተመሰ
ከረላቸው፡ ተስፋቸውን፡ አላገኙም።
፵፤ እግዚአብሔር፡ አስቀድሞ፡ ለኛ፡ የሚበልጠ
ውን፡ ነገር፡ አይተልናልና፡ እርሳቸው፡ ያለኛ፡ እንዳይ
ፈጸሙ።　ም፡ ፲፪፡ ፳፫።

## ምዕራፍ፡ ፲፪፡

፩፤ ስለዚህም፡ ለኛ፡ እሌህን፡ የሚያህሉ፡ ምስክ
ሮች፡ ሳሉን፡ እንደ፡ ደመና፡ የከበቡን። ሸክምን፡ሁሉ፡
ከኛ፡ አውጥተን፡ እንጣል፡ ፈጥኖም፡ የምትተባተበ
ውን፡*ኃጢአት፡ በተመደበልንም፡ †ሩጫ፡በትዕግሥ
ት፡ እንሩጥ።　*ሮሜ፡ ፫፡ ፳፩። †ም፡ ፲፡ ፴፯።
፩፡ ቆሮ፡ ፱፡ ፳፬።
፪፤ ወደ፡ ሃይማኖታችን፡ አለቃ፡ወደ፡ፈጻሚዋም፡
እንይ፡ ወደ፡ የሱስ። ደህ፡ በፊቱ፡ ስላለ፡ ደስታ፡ መስ
ቀሉን፡ የተሸከመ፡ ኃፍረትንም፡ አላሰበም፡ በእግዚ
አብሔር፡በዙፋኑ፡ቀኝ፡ ተቀመጠ። ም፡ ፪፡ ፲፡—፲፫።
ፊል፡ ፪፡ ፰።

፫፤ አሁንም፡ አዩ፡ ደህ፡ ምን፡ የሚያህል፡ ጸብ፡ ከኃጢአተኞች፡ በራሱ፡ ላይ፡ *እንደታገሠ፡ እንዳትደክሙ፡ ነፍሳችሁ፡ እንዳታክት።
*ሉቃ፡ ፪፤ ፴፬። ዮሐ፡ ፲፭፤ ፲፰፤ ፳።

፬፤ ገና፡ ደም፡ እስከ፡ ማፍሰስ፡ አልደረሳችሁምና፡ ከኃጢአት፡ ጋራ፡ በመጋደል።
ም፡ ፲፤ ፴፫።

፭፤ ትእዛዚቱንም፡ ረሳችሁ፡እንደ፡ ልጆች፡ከልብ፡ የምትላችሁን። ልጄ፡ ሆይ፡ልብህ፡ አይጨነቅ፡ እግዚአብሔር፡ በገሠጸህ፡ ጊዜ፡ በቀጣህም፡ ጊዜ፡ አትድከም።
ምሳ፡ ፫፤ ፲፩፤ ፲፪።

፮፤ እግዚአብሔር፡ የወደደውን፡ ይቀጣዋልና፡ የሚቀበለውንም፡ ልጅ፡ ሁሉ፡ ይገርፋል።
ራእ፡ ፫፤ ፲፱።

፯፤ ተግሣፅን፡ ብትሸከሙ፡ እግዚአብሔር፡እንደ፡ ልጆች፡ ይቀበላችኋል። ምን፡ ልጅ፡ ነውና፡አባቱ፡የማይቀጣው።
ዘዳግ፡ ፰፤ ፭። ፪፤ ሳሙኤ፡ ፯፤ ፲፬።

፰፤ እላንተስ፡ ያለ፡ ቅጣት፡ ብትሆኑ፡ እርሳቸው፡ ሁላቸው፡ ያገኙዋት፡ እላንት፡ አውነተኞ፡ ልጆች፡ አይደላችሁም፡ዲቃሎች፡እንጂ። መዝ፡ ፸፫፤ ፲፫—፲፭።

፱፤ የሥጋ፡ አባቶቻችን፡ቢገሥፁን፡የምናፍራቸው፡ ከሆነ፡ እንዴት፡ እጅግ፡ ይገባነ፡ለመንፈስ፡ አባታችን፡ እንገዛና፡ እንድን፡ ዘንድ። ዘኍል፡ ፲፮፤ ፳፪፤ ፳፯።

፲፤ እለዚያ፡ ለጥቂት፡ ዘመን፡ ይቀጡናልና፡ እንደ፡ ወደዱ። እርሱ፡ ግን፡ እንዲረባነ፡ ነው፡ ከቅድስናው፡ እንወስድ፡ ዘንድ።
፩፤ ጴጥ፡ ፩፤ ፲፭፤ ፲፮።

፲፩፤ ተግሣጽ፡ ሁሉ፡ግን፡ ለጊዜው፡ደስ፡አያሰኝም፡ ያሳዝናል፡ እንጂ። ኋላ፡ ግን፡ የሰላምና፡ የጽድቅ፡ ፍሬ፡ ያፈራል፡ ለለመዱበት።
ኢሳ፡ ፴፪፤ ፲፯።
ያዕ፡ ፫፤ ፲፰።

፲፪፤ ስለዚህም፡ የስለለውን፡ እጆቻችሁን፡ አጽኑ፡ ያነከሰውንም፡ ጕልበታችሁን።
ኢሳ፡ ፴፭፤ ፫።

፲፫፤ ለግራችሁም፡የቀና፡መንገድ፡አድርጉ፡ያነከሰ፡ ከመንገድ፡ እንዳይጠፋ፡ እንዲፈወስ፡ እንጂ።

፲፬፤ በስተ፡ ሰው፡ ሁሉ፡ ሰላምን፡ተከተሉ፡ ቅድስናንም፡ያለርሰዋ፡ማንም፡ እግዚአብሔርን፡የማያይ።
መዝ፡ ፴፬፤ ፲፭። ሮሜ፡ ፲፪፤ ፲፰። ፪፤ ጢሞ፡ ፪፤ ፳፪።

፲፭፤ የተጠበቃችሁ፡ ሁኑ፡ ማንም፡ ከላንት፡ ከእግዚአብሔር፡ጸጋ፡ ጐድሎ፡ እንዳይገኝ፡ *የመረረ፡ ሥርም፡ እንዳይበቅል፡እንዳያስቸግራችሁም፡ ከርሱም፡ የተነሣ፡ ብዙ፡ ሰዎች፡ ይረክሳሉ። *ዘዳግ፡ ፳፱፤ ፲፰።

፲፮፤ ከላንት፡አንድ፡ ሰው፡ *ዝማዊ፡ ወይም፡ዓመፀኛ፡እንዳይሆን፡እንደ፡ †ዔሳው፡ በኵርነቱን፡ ባንዲት፡መብል፡እንደ፡ሸጠ። *ኤፌ፡ ፭፤ ፫። ራእ፡ ፳፩፤ ፰።
†ዘፍጥ፡ ፳፭፤ ፴፫፤ ፴፬።

፲፯፤ ታውቃላችሁና፡ ከዚያ፡ *በኋላ፡ በረከት፡ ይወርስ፡ ዘንድ፡ በወደደ፡ ጊዜ፡ እርሱ፡ እንደ፡ ተጣለ፡ለንስሓም፡ስፍራ፡አላገኘምና፡ ምንም፡በልቅሶ፡ቢሻት።
*ዘፍጥ፡ ፳፯፤ ፴፤ ፴፩።

፲፰፤ ወደሚዳሰስ፡ ተራራ፡ አልደረሳችሁምና፡ ወደሚቃጠልም፡ እሳት። ወደ፡ ጽንግም፡ወደ፡ ጨለማም፡ ወደ፡ ዶውሎ፡ ነፋስም። ዘፀአ፡ ፲፱፤ ፲፪፤ ፲፬።
ዘዳግ፡ ፭፤ ፳፪፤ ፳፫።

፲፱፤ ወደ፡ መለከትም፡ ድምጽ፡ ወደ፡ ነገርም፡ ድምጽ፡ የለዚህ፡ ሰሞች፡ ለመኑ፡ ደግሞ፡እንዳይናገራቸው። ዘፀአ፡ ፳፤ ፲፰፤ ፲፱።

፳፤ በታዘዘው፡አልታገሡምና።እንስሳም፡ደግሞ፡ ወደ፡ ተራራው፡ ብትደርስ፡ ትወገራለች።
ዘፀአ፡ ፲፱፤ ፲፪፤ ፲፫።

፳፩፤ እንዲሁም፡ የተፈራ፡ ነበረ፡ ያስፈራ፡ ሙሴም፡ ደግሞ፡ አለ፡ እኔ፡ ፈራሁ፡ ተንቀጠቀጥሁም።
ዘዳግ፡ ፱፤ ፲፱።

፳፪፤ እላንተ፡ግን፡ወደ፡ጽዮን፡ተራራ፡*ደረሳችሁ። ወደ፡ ሕያውም፡ እግዚአብሔር፡ †አገር፡ የሰማዩቱ፡ የሩሳሌም። **ወደ፡ አእላፋም፡ መላእክት።
*መዝ፡ ፪፤ ፮። ፸፤ ፪። †ራእ፡ ፫፤ ፲፪።
**መዝ፡ ፷፰፤ ፲፯። ዳን፡ ፯፤ ፲። ራእ፡ ፭፤ ፲፩።

፳፫፤ በሰማይ፡ ወደ፡ ተጻፉም፡ወደ፡በኵራት፡ *ማኅበር። ወደ፡ †እግዚአብሔርም፡ ወደ፡ሁሉ፡ ፈራጅ። ወደ፡ ተፈጸሙትም፡ ወደ፡ **ቅዱሳን፡ መንፈስቱ።
*ሉቃ፡ ፲፤ ፳። ራእ፡ ፲፱፤ ፲፩። †ም፡ ፲፩፤ ፲፮።
መዝ፡ ፺፫፤ ፫፤ ፬። **ም፡ ፲፩፤ ፵።

፳፬፤ ባዲስ፡ኪዳን፡ መካከለኛም፡ወደለው፡ወደ፡ የሱስ፡ ወደ፡ መርጨትም፡ ደም፡ ከአቤል፡ ደም፡የሚሻል፡ ወደሚናገር። ም፡ ፱፤ ፲፭። ዘፍጥ፡ ፬፤ ፲።

፳፭፤ አሁንም፡ ተጠንቀቁ፡ ፈቀቅ፡ እንዳትሉ፡ ከሚናገራችሁ። እሊያ፡ሰንኳ፡ *ያላመለጡ፡በምድር፡ ላይ፡ ከተናገራቸው፡ቢርቁ፡ እኛስ፡ እንዴት፡ እናመልጣለን፡ ከሰማይ፡ ከሚናገር፡ ብንርቅ።
*ም፡ ፪፤ ፪። ና፡ ፲፤ ፳፰፤ ፳፱።

፳፮፤ ከርሱ፡ በድምፁ፡ ቀድሞ፡ምድርን፡ ካናወጠው። አሁን፡ ግን፡ *ተስፋ፡ ነገረ፡ አለም። እንደገና፡ ደግሞ፡ እናወጣለሁ፡ ምድሪቱን፡ ብቻ፡ አይደለም፡ ሰማዩንም፡ እንጂ። *ሐጌ፡ ፪፤ ፮።

፳፯፤ እንደገና፡ ደግሞም፡ ማለቱ፡ የምትናወጥ፡ ዓለም፡ እንድታልፍ፡ያመለክታል፡ የተፈጠረች፡ ናትና፡ የማትናወጠው፡ ዓለም፡ ትጸና፡ ዘንድ።
መዝ፡ ፻፪፤ ፳፮።

፳፰፤ ስለዚህም፡*የማታልፈውን፡ መንግሥት፡ ተቀብለናልና፡ እግዚአብሔርን፡ በምናገለግልበት፡ጸጋ፡ እንያዝ፡ ደስም፡ እናሰኘው፡ †በፍርሃት፡ በመንቀጥቀጥም። *ዳን፡ ፪፤ ፵፬። ፯፤ ፲፬። †መዝ፡ ፪፤ ፲፩።
ፊል፡ ፪፤ ፲፪።

፳፱፤ አምላካችን፡ ደግሞ፡ የምታቃጥል፡ *እሳት፡ ነውና። *ዘዳግ፡ ፬፤ ፳፬። ኢሳ፡ ፴፫፤ ፲፬።

## ምዕራፍ፡ ፲፫፤

፩፤ የወንድሞች፡ ፍቅር፡ በላንት፡ ትጽና።
ሮሜ፡ ፲፪፤ ፲። ፪፤ ጴጥ፡ ፩፤ ፯።

፪፡ እንግዶችን፡መውደድ፡አትርሱ።በዚህ፡ሰዎች፡ ተገብተዋቸዋልና፡ መላእክትን፡ ይቀበሉ፡ዘንድ፡ሳያውቁ። ሮሜ፡ ፲፪፡ ፲፫። ዘፍጥ፡ ፲፰፡ ፫። ና፡ ፲፱፡ ፪፡ ፫።

፫፡ የታሠሩትን፡ አስቡ፡ እላንተ፡ ከርሳቸው፡ ጋራ፡ ታሥራችሁ፡ እንደ፡ ነበራችሁ፡ መከራ፡ የጸናባቸውንም፡ እላንተ፡ ደግሞ፡ እንደርሳቸው፡ በሥጋ፡ እንደ፡ ሆናችሁ። ማቴ፡ ፳፭፡ ፴፮።

፬፡ መጋባት፡ በሁሉ፡ የከበረች፡ ትሁን፡ መኝታውም፡ ንጹሕ። አመንዝሮችን፡ ግን፡ ጋለሞቶችንም፡ እግዚአብሔር፡ ይፈርድባቸዋል። ዘፀአ፡ ፳፡ ፲፬። ፩፡ ቆሮ፡ ፮፡ ፱። ኤፌ፡ ፭፡ ፭።

፭፡ አካሔዳችሁ፡ ያለ፡ ስስት፡ ይሁን። ነገር፡ ግን፡ ከላንተ፡ ጋራ፡ ያለው፡ ይብቃችሁ። እርሱ፡ ብሏልና። አልተውህም፡ ቸልም፡ አልልህም። ፩፡ ዮሐ፡ ፩፡ ፭።

፮፡ ስለዚህም፡ እኛ፡ በድፍረት፡ እንላለን፡ እግዚአብሔር፡ ረጂ፡ ነው። አልፈራም፡ ሰው፡ ምን፡ *ያደርግብኛል። *መዝ፡ ፶፮፡ ፬። ና፡ ፻፲፯፡ ፮።

፯፡ *አለቆቻችሁን፡ አስቡ፡ የእግዚአብሔርን፡ ቃል፡ የሚነግሩዋችሁን፡ ያካሔዳቸውንም፡ ፍጻሜ፡ አይታችሁ፡ †ሃይማኖታቸውን፡ ተከተሉ። *ቍ፡ ፲፯። †፩፡ ቆሮ፡ ፬፡ ፲፮።

፰፡ የሱስ፡ ክርስቶስን፡ የትላንትናና፡ የዛሬ፡ ነውና፡ እርሱም፡ ለዘላልም፡ እንደሁ፡ ይኖራል። ፩፡ ቆሮ፡ ፫፡ ፲፩። ራእ፡ ፩፡ ፲፯።

፱፡ ወደ፡ እንግዶቹ፡ ትምህርት፡ ወደ፡ ጠማማዎቹም፡ *አትመለሱ። መልካምም፡ ነውና፡ ልባችሁ፡ †እንደጸና፡ በጸጋ፡ በመብልም፡ አይደለም፡ እሊያ፡ ይሔዱባት፡ የነበሩ፡ **አልተረቡምና። *ኤፌ፡ ፬፡ ፲፬። †ምሳ፡ ፳፩፡ ፪። **ሮሜ፡ ፲፬፡ ፲፯።

፲፡ ለኛ፡ መሠዊያ፡ አለነ፡ ድንኳኑን፡ የሚያገለግሉ፡ ከርሱ፡ ይበሉ፡ ዘንድ፡ የማይገባቸው። ም፡ ፰፡ ፬፡ ፭።

፲፩፡ እንስሳዎቹ፡ *ደምዋ፡ ከካህናቱ፡ አለቃ፡ ስለ፡ ኃጢአት፡ ወደ፡ መቅደስ፡ የሚቀርበው፡ ሥጋዋ፡ †ከከተማ፡ በሜዳ፡ ይቃጠላልና። *ዘሌዋ፡ ፲፮፡ ፳፯። †ዘፀአ፡ ፳፱፡ ፲፬።

፲፪፡ ስለዚህም፡ የሱስ፡ ሕዝቡን፡ በደሙ፡ ሊያነጻ፡ ካገር፡ በሜዳ፡ *ሕማማት፡ ተቀበለ። *ዮሐ፡ ፲፱፡ ፲፯።

፲፫፡ አሁንም፡ እኛ፡ ወደርሱ፡ እንውጣ፡ ከከተማ፡ ወደ፡ ሜዳ፡ *መሰደቡን፡ ተሸክመን። *ም፡ ፲፩፡ ፳፮።

፲፬፡ ከዚህ፡ የምትኖር፡ አገር፡ የለችንምና፡ የምትመጣውን፡ እንሻለን፡ እንጂ። ም፡ ፲፩፡ ፲። ፲፪፡ ፳፪።

፲፭፡ እንግዲህ፡ በርሱ፡ የበረከት፡ *መሥዋዕት፡ ሁለግዜ፡ ለእግዚአብሔር፡ እናሳርግ። ይህች፡ እርስዋ፡ †የከንፈሮች፡ ፍሬ፡ የምትሆን፡ ለስሙ፡ የሚመሰክሩ። *፩፡ ጴጥ፡ ፪፡ ፭። †ሆሴ፡ ፲፬፡ ፫።

፲፮፡ በጎ፡ ማድረግንና፡ መከፈልን፡ አትርሱ። እንደዚህ፡ ያለውን፡ መሥዋዕት፡ እግዚአብሔር፡ ይወደዋልና። ፊል፡ ፬፡ ፲፰።

፲፯፡ *ለአለቆቻችሁ፡ ታዘዙ፡ ተገዙላቸውም፡ ስለ፡ ነፍሳችሁ፡ ይተጋሉና፡ ስለላንት፡ †ምላሽ፡ እንደሚሰጡ፡ ይህነን፡ በደስታ፡ ያደርጉ፡ ዘንድ፡ በኃዘንም፡ አይደለም፡ ይህ፡ ለላንት፡ አይረባምና። *ቍ፡ ፯። †ሕዝ፡ ፫፡ ፲፰። ና፡ ፴፫፡ ፪፡ ፰።

፲፰፡ ስለኛ፡ ጸልዩ። ልባችን፡ አምንዋልና፡ መልካምም፡ አሳብ፡ እንደለነ፡ የቀና፡ አካሔድ፡ በሁሉ፡ እንሔድ፡ ዘንድ፡ ስንሻ። ፪፡ ቆሮ፡ ፩፡ ፲፪።

፲፱፡ ይልቁንም፡ ይህነን፡ ታደርጉ፡ ዘንድ፡ እለምናችኋለሁ፡ ፈጥኜ፡ ወደላንት፡ እመለስ፡ ዘንድ።

፳፡ እግዚአብሔር፡ ግን፡ የሰላም፡ አምላኬ፡ ጌታችነን፡ የሱስን፡ የበጎች፡ *ጠባቂችን፡ አለቃ፡ ከሙታን፡ ያስነሣ፡ በዘላለም፡ ሥርዓት፡ ደም። *ኢሳ፡ ፵፡ ፲፩። ሕዝ፡ ፴፬፡ ፳፮። ዮሐ፡ ፲፡ ፲፩።

፳፩፡ እርሱ፡ በመልካምም፡ ስራ፡ ሁሉ፡ ያጽናችሁ፡ ፈቃዱን፡ ታደርጉ፡ ዘንድ፡ በፊቱም፡ ደስ፡ የሚያሰኘውን፡ ያድርግባችሁ፡ በየሱስ፡ ክርስቶስ፡ ምስጋና፡ ያለው፡ ለዘላለሙ። አሜን።

፳፪፡ እኔም፡ እለምናችኋለሁ፡ ወንድሞቼ፡ ሆይ፡ የተግሣጹን፡ ነገር፡ ትችሉ፡ ዘንድ። ጥቂት፡ ነገር፡ ጽፌላችኋለሁና።

፳፫፡ ወንድማችን፡ ጢሞቴዎስ፡ ከግዞት፡ እንደ፡ ተፈታ፡ እወቁ። እርሱም፡ ፈጥኖ፡ ቢመጣ፡ ከርሱ፡ ጋራ፡ አያችኋለሁ።

፳፬፡ አለቆቻችሁን፡ ሁሉ፡ እንዴት፡ ናችሁ፡ በሉ፡ ቅዱሳንንም፡ ሁሉ። የኢጣልያ፡ ሰዎች፡ እንዴት፡ ናችሁ፡ ይሉዋችኋል።

፳፭፡ ጸጋ፡ ከሁላችሁ፡ ጋራ፡ ይሁን። አሜን።

የዕብራውያን፡ መልእክት፡ በኢጣልያ፡ አገር፡ ተጻፈች፡ በጢሞቴዎስም፡ እጅ፡ ተላከች።

# የሐዋርያ ፡ የያዕቆብ ፡ መልእክት ፡ ከቶሊካዊት ።

## ምዕራፍ፡ ፩፡

፩፡ ያዕቆብ፡ የእግዚአብሔርና፡ የጌታ፡ የየሱስ፡ ክርስቶስ፡ ባርያ፡ ለተበተኑ፡ ላሥራ፡ ሁለቱ፡ ነገድ፡ ደስ፡ ይበላችሁ። ፩፡ ጴጥ፡ ፩፡ ፩።

፪፡ ልዩ፡ ልዩ፡ *ፈተና፡ ሲደረስባችሁ፡ ጊዜ፡ በደስታ፡ ሁሉ፡ ቍጠሩት፡ ወንድሞቼ፡ ሆይ። ሮሜ፡ ፭፡ ፫።

፫፡ አውቃችሁ፡ የሃይማኖታችሁ፡ መፈተን፡ ትዕግሥት፡ እንዲያደርግላችሁ።

፬፡ ለትዕግሥትም፡ ፍጹም፡ ሥራ፡ ይሁንላት፡ ፍጹማን፡ ትሆኑ፡ ዘንድ፡ ምሉአንም፡ ከማናቸውም፡ ሳትጉድሉ።

፭፡ ማንም፡ ከላንት፡ ጥበብ፡ ቢጐድለው፡ ለሁሉ፡ ሳይለይ፡ የሚሰጠውን፡ የማይላገድም፡ እግዚአብሔርን፡ *ይለምን። *ምሳ፡ ፪፡ ፫፡ ፬። ማር፡ ፲፩፡ ፳፬።

፮፡ በሃይማኖቱ፡ ግን፡ ይለምን፡ ሳይጠራጠርም። ተጠራጥሮ፡ የሚለምን፡ ንፋስ፡ የምትመታውን፡ የምትመልሰውም፡ የባሕርን፡ ሞገድ፡ ይመስላልና።

፯፡ ለዚያም፡ ሰው፡ ከእግዚአብሔር፡ ዘንድ፡ አንዳችን፡ የሚወስድ፡ አይምሰለው።

፰፡ ሁለት፡ ልብ፡ ያለው፡ ሰው፡ በመንገዱ፡ ሁሉ፡ የጸና፡ አይደለውም። ም፡ ፬፡ ፰።

፱፡ የተዋረደውም፡ ወንድም፡ በከፍታው፡ ይመካ። ም፡ ፪፡ ፭።

፲፡ ባለጠጋ፡ ግን፡ በትሕትናው። እንደ፡ ሣዕር፡ አበባ፡ ያልፋልና። ፩፡ ጴጥ፡ ፩፡ ፳፬።

፲፩፡ ጸሓይ፡ ትወጣለችና፡ ከትኩሳት፡ ጋራ። ሣዕሩም፡ ይደርቃል፡ አበባውም፡ ይረግፋል፡ የመልኩም፡ ደም፡ ግባት፡ ይጠፋል፡ እንደሁም፡ ይረግፋል፡ ባለጠጋው፡ በመንገዱ። ኢሳ፡ ፵፡ ፮፡ ፯።

፲፪፡ በመከራ፡ የሚታገሥ፡ ሰው፡ *ብፁዕ፡ ነው። ከተፈተነ፡ በኋላ፡ †የሕይወትን፡ አክሊል፡ ይወስዳልና። እግዚአብሔር፡ ለሚወዱት፡ ተስፋ፡ ያስደረገበቱን። *ራእ፡ ፫፡ ፲፱። †፪፡ ጢሞ፡ ፬፡ ፰።

፲፫፡ ማንም፡ በተፈተነ፡ ጊዜ፡ እግዚአብሔር፡ ፈተነኝ፡ አይበል። እግዚአብሔር፡ በክፉ፡ አይፈተንምና፡ ማነንም፡ አይፈትንም። ፩፡ ቆሮ፡ ፲፡ ፲፫።

፲፬፡ ሁሉ፡ ኢያንዳንዱ፡ ይፈተናል፡ እንጂ፡ ከገዛ፡ ምኞቱ፡ ሲሳብና፡ ሲያባበል። ሮሜ፡ ፯፡ ፯፡ ፰።

፲፭፡ መመኘት፡ ግን፡ ባረገዘች፡ ጊዜ፡ ኃጢአትን፡ ትወልዳለች። ኃጢአትም፡ በተፈጸመች፡ ጊዜ፡ *ሞት፡ ትወልዳለች። *ሮሜ፡ ፮፡ ፳፫።

፲፮፡ አትሳቱ፡ ወንድሞቼ፡ ሆይ፡ የተወደዳችሁ።

፲፯፡ በጎ፡ ስጦታ፡ ሁሉ፡ ፍጹምም፡ አሰጣት፡ ሁሉ፡ ከላይ፡ ነው፡ ከብርሃናት፡ አባት፡ ወርዶ። በርሱ፡ ዘንድ፡ ከቶ፡ *መለወጥና፡ የጽላል፡ መመለስ፡ እንኳ፡ የሌለው። *ማል፡ ፫፡ ፮። ፩፡ ዮሐ፡ ፩፡ ፭።

፲፰፡ እርሱ፡ በፈቃዱ፡ በውነት፡ ቃል፡ *ወለደን፡ የቀደማያት፡ አይነት፡ ለፍጥረቶቹ፡ እንሆን፡ ዘንድ። *ዮሐ፡ ፩፡ ፲፫። ፩፡ ጴጥ፡ ፩፡ ፳፫።

፲፱፡ ስለዚህም፡ ወንድሞቼ፡ ሆይ፡ የተወደዳችሁ ከላንት፡ ሰው፡ ሁሉ፡ ለመስማት፡ የፈጠነ፡ ይሁን፡ ለመናገርም፡ የዘገየ፡ ለቍጣም፡ የዘገየ። መክ፡ ፯፡ ፲።

፳፡ የሰው፡ ቍጣ፡ የእግዚአብሔርን፡ ጽድቅ፡ አይሰራምና። ኤፌ፡ ፬፡ ፳፮።

፳፩፡ ስለዚህም፡ ርኩሰትን፡ ሁሉ፡ የክፋትንም፡ መላት፡ *አርቁ። የተተከለውንም፡ ቃል፡ በገርነት፡ ተቀበሉ፡ ችሎት፡ ያለውን፡ ነፍሳችሁን፡ ያድን፡ ዘንድ። *ሮሜ፡ ፲፫፡ ፲፪። ቆላ፡ ፫፡ ፰።

፳፪፡ ቃልንም፡ *አድራጎች፡ ሁኑ፡ ሰሞችም፡ ብቻ፡ አይደለውም፡ ራሳችሁን፡ እንደታሉ። *ማቴ፡ ፯፡ ፳፩። ሮሜ፡ ፪፡ ፲፫።

፳፫፡ ማንም፡ ቃልን፡ *ሰሚ፡ ቢሆን፡ አድራጊም፡ አይደለም፡ ይህ፡ የፍጥረቱን፡ ፊት፡ በማስታወት፡ የሚያየውን፡ ሰው፡ ይመስላልና። *ሉቃ፡ ፮፡ ፵፱።

፳፬፡ ራሱንም፡ ተመለከተና፡ ሔደ፡ የዚያን፡ ጊዜውም፡ የነበረውን፡ ምሳሌ፡ ይረሳል።

፳፭፡ ፍጹም፡ *ሕግን፡ ግን፡ አርነት፡ የምታወጣውን፡ አጥልቆ፡ ያሚመለከት፡ የሚጸናባትም፡ የማይረሳ፡ ሰሚ፡ ስራን፡ አድራጊ፡ እንጂ፡ በማድረጉ፡ †የተመሰገነ፡ ይሆናል። *ም፡ ፪፡ ፲፪። †ዮሐ፡ ፲፫፡ ፲፯።

፳፮፡ በመካከላችሁ፡ ማንም፡ አምልኮኛ፡ ሁኖ፡ ቢመስለው፡ ልሳኑን፡ የማይለጉም። ልቡን፡ ያስታል፡ እንጂ። የርሱ፡ አምልኮ፡ ከንቱ፡ ናት። መዝ፡ ፴፬፡ ፲፬።

፳፯፡ የነጻች፡ በእግዚአብሔር፡ ዘንድም፡ ያላደፈች፡ አምልኮ፡ ይህች፡ ናት። ሰው፡ አባትና፡ እናት፡ የሌላቸውን፡ ባልቴቶችንም፡ በመከራቸው፡ ይጐበኛቸው፡ ዘንድ፡ ራሱንም፡ ከዓለም፡ ርኩሰት፡ ይጠብቅ፡ ዘንድ።

## ምዕራፍ፡ ፪፡

፩፡ ወንድሞቼ፡ ሆይ፡ የጌታችነን፡ የየሱስ፡ ክርስቶስን፡ ሃይማኖት፡ የምስጋና፡ ጌታ፡ በአድልዎ፡ ገጽ፡ አትያዙ።

፪፡ ወደ፡ ጉባዔ፡ ወደ፡ ተከማቻችሁበት፡ አንድ፡ ሰው፡ ቢገባ፡ የወርቅ፡ ቀለበት፡ በፃቱ፡ ያደረገ፡ እርሱም፡ መልካም፡ ልብስ፡ ለብሶ። ደግሞም፡ ድኃ፡ ሰው፡ ቢገባ፡ ባደፈ፡ ልብስ።

፫፤ መልካምም፡ ልብስ፡ ወደ፡ ለበሰው፡ ብታዩ፡ እንደህም፡ ትሉታላችሁ። አንተ፡ ከዚህ፡ በመልካም፡ ስፍራ፡ ተቀመጥ፡ ምስኪኑንም፡ ትሉታላችሁ። አንተ፡ ከዚያ፡ ቁም፡ ወይም፡ ወዲያ፡ ተቀመጥ፡ ከግሬ፡ ድኳ፡ በታች።

፬፤ እንጊደህ፡ ያድልዎ፡ ነገር፡ ማድረጋችሁ፡ አይደለምን። በክፋም፡ ሐሊና፤ አልፈረደችሁምን።

፭፤ ስሙ፡ ወንድሞቼ፡ ሆይ፡ የተወደዳችሁ። እግዚአብሔር፡ የዚህን፡ ዓለም፡ ድኆች፡ *የመረጠ፡ አይደለምን፡ በሃይማኖት፡ ባለጠጎች፡ ለወደጆቹም፡ ተስፋ፡ ያደረገባትን፡መንግሥት፡ወራሾች፡ ይሆኑ፡ዘንድ።
*፩፤ ቆሮ፡ ፩፤ ፳፯።። ዘፀአ፡ ፳፯።።

፮፤ እላንተ፡ግን፡ድኻውን፡አቃለላችሁ።ባለጠጎች፡ የግድ፡ የሚልዋችሁ፡ አይደሉምን፡ እርሳቸውም፡ወደ፡ ፍርድ፡ ሸንጎ፡ ይጐትዋችኋል።

፯፤ በላንትም፡ የተጸራውን፡ የከበረውን፡ ስም፡ የሚሰድቡ፡ አይደሉምን።

፰፤ የንጉሥን፡ሕግ፡ብትፈጽሙ፡*በመጽሐፍ፡ እንደ፡ተጻፈ፡ ባልንጀራህን፡ ወደድ፡ እንደ፡ ነፍስህ፡ መልካም፡ ታደርጋላችሁ።
*ማር፡ ፲፪፤ ፴፩።።
ዘሌዋ፡ ፲፱፤ ፲፰።።

፱፤ ፊት፡አደታችሁ፡ግን፡ብታደሉ፡ኃጢአት፡ ታደርጋላችሁ፡ሕግም፡ ትዘልፋችኋለች፡ እንደ፡ ተላላፎች።
ዘዳግ፡ ፩፤ ፲፯።። ም፡ ፲፮፤ ፲፱።።

፲፤ ሕግን፡ሁሉ፡*የሚጠብቅ፡ባንዲቱም፡ የሚበድል፡ በሁሉ፡ የተላለፈ፡ ሁንዋልና።
*ማቴ፡ ፭፤ ፲፱።።

፲፩፤ አታመንዝር፡ *ያለው፡ ደግሞን፡ አትግደል፡አለ። አሁን፡ ግን፡ ባታመነዝርም፡ ከገደልህ፡ ፈጽመህ፡ ሕግን፡ተላለፍህ።
*ዘፀአ፡ ፳፤ ፲፫፤ ፲፬።።

፲፪፤ እንደህ፡ ተናገሩ፡ እንደህም፡ አድርጉ፡ *በአርነት፡ሕግ፡የምትፈረዱ፡እንደላችሁ።
*ም፡ ፩፤ ፳፭።።

፲፫፤ ምህረት፡ የሌለበት፡*ፍርድ፡ይሆናልና፡ምህረት፡ ለማያደርግ። ምህረትም፡ በፍርድ፡ ላይ፡ ትመካለች።
*ማቴ፡ ፭፤ ፯።። ም፡ ፲፰፤ ፴፤ ፴፩።።
ም፡ ፳፭፤ ፵፭፤ ፵፮።።

፲፬፤ ምን፡ ጥቅም፡ ነው፡ ወንድሞቼ፡ ሆይ፡ አንድ፡ ሰው፡ቢል፡ሃይማኖት፡አለኝ፡*ምግባርም፡ የለውም። ሃይምኖቱ፡ታድነው፡ ትችላለችን።
*ማቴ፡ ፯፤ ፳፮።።

፲፭፤ ወንድም፡ ወይም፡ እት፡ ዕራቁታቸውን፡ ቢሆኑ፡የዕለት፡ራታቸውንም፡ የሚኙ።
ሉቃ፡ ፫፤ ፲፩።።

፲፮፤ እንዲም፡ ከላንት፡ ቢላቸው፡ በደህና፡ ሒዱ፡ ደሙቃችሁ፡ጽገቡም። ሥጋቸው፡ግን፡ የሚሻውን፡አስጥዋቸውም።ምን፡ ይጠቅማል።
፩፤ ዮሐ፡ ፫፤ ፲፯።።

፲፯፤ እንደሁ፡ ሃይማኖትም፡ ምግባር፡ ከሌላት፡ እርስዋ፡ የሞተች፡ናት፡ለብቻዋ፡ ስትሆን።

፲፰፤ ነገር፡ግን፡አንድ፡ ሰው፡ይላል። አንተ፡ ሃይማኖት፡ አለህ፡እኔም፡ ምግባር፡ አለኝ። አንተ፡ ሃይማኖትህን፡ ያለ፡ ምግባር፡ *አሳየኝ፡ እኔም፡ ሃይማኖቴን፡ ከምግባሬ፡አሳይሃለሁ።
*ገላት፡ ፭፤ ፮።።

፲፱፤ አንተ፡ታምናለህ፡እግዚአብሔር፡ አንድ፡እንደሆነ፡ መልካም፡ ታደርጋለህ። ሰይጣናትም፡ ደግሞ፡ ያምናሉ፡ ይንቀጠቀጡማል።

፳፤ ነገር፡ግን፡ ትሻለህን፡ ታውቅ፡ ዘንድ፡አንተ፡ ከንቱ፡ሰው፡ሃይማኖት፡ ምግባር፡ የሌለባት፡ የሞተች፡ እንደሆነች።

፳፩፤ አባታችን፡ አብርሃም፡ በምግባሩ፡ የጸደቀ፡አይደለምን፡ልጁን፡ ይስሐቅን፡ ለመሥዋዕት፡ ባቀረበው፡ጊዜ።
ዘፍጥ፡ ፳፪፤ ፱፤ ፲፤ ፲፪።።

፳፪፤ ተመልከት፡ሃይማኖት፡ ከምግባሩ፡ ጋራ፡ እንደደረገች ። ከምግባርም፡ የተነሣ፡ ሃይማኖት፡ ተፈጸመች።

፳፫፤ መጽሐፍም፡*ያለው፡ተፈጸመ። አብርሃም፡ በእግዚአብሔር፡ አመነ፡ ጽድቅም፡ ሆኖ፡ ተቈጠረለት፡ የእግዚአብሔርም፡ †ወደጅ፡ተባለ።
*ዘፍጥ፡ ፲፭፤ ፮።። †ኢሳ፡ ፵፩፤ ፰።።

፳፬፤ አሁንስ፡ አያችሁ፡ ሰው፡ በምግባሩ፡ እንዲጸድቅ፡ በሃይማኖትም፡ ብቻ፡ አይደለውም።

፳፭፤ እንደሁም፡ *ረዓብ፡ ጋለሞታ፡ በምግባርዋ፡ የጸደቀች፡ አይደለችምን፡ ጕበኞችን፡ በተቀበለች፡ ጊዜ፡ በሌላ፡ መንገድም፡ ባወጣቻቸው፡ ጊዜ።
*ዕብ፡ ፲፩፤ ፴፩።።

፳፮፤ ነፍስ፡ የሌለችበት፡ ሥጋ፡ የሞተ፡ እንደ፡ ሆነ፡ እንደሁም፡ *ሃይማኖት፡ ያለ፡ ምግባር፡ የሞተች፡ ናትና።
*ቍ፡ ፲፯።።

## ምዕራፍ፡ ፫፤

፩፤ እጅግ፡መምህራን፡አትሁኑ፡ ወንድሞቼ፡ ሆይ፡ ታላቅ፡ ፍርድ፡እንድንወስድ፡ ታውቃላችሁና።

፪፤ እኛ፡ ሁላችን፡ ብዙ፡ ጊዜ፡ እንበድላለንና። በነገሩ፡ የማይስት፡ይህ፡ ፍጹም፡ ሰው፡ ነው፡እርሱም፡ሥጋውን፡ ሁሉ፡ ይገዛ፡ ዘንድ፡ ይችላል።

፫፤ እነሆ፡*ልጓም፡እናደርጋለን፡ በፈረስ፡ አፍ፡ ትታዘዝልን፡ ዘንድ፡ ሥጋዋንም፡ ሁሉ፡ እንስበዋለን።
*መዝ፡ ፴፪፤ ፱።።

፬፤ ደግሞም፡ እነሆ፡ ታላላቆች፡ መርከቦች፡ ከጸናች፡ዓውሎ፡ነፋስ፡ተነድተው፡ በታናሽ፡እንጨት፡ይመለሳሉ፡ የመርከብ፡ መሪ፡ፈቃድ፡ ወደሚወደው፡ ስፍራ፡ሁሉ።

፭፤ እንደሁም፡ መላስ፡ታናሽ፡ብልት፡ነው፡ታላላቅም፡ ነገር፡ ይናገራል። እነሆ፡ እሳት፡ ጥቂት፡ ብትሆን፡ ምንድር፡ የሚያህልንስ፡ ታቃጥላለች።

፮፤ መላስም፡ እሳት፡ ነው፡ የዓለም፡ ግፍ፡ ሁሉ፡ የመላበት። እንደሁ፡መላስ፡በብልታችን፡ተሰርትዋል፡ ሥጋንም፡ ሁሉ፡ *ያረክሳል፡ የፍጥረታችንንም፡ ሩጫ፡ ያቃጥላል፡ ከገሃነም፡ ትነደለች።
*ማቴ፡ ፲፭፤ ፲፩—፲፱።። ም፡ ፲፪፤ ፴፯፤ ፴፮።።

፯፤ የእንስሳ፡ባሕርይ፡ሁሉ፡ የአራዊትም፡ የአዕዋፍም፡ የሚንቀሳቀሰውም፡ በባሕርም፡ ያሉ፡ እንሰሶች፡ይለመደሉ፡ በሰው፡ ባሕርይም፡ ተለምደዋል።

፰፥ መላስን፡ግን፡ከሰው፡ ማንም፡ አይችልም፡ ደገ
ዛው፡ ዘንድ። ክፉ፡ ዓመፀኛም፡ ነውና፡ *የሞት፡ መር
ዝ፡የመላበት።                     *መዝ፡ ፻፵፥ ፫።
፱፥ በርሱ፡እግዚአብሔር፡ አብን፡ እናመሰግናለን።
በርሱም፡ ሰውን፡ እንረግማለን፡ በእግዚአብሔር፡ አ
ምሳል፡ የተፈጠረውን።               ዘፍ፡ ፩፥ ፳፮።
፲፥ ካንድ፡ አፍ፡ ይወጣል፡ በረከትና፡ መርገምዋ።
አይገባም፡ወንድሞቼ፡ሆይ፡ ይህ፡ነገር፡ እንደዚህ፡ ይሆ
ን፡ ዘንድ።
፲፩፥ ወይስ፡ ካንድ፡ ምንጭ፡ የጨው፡ ውኃና፡ ጣፋ
ጭ፡ውኃ፡ ይፈሳልን።
፲፪፥ ወይስ፡ወንድሞቼ፡ ሆይ፡ በለስ፡ወይራ፡ታፈራ
ለችን። ወይንም፡ በለስን። እንደዚሁም፡ አንድ፡ ምን
ጭ፡ መራራ፡ ውኃ፡ የጣፈጠም፡ አያፈስም።
፲፫፥ ማነው፡ከላንት፡ *ጠቢብ፡አስተዋይም። ከመ
ልካም፡አካሔዱ፡ተሥራውን፡ ይገለጥ፡ በጥበብ፡ የው
ሃት።           *ኤፌ፡ ፭፥ ፲፭። ተም፡ ፪፥ ፲፰።
፲፬፥ *ቅንዓት፡ ግን፡ ቢኖርባችሁ፡ መተማማትም፡
በልባችሁ፡ አትመኩ፡ በውነትም፡ ላይ፡ አትዋሹ።
                              *ኤፌ፡ ፬፥ ፴፩።
፲፭፥ ይህች፡ ጥበብ፡ *ከላይ፡ የወረደች፡ አይደለች
ም፡ነገር፡ግን፡ የምድር፡ናት፡ የሥጋም፡ ናት፡ የሰይጣን
ም፡ናት።                      *ም፡ ፩፥ ፭፥ ፲፫።
፲፮፥ ቅንዓትና፡መተማማት፡ባለበት፡ ስፍራ፡ ከዚ
ያ፡ አንድነት፡ የለምና፡ ክፉም፡ ሥራ፡ ሁሉ፡ አለበት።
፲፯፥ ከሰማይ፡ ግን፡ የወረደች፡ ጥበብ፡ ታራቂ፡ አስ
ቀድሞ፡ ንጹሕ፡ ነው፡ ደግሞም፡ የዕርቅ፡ ወዳጅ፡ ገር
ም፡ እሺ፡ባይም፡ ምሕረትና፡ መልካም፡ ፍሬ፡ የመላ
ባት፡ ያለ፡ ማድላትና፡ ያለ፡ ግብዝነት።
፲፰፥ የጽድቅ፡ *ፍሬ፡ግን፡ በሰላም፡ ትዘራለች፡ ሰላ
ም፡ ለሚያደርጉ።                 *ኢሳ፡ ፴፪፥ ፲፯።

## ምዕራፍ፡ ፬፥

፩፥ ጽል፡ ክርክርም፡ ከወዴት፡ መጣችባችሁ። ከዚ
ህ፡ አይደለችምን፡ በብልታችሁ፡ ከምትታወክ፡ ፍት
ወታችሁ።                      ፩፥ ጴጥ፡ ፪፥ ፲፩።
፪፥ ትመኛላችሁ፡ለላንትም፡ አይሆንም። ትገድላ
ላችሁ፡ ትቀኑማላችሁ፡ መውሰድም፡ አይሆንላችሁ
ም። ትጣላላችሁ፡ ትዋጉማላችሁ። ምንም፡ የላችሁ
ም፡ ስላለመናችሁ።
፫፥ *ትለምናላችሁ፡ አትቀበሉም፡ ለመልካም፡ አ
ትለምኑምና፡ በፍትወታችሁ፡ ልትፈጁት፡ ነው፡ አ
ንጂ።                          *መዝ፡ ፲፰፥ ፵፪።
፬፥ እላንት፡ አመንዝሮች፡ አመንዝራዪቶችም፡ አ
ታውቁምን፡ የዓለም፡ፍቅር፡ በእግዚአብሔር፡ ላይ፡
ጸላትነት፡ እንደ፡ ሆነች። የዓለም፡ ወዳጅ፡ መሆን፡ የ
ሚወድ፡ የእግዚአብሔር፡ ጸላት፡ ሁና፡ ተገኘ።
     ሉቃ፡ ፮፥ ፳፮። ሮሜ፡ ፰፥ ፯። ፩፥ ዮሐ፡ ፪፥ ፲፭።
፭፥ ወይስ፡ ይመስላችኋልን፡ *መጽሐፍ፡ በከንቱ፡
የሚናገር። በኛ፡ ያደረብነ፡ መንፈስ፡ በቅንዓት፡ ይወ
ዳል።                          *ገላት፡ ፭፥ ፲፯።
፮፥ ነገር፡ግን፡ ጸጋውን፡ አብልጦ፡ ይሰጣል። ስለዚህ
ም፡ ይላል ። *እግዚአብሔር፡ ልባቸውን፡ የሚያስታ
ብዩን፡ ሰዎች፡ ይቃወማል፡ ለትሑታን፡ ግን፡ ጸጋ፡ ይሰ
ጣል።            *ኢዮብ፡ ፳፪፥ ፳፱። ማቴ፡ ፳፫፥ ፲፪።
፯፥ አሁንም፡ለእግዚአብሔር፡ ተገዙ። ሰይጣንን፡
*ትቋቋሙ፡ ከላንትም፡ ይሸሻል።      *ኤፌ፡ ፮፥ ፲፪።
፰፥ ወደ፡ እግዚአብሔር፡ *ቅረቡ፡ እርሱም፡ ወደላ
ንት፡ይቀርባል። እጃችሁን፡ ተአንጹ፡እላንት፡ ኃጢአተ
ኞች፡ልባችሁንም፡ አጽሩ፡ በሁለት፡ ልብ፡ የምትሆኑ።
                    *ዘካ፡ ፩፥ ፫። ተኢሳ፡ ፩፥ ፲፮።
፱፥ ተቸገሩ፡ አልቅሱም፡ እዘኑም። ሳቃችሁ፡ ወደ፡
ልቅሶ፡ ይመለስ፡ ደስታችሁም፡ ወደ፡ ኃዘን።
፲፥ በእግዚአብሔር፡ ፊት፡ *ዝቅ፡ ዝቅ፡ በሉ፡ ከፍ፡
ከፍም፡ ያደርጋችኋል።              *፩፥ ጴጥ፡ ፭፥ ፮።
፲፩፥ እርሱ፡በርሳችሁ፡ *አትናገሩ፡ እላንት፡ ወንድ
ሞች። በወንድሙ፡ ላይ፡ የሚናገር፡ በወንድሙም፡
የሚፈርድ፡ ፈጽሞ፡ በሕግ፡ ላይ፡ይናገራል፡ በሕግም፡
ይፈርዳል። በሕግም፡ ከፈረድህ፡ አንተ፡ ሐግን፡ አድ
ራጊ፡አይደለህም፡ ፈራጅ፡ እንጂ።    *መዝ፡ ፲፭፥ ፫።
                              ፩፥ ጴጥ፡ ፪፥ ፩።
፲፪፥ አንድ፡ነውና፡ የሕግ፡ አጋጊና፡ ፈራጅ፡ ያድን፡ ዘ
ንድ፡ይገልም፡ዘንድ፡ ችሎት፡ ያለው። *አንተ፡ ማነህ፡
በባልንጀራህ፡ትፈርድ፡ዘንድ።          *ማቴ፡ ፯፥ ፩።
፲፫፥ አሁንም፡ ሒዱ፡ እንዲህ፡ *የሚሉትን፡ ሰዎ
ች። ዛሬ፡ ወይም፡ነገ፡ ወደዚያች፡ አገር፡ እንሔዳለን፡
ከዚያም፡ አመት፡ እናደርጋለን፡ እነነግድማለን፡ እና
ተርፍማለን።                     *ምሳ፡ ፳፯፥ ፩።
፲፬፥ እላንትም፡ *አታውቁም፡ ነገ፡ የሚሆነውን።
ሕይወታችን፡ምንድር፡ናትና። እንደ፡ ጽጋግ፡ አይደለ
ችምን፡ ጥቂት፡ ታይቶ፡ የሚጠፋ።      *ሉቃ፡ ፲፪፥ ፳።
፲፭፥ በምትሉበት፡ ፈንታ። እግዚአብሔር፡ ቢፈቅ
ደውሖብንኖርም፡ ይህነን፡ ወይም፡ ያነን፡እናደርጋለን።
                              የሐዋ፡ ፲፰፥ ፳፩።
፲፮፥ ነገር፡ ግን፡ ዛሬ፡ በማስባችሁ፡ ትመካላችሁ።
እንደዚህ፡ ያለው፡ መመካት፡ ሁሉ፡ ክፉ፡ ነው።
፲፯፥ *መልካም፡ ነገርም፡ ማድረግ፡ የሚያውቅ፡ የ
ማያደርገውም፡ ያም፡ ኃጢአት፡ ይሆንበታል።
                              *ሉቃ፡ ፲፪፥ ፵፯።

## ምዕራፍ፡ ፭፥

፩፥ አሁንም፡ ሒዱ፡ እላንት፡ *ባለጠጎች፡ አልቅሱ፡
ዋይም፡ በሉ፡ በሚመጣባችሁ፡ መከራ።
                    *ምሳ፡ ፲፩፥ ፳፰። ሉቃ፡ ፮፥ ፳፬።
፪፥ *ባለጠግነታችሁ፡ ጠፍትዋልና፡ልብሳችሁንም፡
ብል፡ በልቶታልና።                 *ማቴ፡ ፮፥ ፲፱።
፫፥ ወርቃችሁ፡ብራችሁም፡ ዛገ፡ዝገቱም፡ምስክር፡
ይሆንባችኋል፡ ሥጋችሁንም፡ ይበላዋል፡ እንደሳት።
ለኋለኛው፡ ቀን፡ መዝገብ፡ አከማቻችሁት።

፬፡ እነሆ፡ የሠራተኞች፡ ምድራችሁን፡ ያጨዱት፡ ዋጋ፡ እላንት፡ የቀማችኋቸው፡ ይጮኻል። ያጨዶች ም፡ድምጽ፡ወደ፡ ፀባዖት፡ ወደ፡ እግዚአብሔር፡ጆሮ፡ ደረሰ። ዘዳግ፡ ፳፬፡ ፲፬፡ ፲፭፡፡

፭፡ በምድር፡ ላይ፡ ደኅላችሁ፡ በቤሰኝነት፡ ተቀመ ጣችሁ።ልባችሁን፡አደነደናችሁ፡በበዓል፡ ቀን፡እንደ፡ ሆነ። ሉቃ፡ ፲፮፡ ፲፱፡ ፳፭፡፡

፮፡ በጻድቁም፡ ፈረዳችሁ፡ ገደላችሁትም፡ አልተ ጠናወታችሁምም።

፯፡ አሁንም፡ ወንድሞቼ፡ ሆይ፡ *ታገሡ፡እስከ፡ጌ ታ፡መገለጥ፡ድረስ። እነሆ፡ ገባሬ፡ የከበረችቱን፡ ምድ ር፡ፍሬ፡ደጅ፡ ይጸናል፡ ሲታገሥላት፡ የፊተኛውንና፡የ ኋለኛውን፡ ዝናም፡ እስክትወስድ፡ ድረስ።

*ሉቃ፡ ፳፩፡ ፲፱፡፡ ዕብ፡ ፲፡ ፴፮፡፡

፰፡ እላንትም፡ደግሞ፡ታገሡ፡ ልባችሁን፡ አጽኑ፡ የ ጌታ፡መምጣት፡ ቀርብዋልና።

፱፡ እርሱ፡ በርሳችሁ፡ አትተዛዘኑ፡ ወንድሞቼ፡ሆ ይ፡ እንዳትኰነኑ። እነሆ፡ *ፈራጅ፡ በደጅ፡ ፊት፡ ቁም ዋልና። *ማቴ፡ ፳፬፡ ፴፫፡፡

፲፡ ነቢያትን፡ በጌታ፡ ስም፡ የተናገሩትን፡ ወንድሞ ቼ፡ ሆይ፡ የመከራንና፡ የትዕግሥትን፡ ምሳሌ፡ ተቀበ ሉ። እነሆ፡ የታገሡትን፡ እናመሰግናለን።

ማቴ፡ ፭፡ ፲፪፡፡

፲፩፡ የኢዮብን፡*ትዕግሥት፡ሰምታችኋል፡የእግዚ አብሔርንም፡ ፍጻሜ፡አያችሁ፡ †እግዚአብሔር፡ ም ህረቱ፡ የበዛ፡ ነውና፡ የሚራራም።

*ኢዮብ፡ ፩፡ ፳፩፡ ፳፪፡፡ †መዝ፡ ፻፫፡ ፰፡፡

፲፪፡ ከሁሉ፡ ይልቅ፡ ግን፡ ወንድሞቼ፡ ሆይ፡ አትማ ሉ። በሰማይ፡ በምድርም፡ በሌላም፡ መሐላ። በነገራ ችሁ፡ ግን፡ አዎን፡ አዎን፡ ይሁን፡ አይደለም፡ አይደለ ም፡ከፍርድ፡ በታች፡ እንዳትወድቁ።

ማቴ፡ ፭፡ ፴፬፡—፴፯፡፡

፲፫፡ ማንም፡ከላንት፡ *በመከራ፡ ቢሆን፡ ይጸልይ። ደስ፡ ቢለውም፡ †ይዘምር። *መዝ፡ ፶፡ ፲፭፡፡

†ቆላ፡ ፫፡ ፲፮፡፡

፲፬፡ ማንም፡ከላንት፡ ቢታመም፡ የቤተ፡ ክርስቲያ ኖን፡ቀሳውስት፡ይጥራ፡ ይጸልዩለትም፡ *ዘይትም፡ይ ቀቡት፡በጌታ፡ስም። *ማር፡ ፮፡ ፲፫፡፡

፲፭፡ የሃይማኖትም፡ *ጸሎት፡ ድውዩን፡ ትፈውሳ ለች፡ ጌታም፡ ያስነሣዋል። ኃጢአትም፡ ሰርቶ፡ እንደ ሆነ፡ትሰረይለታለች። *መዝ፡ ፴፡ ፫፡፡

፲፮፡ እርሱ፡ በርሳችሁ፡ ተናዘዙ፡ በኃጢአታችሁ፡ አ ንዱ፡ም፡ ላንዱ፡ ይጸልይለት፡ *እንድትፈወሱ። የጻድ ቅ፡ ጸሎት፡ ታላቅ፡ ኃይል፡ ታደርጋለች።

*መዝ፡ ፻፵፭፡ ፲፰፡፡

፲፯፡ ኤልያስ፡ ሰው፡ ነበረ፡ እንደኛ፡በአኰል፡ ሕማ ማት፡ጸሎትም፡ጸለየ፡ ከሰማይ፡ ዝናም፡ እንዳይዘን ም። በምድር፡ ላይም፡ *አልዘነመም፡ ሦስት፡ አመት፡ ከስድስት፡ወር። *፩፡ ነገሥ፡ ፲፯፡ ፩፡፡ ሉቃ፡ ፬፡ ፳፭፡፡

፲፰፡ ደግሞም፡ ጸለየ፡ ሰማዩም፡ ዝናም፡ ሰጠች፡ ምድሪቱም፡ፍሬዋን፡አበቀለች። ፩፡ ነገሥ፡ ፲፰፡ ፵፪፡፡

፲፱፡ ወንድሞቼ፡ ሆይ፡ ከላንት፡ ማንም፡ ከውነት፡ መንገድ፡ቢስት፡የሚመልሰውም፡ቢኖር።

ገላት፡ ፮፡ ፩፡፡

፳፡ ያወቅ፡ ኃጢአተኛን፡ ከስሕተት፡ መንገድ፡ የ ሚመልስ፡ነፍስን፡ከሞት፡ የሚያድን፡ እንደሆነ፡ የኃ ጢአትንም፡ ብዛት፡ ይሰውራል።

# የሐዋርያ ፡ የጴጥሮስ ፡ መልእክት ፡ ከቶሊካዊት ፡ መጀመርያይቱ።

ምዕራፍ፡ ፩፡

፩፡ ከጴጥሮስ፡ከየሱስ፡ክርስቶስ፡ ሐዋርያ፡ ወደ፡ተ በተኑት፡ ስደተኞች፡ በጳንጦስ፡ አገር፡ በገላትያም፡ በ ቀጰደቅያም፡በእስያም፡ በቢቲንያም፡ የተቀመጡ።

ያዕ፡ ፩፡ ፩፡፡

፪፡ ቀደመው፡ *የተመረጡት፡ እንደ፡ እግዚአብ ሔር፡አብ፡እውቀት፡በመንፈስ፡ቅድስና፡ለመታዘዝ፡ ለየሱስ፡ክርስቶስም፡ለደሙ፡ መርጨት። ጸጋ፡ ምህረ ትም፡ ትብዛላችሁ። *ሮሜ፡ ፰፡ ፳፱፡፡

፫፡ እግዚአብሔር፡*ይመስገን፡የጌታችንም፡ የየሱ ስ፡ክርስቶስ፡ አባት፡ በምህረቱ፡ብዛት፡ ደግሞ፡ የወለ ደን፡ወደ፡ ሕይወት፡ ተስፋ፡ በየሱስ፡ ክርስቶስ፡ ትንሣ ኤ፡ ከሙታን። ፪፡ ቆሮ፡ ፩፡ ፫፡፡

፬፡ ወደማያረጅ፡ ወደማይጠፋም፡ *ወደማይለ ወጥም፡ርስት፡ በሰማይ፡ የተጠበቀላችሁን።

*ቆላ፡ ፩፡ ፲፪፡፡

፭፡ እላንት፡በእግዚአብሔር፡ኃይል፡ *የተጠበቃች ሁ፡በሃይማኖት፡ ለመድኃኒት፡ በኋለኛው፡ ዘመን፡ ይ ገለጥ፡ዘንድ፡ለተዘጋጀው። *ዮሐ፡ ፲፡ ፳፰፡፡ ፲፯፡ ፲፩፡፡

፮፡ ዛሬ፡ በርሱ፡*ደስ፡ የሚላችሁ፡ ጥቂትም፡ ልባች ሁ፡ቢያዝን፡በተላለፈ፡ መከራ፡ †ስትፈተኑ፡ ለላንት፡ የሚገባ፡ቢሆን። *ሮሜ፡ ፭፡ ፪፡፡ ፪፡ ቆሮ፡ ፬፡ ፲፯፡፡

†ም፡ ፭፡ ፲፡፡

፯፡ የሃይማኖታችሁ፡መፈተን፡ *ከሚጠፋ፡ወርቅ፡ የሚከብር፡ ምንስ፡ በእሳት፡ ቢጸራ፡ ደገኝ፡ ዘንድ፡ ለ ትምክሕት፡ ለምስጋናም፡ ለክብርም፡በየሱስ፡ ክርስ ቶስ፡ መገለጥ። *ም፡ ፲፯፡ ፫፡፡ መልክ፡ ፫፡ ፫፡፡

፰፤ *ያላያችሁት፡ የምትወዱትም፡ ዛሬም፡ አታዩ
ትም፡ ነገር፡ ግን፡ አመናችሁበት፡ በብዙም፡ ደስታ፡ ደ
ስ፡አላችሁ፡ በማይነገርበት፡ደስታ፡ክብር፡የመላበት።
*ዮሐ፡ ፳፡ ፳፱፡፡ ፩፡ ቆሮ፡ ፭፡ ፯፡፡
፱፤ የሃይማኖታችሁን፡ *ፍጻሜ፡ ስትወስዱ፡የነፍሳ
ችሁን፡ ደህንነት። *ሮሜ፡ ፮፡ ፳፪፡፡
፲፤ ስለዚህም፡መድኃኒት፡*ነቢያት፡ፈለጉ፡መረመ
ሩም፡ በዚች፡ ለላንት፡ በሆነችው፡ ጸጋ፡ ትንቢት፡ የተ
ናገሩ። *ደን፡ ፱፡ ፳፫፡ ፳፬፡፡ ሉቃ፡ ፲፡ ፳፬፡፡
፲፩፤ ቢመረምሩ፡ ምን፡ ወይም፡ ማናቸው፡ዘመን፡
የነበረባቸው፡ የክርስቶስ፡ መንፈስ፡ እንደ፡ አመለከ
ተ፡ ስለ፡ ክርስቶስ፡ *ሕማማት፡ ከዚያ፡ በኋላም፡ ስ
ለሚመጣው፡ ክብሩ፡ ቀድሞ፡ በመሰከረ፡ ጊዜ።
*መዝ፡ ፳፪፡ ፯፡፡ ኢሳ፡ ፶፫፡፡
፲፪፤ ይህም፡ ተገለጠላቸው፡ ለራሳቸው፡ ሊያገለግ
ሉ፡ አይደለም፡ ለኛ፡እንጂ፡ያ፡ነገር፡ዛሬ፡ለላንት፡ የተ
ወራ፡ ወንጌልን፡ ከሰበኩላችሁ፡ሰዎች፡በመንፈስ፡ ቅ
ዱስ፡ ከሰማይ፡ በተላከው። ይህም፡ ነገር፡ *መላእክ
ት፡ የሚወዱ፡ ያዩት፡ ዘንድ። *ኤፌ፡ ፫፡ ፲፡፡
፲፫፤ ስለዚህም፡ የልባችሁን፡ ወገብ፡ *አጽኑ፡ ንቁ
ም፡ ፈጽማችሁም፡ በየሱስ፡ ክርስቶስ፡መገለጥ፡የም
ትሰጣችሁን፡ ጸጋ፡ ተስፋ፡ አድርጉ። *ኤፌ፡ ፫፡ ፲፡፡
፲፬፤ እንደሚያዘዙ፡ ልጆች፡ በቀደመችውም፡ *ፍ
ትወት፡ ያለውቀት፡ ባደረጋችኋት፡ አትምሰሉ።
*ሮሜ፡ ፲፪፡ ፪፡፡
፲፭፤ ነገር፡ ግን፡ እንደ፡ ጸራችሁ፡ እንደ፡ቅዱሱ፡ እላ
ንት፡ ደግሞ፡ *ቅዱሳን፡ ሁኑ፡ በአካሔዳችሁ፡ ሁሉ።
*ሉቃ፡ ፩፡ ፸፭፡፡
፲፮፤ *ተጽፎዋልና። ቅዱሳን፡ ሁኑ፡ ፣እኔ፡ ቅዱስ፡
ነኝና። *ዘሌዋ፡ ፲፩፡ ፵፬፡፡ †መዝ፡ ፸፩፡ ፳፪፡፡
፲፯፤ ያለ፡ *አድልዎም፡ የሚፈርደውን፡ ለሁሉም፡
እያንዳንዱ፡ እንደ፡ ስራው፡ የሚሰጠውን፡ አባት፡
የምትሉት፡ ብትሆኑ፡ ከዚህ፡ እንግድነት፡በተቀመጣ
ችሁበት፡ ዘመን፡ ሁሉ፡ በፍርሃት፡ ሒዱ።
*የሐዋ፡ ፲፯፡ ፴፩፡፡
፲፰፤ ታውቃላችሁና፡በሚጠፋ፡ *በወርቅና፡ በብር፡
ከከንቱ፡ ስራችሁ፡ *እንደልደናችሁ፡ ካባቶቻችሁ፡ ከ
ተቀበላችሁት። *፩፡ ቆሮ፡ ፮፡ ፳፡፡ ና፡ ፯፡ ፳፫፡፡
†ቲቶ፡ ፪፡ ፫፡፡
፲፱፤ ነገር፡ ግን፡ በከበረው፡ በበግ፡ ደም፡ ነውር፡ ርኩ
ሰትም፡ የሌለበት፡ እርሱም፡ክርስቶስ።
፳፤ ከጥንቱም፡ *የተመረጠ፡ ዓለም፡ ሳይፈጠር፡
በኋለኛው፡ ዘመን፡ ግን፡ ተገለጠ፡ ስለላንት።
*ሮሜ፡ ፲፮፡ ፳፭፡፡
፳፩፤ በርሱም፡ በእግዚአብሔር፡ *አመናችሁ፡ ከ
ሙታን፡ ተነስነሣው፡ ክብርም፡ በሰጠው፡ ሃይማኖታ
ችሁና፡ ተስፋችሁ፡ በእግዚአብሔር፡ ይሆን፡ ዘንድ።
*ዮሐ፡ ፲፬፡ ፮፡፡ †የሐዋ፡ ፫፡ ፲፭፡፡
፳፪፤ ነፍሳችሁንም፡ ካነጻችሁ፡ ለውነት፡ በመታዘ
ዛችሁ፡ ወደ፡ ወንድሞች፡ ፍቅርም፡ ያለ፡ ሽንገላ፡ ከ
መጣችሁ። እርሱ፡ በርሳችሁ፡ ተዋደዱ፡ በንጹሕ፡ ል
ብ፡ በፍጹምም፡ ውድ።
፳፫፤ ከሚጠፋ፡ ዘር፡ አልተወለዳችሁምና፡ ነገር፡
ግን፡ከማይጠፋ፡ ከዘላለሙ፡ ከሕያው፡ከእግዚአብ
ሔር፡ ቃል፡ የተነሣ። ዮሐ፡ ፩፡ ፲፫፡፡ ያዕ፡ ፩፡ ፲፰፡፡
፳፬፤ ስው፡ ሁሉ፡ እንደ፡ ሣዕር፡ ነውና። የሰውም፡
ክብር፡ ሁሉ፡ እንደ፡ ሣዕር፡ አበባ። ሣዕሩ፡ ይደርቃል፡
አበባውም፡ ይረግፋል። ኢሳ፡ ፵፡ ፮፡ ፯፡፡
ያዕ፡ ፩፡ ፲፡ ፲፩፡፡
፳፭፤ የእግዚአብሔር፡ቃል፡ግን፡ ለዘላለም፡ ይኖራ
ል። በወንጌልም፡ የተሰበከላችሁ፡ ቃል፡ ይህ፡ነው።

## ምዕራፍ፡ ፪፤

፩፤ አሁንም፡ ክፉ፡ ነገርን፡ ሁሉ፡ *ጣሉ፡ ተንኰልን
ም፡ ሁሉ፡ ግብዝነትንም፡ ቅናትንም፡ ሐሜትንም፡
ሁሉ። *ሮሜ፡ ፮፡ ፬፡፡ ና፡ ፲፪፡ ፱፡፡ ፩፡ ቆሮ፡ ፲፬፡ ፳፡፡
፪፤ ዛሬም፡ እንደ፡ ተወለዱ፡ *ሕፃናት፡ አእምሮ፡
ወደለውና፡ ወደውነተኛው፡የቃልን፡ወተት፡ ተናፍቁ፡
በርሱ፡ ታድጉ፡ ዘንድ። *ዕብ፡ ፭፡ ፲፪፡ ፲፫፡፡
†ማቴ፡ ፲፰፡ ፫፡፡
፫፤ ቀምሳችሁ፡ እንደ፡ ሆናችሁ፡ ጌታ፡ ምህረተኛ፡
እንደሆነ። መዝ፡ ፴፬፡ ፱፡፡
፬፤ የቀረባችሁት፡ የሕይወት፡ ደንጊያ፡ በሰውም፡
ዘንድ፡ የተናቀ፡ ነው፡ ግን፡ በእግዚአብሔር፡ ዘንድ፡
የተመረጠና፡ የከበረ፡ ነው። መዝ፡ ፻፲፰፡ ፳፪፡፡
፭፤ እላንትም፡ ደግሞ፡ የሕይወት፡ ደንጎች፡ ሆናች
ሁ፡ ትሠሩ፡ ዘንድ፡ መንፈሳውያን፡ *መቅደስ፡ ሁናች
ሁ፡ የተቀደሳችሁ፡ †ካህናት፡ መንፈሳዊት፡ **መሥ
ዋዕት፡ ታቀርቡ፡ ዘንድ፡ በእግዚአብሔር፡ ዘንድ፡ የተ
ቀበለች፡ በየሱስ፡ ክርስቶስ። *ኤፌ፡ ፪፡ ፳፩፡፡
†ቀ፡ ፱፡፡ **ሮሜ፡ ፲፪፡ ፩፡፡
፮፤ በመጽሐፍ፡ *ተጽፎዋልና። እነሆ፡ በፅዮን፡ የ
ማዝን፡ ራስ፡ የተመረጠ፡ ደንጊያ፡ የከበረም፡ አኖራ
ለሁ፡ የሚያምንበትም፡ አያፍርም።
*ኢሳ፡ ፳፰፡ ፲፮፡፡
፯፤ ይህቺም፡ክብር፡ ለላንት፡ ናት፡ እላንት፡ ያመና
ችሁበት፡ ለማያምኑበት፡ ግን፡ አናጾች፡ የናቁት፡ ደን
ጊያ፡ እርሱ፡ የማዝን፡ ራስ፡ ሆነ። *ማቴ፡ ፳፩፡ ፵፪፡፡
፰፤ *የንቅፋትም፡ ደንጊያ፡ የመሰናከልም፡ ይሆን
ባቸዋል፡ በቃል፡ ለሚሰናከሉ፡ ስላልታዘዙ። እርሳቸ
ውም፡ለዚህ፡ተሰጡ። *ኢሳ፡ ፰፡ ፲፬፡፡ ሮሜ፡ ፱፡ ፴፫፡፡
፱፤ እላንት፡ ግን፡ የተመረጠ፡ *የመንግሥትና፡ የክ
ህነትም፡ ወገን፡ ናችሁ። የተቀደሰች፡ ዘር። ለርስት፡
የተለየ፡ ሕዝብ። ከጨለማ፡ ወደማይነገር፡ወደ፡ ብር
ሃኑ፡ የጸራችሁን፡ ስራ፡ ትገልጡ፡ ዘንድ።
*ዘፀአ፡ ፲፱፡ ፮፡፡ ራእ፡ ፩፡ ፮፡፡
፲፤ እላንት፡ *ከጥንቱ፡ ወገን፡ ያልነበራችሁ፡ አሁን፡
ግን፡ ፈጽማችሁ፡ ወገን፡ ሆናችሁ፡ ለእግዚአብሔር።

ይቅር፡ የተባላችሁም፡ አልነበራችሁም፡ ዛሬ፡ ግን፡ ይቅር፡ ተባላችሁ። *ሆሴ፡ ፪፡ ፳፫፡፡ ሮሜ፡ ፱፡ ፳፭፡፡

፲፩፡ ወዳጆቼ፡ ሆይ፡ *እንደ፡ እንግዶች፡ እንደ፡ መንገድም፡ አላፊዎች፡ እለምናችኋለሁ፡ ነፍስን፡ ከምትዋጋ፡ ከሥጋዊት፡ መመኘት፡ **ትርቁ፡ ዘንድ።
*መዝ፡ ፴፱፡ ፲፫፡፡ †ምሳ፡ ፩፡ ፴፪፡፡ **ሮሜ፡ ፲፫፡ ፲፫፡፡

፲፪፡ አካሔዳችሁም፡በአሕዛብ፡መካከል፡አሳምሩ፡በክፉ፡የሚናገሩባችሁ፡*መልካሙን፡ሥራችሁን፡ ባዩ፡ ጊዜ፡ በጥያቄ፡ ቀን፡ እግዚአብሔርን፡ያመሰግኑ፡ ዘንድ። *ማቴ፡ ፭፡ ፲፮፡፡

፲፫፡ አሁንም፡ ለሰው፡ሥርዓት፡ ሁሉ፡ *ተገዙ፡ስለ፡ እግዚአብሔር፡ለንጉሥም፡ ቢሆን፡ በሁሉ፡ ላይ፡ ሁኖዋልና። *ሮሜ፡ ፲፫፡ ፩፡ ፭፡፡ ቲቶ፡ ፫፡ ፩፡፡

፲፬፡ ለመኳንንትም፡ ቢሆን፡ ከርሱ፡ ተልከዋልና፡ በክፉ፡ አድራጊዎች፡ ላይ፡ መቅሠፍትን፡ ሊያመጡ፡ በበጎ፡ አድራጊዎች፡ ግን፡ ምስጋና።

፲፭፡ ይህች፡ የእግዚአብሔር፡ ፈቃድ፡ ናትና፡ በጎ፡ *በማድረግ፡ የሰነፎችን፡ ያለማወቅ፡ ዝም፡ ታሰኙ፡ ዘንድ። *ም፡ ፫፡ ፲፮፡፡

፲፮፡ የሰው፡ *ልጆች፡ ሁናችሁ፡ የሰው፡ ልጅነታችሁም፡ ለክፋት፡ መሸፈኛ፡ አትሁን፡ እንደ፡ እግዚአብሔር፡ ባሮች፡ እንጂ። *ገላ፡ ፭፡ ፲፫፡፡

፲፯፡ ሁሉን፡ *አክብሩ። ወንድሞችን፡ ውደዱ። እግዚአብሔርን፡ ፍሩ፡ †ንጉሥን፡ አክብሩ።
*ሮሜ፡ ፲፪፡ ፲፡፡ †ማቴ፡ ፳፪፡ ፳፩፡፡

፲፰፡ *ባሮች፡ ለጌቶቻቸው፡ ይገዙ፡በፍርሃት፡ሁሉ። ለመልካሞች፡ ብቻ፡ ለየዋሃንም፡ አይደለም፡ ለጠማሞችም፡ እንጂ። *ኤፌ፡ ፮፡ ፭፡፡ ቲቶ፡ ፪፡ ፱፡፡

፲፱፡ ይህች፡ ጸጋ፡ናትና፡ ማንም፡ ስለ፡ እግዚአብሔር፡ አዘንን፡ ቢታገሥ፡ ግፍ፡ ባገኘው፡ ጊዜ።

፳፡ ምን፡ ትምክሕት፡ አላችሁን፡ ኃጢአትን፡ ሰርታችሁ፡ መከራ፡ ብትቀበሉና፡ ብትታገሡ። ነገር፡ ግን፡ *መልካም፡ አድርጋችሁ፡ መከራ፡ ብትቀበሉ፡ ብትታገሡም፡ ይህ፡ ጸጋ፡ ነው፡ በእግዚአብሔር፡ ዘንድ።
*ም፡ ፫፡ ፲፬፡ ፲፯፡፡ ፬፡ ፲፬፡፡ ማቴ፡ ፭፡ ፲፡፡

፳፩፡ ለዚህ፡ ተጸርታችኋልና። ክርስቶስ፡ ደግሞ፡ ስለኛ፡ሕማም፡ ተቀብሎዋልና፡ለኛ፡ *ምሳሌን፡ትቶ፡ ፍለጋውን፡ ትከተሉ፡ ዘንድ። *ማቴ፡ ፲፮፡ ፳፬፡፡

፳፪፡ ኃጢአት፡ ያልሰራ፡ አሰትም፡ ባፉ፡ ያልተገኘበት። ኢሳ፡ ፶፫፡ ፱፡፡ ዮሐ፡ ፰፡ ፵፮፡፡ ፪፡ ቆሮ፡ ፭፡ ፳፩፡፡

፳፫፡ ሲሰድቡትም፡ አልተሳደበም። መከራም፡ ሲያመጡበት፡ አልተቃየመም። እውነተኛውን፡ ፍርድ፡ ለሚፈርደው፡ እንጂ፡ ነፍሱን፡ ሰጠ።
ኢሳ፡ ፶፫፡ ፯፡፡

፳፬፡ እርሱ፡ *ኃጢአታችነን፡ በሥጋው፡ በንጨት፡ ላይ። ከኃጢአት፡*ወጥተን፡ለጽድቅ፡እንኖር፡ዘንድ። በቊስሉ፡ የተፈወሳችሁ። *፩፡ ዮሐ፡ ፫፡ ፭፡፡
†ሮሜ፡ ፮፡ ፲፩፡፡

፳፭፡ እንደ፡ *ጠፉ፡ በጎች፡ ነበራችሁና፡ ነገር፡ ግን፡ አሁን፡ ወደ፡ ነፍሳችሁ፡ †እረኛና፡ ጠባቂ፡ ተመለሳችሁ። *ኢሳ፡ ፶፫፡ ፮፡፡ ሕዝ፡ ፴፬፡ ፭፡፡ †ዮሐ፡ ፲፡ ፲፪፡፡
ም፡ ፭፡ ፬፡፡

## ምዕራፍ፡ ፫፡

፩፡ እንደሁም፡ እላንት፡ ሴቶች፡ ለባሎቻችሁ፡ ተገዙ። ከርሳቸው፡ ሰዎች፡ ቢኖሩ፡ ለነገር፡ የማይገዙ፡ ይረቡ፡ ዘንድ፡ ያለ፡ ነገር፡ በሴቶቻቸው፡ አካሔድ።
ኤፌ፡ ፭፡ ፳፪፡፡

፪፡ የነጻቸውን፡ አካሔዳችሁን፡ ባዩ፡ ጊዜ፡ በፍርሃት።

፫፡ አሊያ፡ ጌጻቸው፡ከአፍአ፡ ያደደለ፡ የራስ፡ ጽጕር፡ በመሰራት፡በወርቅም፡ ዝርግፍ፡በጌጽም፡ ልብስ።
ኢሳ፡ ፫፡ ፲፰፡፡ ፩፡ ጢሞ፡ ፪፡ ፱፡፡

፬፡ ነገር፡ ግን፡ በማጠፋ፡ በተሰወረች፡ በልብ፡ ሰውነት፡ በየዋህም፡ ነፍስ፡ ጸጥ፡ ባለ፡ በእግዚአብሔር፡ ፊት፡ ገናንነቱ፡ የከበረ።

፭፡ ቀድሞ፡ እንደህ፡ነፍሳቸውን፡ ያስጌጹ፡ነበሩና፡ የተቀደሱት፡ በእግዚአብሔር፡ የታመኑ፤ ሴቶች፡ ለባሎቻቸውም፡ የተገዙ።

፮፡ ለአብርሃም፡ እንደ፡ ተገዛች፡ እንደ፡ሳራ፡ ጌታዬም፡ ትለው፡ ነበረች። እላንት፡ ልጆችዋ፡ የሆናችሁ፡ መልካም፡ ስታደርጉ፡ ከፍርሃትም፡ ሁሉ፡ አንዳች፡ ሳትፈሩ።

፯፡ እላንትም፡ ወንዶች፡ እንደሁ፡ በውቀት፡ ተቀመጡ፡ ከርሳቸው፡ ጋራ፡ አውቃችሁም፡ የሴቶች፡ ፍጥረት፡ ደካማ፡ እንደሆነ፡ አክብሮዋቸው። ከላንትም፡ ጋራ፡ የሕይወት፡ ጸጋ፡ ይወርሳሉና፡ በነገሩ፡ ሁሉ፡ ጸሎታችሁን፡ እንዳትቈርጡ። ኤፌ፡ ፭፡ ፳፭፡፡

፰፡ የዚህም፡ ፍጻሜ፡ ያንድ፡ ልብ፡ ትሆኑ፡ ዘንድ፡ ነው፡ ከሚያዝንም፡ ጋራ፡ የምታዝኑ። እንደ፡ ወንድሞችም፡ የምትወዱ። መሐሮችም። የተዋረዳችሁም።

፱፡ በክፉም፡ክፉ፡አትመልሱ፡በስድብም፡ስድብ። ይህነን፡ ትታችሁ፡ ባርኩ፡ እንጂ። ለዚህ፡ እንደ፡ ተጸራችሁ፡ አውቃችኋልና፡ በረከትን፡ ትወርሱ፡ ዘንድ።
፩፡ ተሰ፡ ፭፡ ፲፭፡፡

፲፡ *ተጽፎዋልና። ሕይወትን፡ይወድ፡ዘንድ፡ መልካምንም፡ ዘመን፡ያይ፡ ዘንድ፡ የሚሻ፡ †መላሱን፡ ከክፉ፡ ይከልክል፡ ከንፈሮቹንም፡ሸንግላውን፡ እንዳይናገሩ። *መዝ፡ ፴፬፡ ፲፫፡፡ †ያዕ፡ ፩፡ ፳፮፡፡

፲፩፡ ከክፉ፡ ይራቅ፡ መልካምም፡ ያድርግ። ሰላምን፡ ይሻ፡ ይከተላትም።

፲፪፡ የእግዚአብሔር፡ ዓይኖች፡ በጻድቃን፡ ላይ፡ ናቸው፡ ጆሮቹም፡ ልመናቸውን፡ ይሰማሉ። የእግዚአብሔር፡ ፊት፡ ግን፡ ክፉ፡ በሚያደርጉ፡ ላይ፡ ነው።

፲፫፡ ማነው፡ የሚጐዳችሁ፡ የመልካም፡ ተከታዮች፡ ብትሆኑ። መዝ፡ ፴፬፡ ፲፮፡ ፲፭፡፡

፲፬፡ ነገር፡ ግን፡ ስለ፡ *ጽድቅ፡ መከራ፡ ብትቀበሉ፡ ደግሞ፡ ብፁዓን፡ናችሁ። ከፍርሃታቸውም፡አትፍሩ፡ አትደንግጡም። *ም፡ ፪፡ ፲፡—፲፩።

፲፭፡ ነገር፡ ግን፡ ጌታን፡ እግዚአብሔርን፡ በልባችሁ፡ ቀድሱት። በጊዜውም፡ ሁሉ፡ የተዘጋጃችሁ፡ ሁኑ፡ ለሚጠይቋችሁ፡ ሁሉ፡ስላላችሁ፡ ተስፋ፡ ለመመለስ፡ በየውሃት፡ በፍርሃትም።

፲፮፡ በመልካም፡ ሕሊና፡ያፍሩ፡ዘንድ፡እንደ፡ክፉ፡ ሰዎች፡የሚናገሩባችሁ። መልካሙንም፡ አኩሔዳችሁን፡ በክርስቶስ፡ የሚያነውሩ።

፲፯፡ መልካም፡ስታደርጉ፡ መከራ፡ ትቀበሉ፡ዘንድ፡ እግዚአብሔር፡ ቢወደው። ክፉ፡ ስታደርጉ፡ መከራን፡ ከመቀበል፡ ይሻላልና። ቀ፡ ፲፬።

፲፰፡ ክርስቶስ፡ ደግሞ፡ አንድ፡ጊዜ፡ ስለ፡ ኃጢአት፡ አሞቷልና፡ ጻድቁ፡ ስለ፡ ዓመፀኞች። እኛን፡ ወደ፡ እግዚአብሔር፡ ያቀርበን፡ ዘንድ። በሥጋም፡ ሞተ፡ በመንፈስ፡ ግን፡ ሕያው፡ ሆነ። ም፡ ፪፡ ፳፩።

፲፱፡ በርሱም፡ *በግዞት፡ ወደሉ፡ ነፍሶች፡ ሒዶ፡ሰበከላቸው። *ም፡ ፬፡ ፯።

፳፡ ቀድሞ፡ እምቢ፡ ብለው፡ ለነበሩ፡ የእግዚአብሔር፡ ምሀረት፡ ረጅም፡ ዘመን፡በዘገየች፡ጊዜ፡ በኖህ፡ ዘመን፡ እርሱ፡ መርከብን፡ ሲሰራ። ጥቂቶች፡ እርሳቸውም፡ስምንት፡ሰዎች፡ በውኃ፡አልፈው፡ የዳኑባት። ዘፍ፡ ፯፡ ፲፯።

፳፩፡ ለርሱም፡ ዛሬ፡ ምሳሌ፡ ያለች፡ እርስዋም፡ *ጥምቀት፡ ታድነናለች። (ከሥጋ፡ እድፋን፡ ማፀብ፡አይደለም፡ የበጎ፡ ሕሊና፡ ልመና፡ ወደ፡እግዚአብሔር፡ እንጂ)። በየሱስ፡ክርስቶስ፡ትንሣኤ። *ኤፌ፡ ፭፡ ፳፯።

፳፪፡ እርሱ፡በእግዚአብሔር፡*ቀኝ፡ያለ፡ወደ፡ሰማይ፡ ወጥቶ፡መላእክትም፡ ሥልጣናትም፡ ኃይላትም፡ ይገዙለታል። *ኤፌ፡፩፡፳፡፳፩።

ምዕራፍ፡ ፬፡

፩፡ እንግዲህ፡ክርስቶስ፡በሥጋው፡ ሕማም፡ስለኛ፡ ከተቀበለ፡ እንደሁ፡እላንተ፡ ደግሞ፡ ይህነን፡ፈቃድ፡ እንደ፡ እቃ፡ ጦር፡ ልበሱ። በሥጋው፡መከራ፡ የተቀበለ፡ ከኃጢአት፡ ወጥትዋልና።

፪፡ በሰው፡ መመኘት፡ ደግሞ፡ እንዳይኖር፡ በሥጋ፡ በሚቀርበት፡ ዘመን፡ ሁሉ፡ የእግዚአብሔርን፡ ፈቃድ፡ እንዲያደርግ፡ እንጂ።

፫፡ ያለፈው፡ ዘመን፡ *ይበቃናልና፡ የአሕዛብን፡ ፈቃድ፡ ያደረግነበት፡ በሴሰኝነት፡ ሒደን፡ በመመኘትም፡ በስካርም፡ በመብልም፡ በዘፈንም፡ በርኩሰትም፡ በሚያስጸይፍም፡ በጣዖት፡ አምልኮት። *ኤፌ፡ ፪፡ ፪፡ ፫። ቲቶ፡ ፫፡ ፫።

፬፡ አሁንም፡ ለርሳቸው፡ ልዩ፡ ሆናችሁበት፡ ይህንነት፡ በሌለባት፡ገበተኛነቱም፡ ስራቸው፡ ስላልተከተላችኋቸው፡ ይሰድባችሁማል።

፭፡ እርሳቸውም፡ምላሽ፡ይሰጣሉ፡ በሕያዋንና፡ በሙታን፡ይፈርድ፡ዘንድ፡ላለው።፪፡ጢሞ፡፬፡፩፡—፰።

፮፡ ስለዚህም፡ *ለሙታን፡ ደግሞ፡ በወንጌል፡ ተሰበከ፡ እንደ፡ ሰው፡ በሥጋ፡ እንዲፈረድባቸው፡ በመንፈስ፡ ግን፡ ለእግዚአብሔር፡ ሕያዋን፡ እንዲሆኑ። *ም፡ ፫፡ ፲፱።

፯፡ የነገር፡ሁሉ፡ መጨረሻ፡ቀርብዋል። ስለዚህም፡ አስተውሉ፡ ለጸሎትም፡ ትጉ። ፩፡ ቆር፡ ፲፡ ፲፩። ፩፡ ዮሐ፡ ፪፡ ፲፰።

፰፡ ከሁሉም፡ በፊት፡ እርሱ፡ በርሳችሁ፡ የምትቃጠል፡ ፍቅር፡ ትኑርላችሁ። *ፍቅር፡ የኃጢአትን፡ ብዛት፡ ትሰውራለችና። *ምሳ፡ ፲፡ ፲፪። ያዕ፡ ፭፡ ፳።

፱፡ እንግዶችን፡ የምትወዱ፡ ሁኑ፡ እርሱ፡ በርሳችሁ፡ ያለ፡ ማንጐራጐር። ዕብ፡ ፲፫፡ ፪፡—፯።

፲፡ ሁሉም፡ ኢያንዳንዱ፡ በተቀበለው፡ ጸጋ፡ መጠን፡ ባልንጀራውን፡ያገልግለው። እንደ፡ እግዚአብሔር፡ እንደ፡ ልዩ፡ ልዩ፡ ጸጋው፡ ደህና፡ መጋቦች።

፲፩፡ የሚናገር፡ ቢሆን፡ እንደ፡ እግዚአብሔር፡ቃል፡ ይናገር። የሚያገለግል፡ እግዚአብሔር፡ኃይል፡እንደ፡ ሰጠው፡ ያገልግል፡ እግዚአብሔር፡ በሁሉ፡ ይመሰገን፡ ዘንድ፡ በየሱስ፡ ክርስቶስ ምስጋና፡ ያለው፡ ችሎትም፡ ለዘላለም። አሜን። ሮሜ፡ ፲፪፡ ፮።

፲፪፡ ወዳጆቼ፡ ሆይ፡ የምትመጣባችሁን፡ መከራ፡ እንደ፡ እሳት፡ የምትሆንን፡ አታድንቁ፡ እንደ፡ልዩ፡ ስራ። ም፡ ፩፡ ፯፡ ፮።

፲፫፡ ነገር፡ግን፡በክርስቶስ፡ሕማም፡አንድ፡በመሆናችሁ፡ደስ፡ ይበላችሁ። ክብሩ፡ በተገለጠ፡ጊዜ፡ እጅግ፡ ደስ፡ ይላችሁ፡ ዘንድ፡ደግሞ። የሐዋ፡ ፭፡ ፵፩። ሮሜ፡ ፰፡ ፲፯። ያዕ፡ ፩፡ ፪።

፲፬፡ ስለ፡ክርስቶስ፡ስምም፡ ቢላገድዋችሁ፡ ብፁዓን፡ ናችሁ። ክብር፡ ያለበት፡ የእግዚአብሔር፡ መንፈስ፡ ያርፍባችኋልና፡ ከርሳቸው፡ ይሰደባል፡ በላንት፡ዘንድ፡ ግን፡ ይከብራል። ም፡ ፪፡ ፳።

፲፭፡ ነገር፡ ግን፡ ማንም፡ ከላንት፡ መከራ፡ የሚቀበል፡አይሁን፡እንደ፡ነፍሰ፡ገዳይ፡ እንደ፡ ሌባም፡ እንደ፡ ክፉ፡ ሰሪም፡ እንደ፡ ለገመኛም።

፲፮፡ ክርስቲያን፡ ግን፡ ስለ፡ ሆነ፡ቢሆን፡ አይፈር። በዚህ፡ ስም፡ መክንያት፡ እግዚአብሔርን፡ *ያመስግን፡እንጂ። *ፊል፡ ፩፡ ፳፱።

፲፯፡ ፍርድ፡ የሚጀመርበት፡ ጊዜ፡ አለና፡ በእግዚአብሔር፡ ቤት። በኛም፡ የተጀመረብነ፡ ከሆነ፡ የእግዚአብሔርን፡ ወንጌል፡ የሚክዱ፡ ፍጻሜ፡ ምን፡ ይሆናል። ኤር፡ ፳፭፡ ፳፱። ሕዝ፡ ፱፡ ፮።

፲፰፡ ጻድቅም፡የግድ፡የሚድን፡ ከሆነ፡ ኃጢአተኛ፡ ዓመፀኛስ፡ በወዴት፡ ይገለጥ፡ ዘንድ፡ አለው። ምሳ፡ ፲፩፡ ፴፩። ሉቃ፡ ፳፫፡ ፴፩።

፲፱፡ ስለዚህም፡መከራ፡የሚቀበሉ፡ እንደ፡እግዚአብሔር፡ ፈቃድ፡ ነፍሳቸውን፡ ለእግዚአብሔር፡ አደራ፡ ይስጡ፡ ለታመነ፡ ፈጣሪ፡ መልካም፡ በማድረግ። መዝ፡ ፴፩፡ ፮።

ምዕራፍ፡ ፭፡

፩፥ በላንት፡ ዘንድ፡ ያሉትን፡ ሽማግሌዎች፡ እለምናቸዋለሁ፡ እኔ፡ *ሽማግሌ፡ እንደርሳቸው፡ የክርስቶስም፡ ሕማም፡ የምመሰክር፡ እንድነትም፡ ያለኝ፡ የሚገለጠውም፡ †ክብር። *፪፡ ዮሐ፡ ፩፡፡ †ሮሜ፡ ፰፡ ፲፯፡፡

፪፥ በላንት፡ዘንድ፡ያለውን፡የእግዚአብሔርን፡መንጋ፡ ትጠብቁና፡ ትጐበኙዋቸውም፡ ዘንድ፡ በግድ፡ አይደለም፡ በልብ፡ፈቃድ፡እንጂ። ረብ፡ ለማግኘት፡ አይደለም፡ በርኅራኄ፡ እንጂ። ዮሐ፡ ፳፩፡ ፲፯፡፡ የሐዋ፡ ፳፡ ፳፰፡፡ ፩፡ ጢሞ፡ ፫፡ ፪፡፡

፫፥ እንደ፡ ጌቶችም፡ *በእግዚአብሔር፡ ርስት፡ ላይ፡ አይደለም፡ ለመንጎች፡ †ምሳሌ፡ እንደሚሆኑ፡ እንጂ። *፪፡ ቆሮ፡ ፩፡ ፳፬፡፡ †ቲቶ፡ ፪፡ ፯፡፡

፬፥ የጠባቆችም፡ *አለቃ፡ በተገለጠ፡ ጊዜ፡ የማይጠፋውን፡ †የክብርን፡ አክሊል፡ ትወስዳላችሁ። *ዕብ፡ ፲፫፡ ፳፡፡ †፩፡ ቆሮ፡ ፱፡ ፳፭፡፡ ፪፡ ጢሞ፡ ፬፡ ፰፡፡

፭፥ እንደሁም፡ እላንት፡ ጐበዛዝት፡ ለሽማግሌዎች፡ ተገዙ። *ሁላችሁም፡ እርስ፡ በርሳችሁ፡ ተገዙ። ትሕትናውንም፡ ልበሱ። †እግዚአብሔር፡ ልባቸውን፡ የሚያስታብዩን፡ ይጣላልና፡ ለትሑታን፡ግን፡ ጸጋውን፡ ይሰጣል። *ኤፌ፡ ፭፡ ፳፩፡፡ †ማቴ፡ ፳፫፡ ፲፪፡፡ ያዕ፡ ፬፡ ፮፡፡

፮፥ እንግዲህ፡ ዝቅ፡በሉ፡ ከጸናችው፡ ከእግዚአብሔር፡ እጅ፡ በታች፡ በጊዜው፡ ከፍ፡ ከፍ፡ ያደርጋችሁ፡ ዘንድ። ኢዮብ፡ ፳፪፡ ፳፱፡፡ ያዕ፡ ፬፡ ፲፡፡

፯፥ ትካዛችሁንም፡ ሁሉ፡ በርሱ፡ ጣሉት፡ እርሱ፡ ያስብላችኋልና። ማቴ፡ ፮፡ ፳፭፡፡ ፊል፡ ፬፡ ፮፡፡

፰፥ አቅማችሁን፡ ጠብቁ፡ ትጉም፡ ሰይጣን፡ ጸላታችሁ፡ እንደሚጮህ፡ አንበሳ፡ ይዞራልና፡ የሚውጠውን፡ ሰው፡ ሽቶ። ሉቃ፡ ፳፩፡ ፴፮፡፡ ፩፡ ተሰ፡ ፭፡ ፮፡፡

፱፥ እርሱን ፡ በሃይማኖት ፡ ጸንታችሁ ፡ ተቃወሙት። እንደህም፡ ያለ፡ መከራ፡ በዓለም፡ ባሉ፡ በወንድሞቻችሁ፡ እንዲፈጸም፡ እወቁ። ኤፌ፡ ፮፡ ፲፩፡፡

፲፥ የጸጋም፡ ሁሉ፡ አምላክ፡ እኛን፡ ወደ፡ ዘላለም፡ ክብሩ፡ በክርስቶስ፡ የሱስ፡ የጸራን፡ ጥቂት፡ መከራ፡ ከተቀበላችሁ፡ በኋላ፡ እርሱ፡ ያበጃችኋል፡ ያጸናችኋልም፡ ያበርታችኋልም ፡ ይመሠርታችኋልም። ም፡ ፩፡ ፮፡፡

፲፩፥ ለርሱ፡ ክብር፡ ችሎትም፡ ይሁን፡ ለዘላለም። አሜን።

፲፪፥ በስልዋኖስ፡ እጅ፡ በታመነ፡ ወንድም፡ እኔ፡ እንደ፡ ቈጠርሁት፡ ጥቂት፡ ነገር፡ ጻፍሁላችሁ፡ ላጸናችሁ፡ ልመሰክርላችሁም፡ ይህ፡ የእግዚአብሔር፡ እውነተኛ፡ ጸጋ፡ እንደ፡ ሆነ፡ እላንት፡ የቆማችሁበት። ዕብ፡ ፲፫፡ ፳፪፡፡

፲፫፥ እንደኔ፡ የተመረጠች፡ ትላችኋለች፡ ከላንት፡ ጋራ፡ የተመረጸችው፡ ቤተ፡ክርስቲያን፡ በባቢሎን፡ ያለችው፡ *ማርቆስም፡ ልጄ። የሐዋ፡ ፲፪፡ ፲፪፡ ፳፭፡፡ ፪፡ ጢሞ፡ ፬፡ ፲፩፡፡

፲፬፥ እርስ፡ በርሳችሁ፡ *ተሳለሙ፡ በፍቅር፡ ሰላም። ለላንት፡ ሰላም፡ ይድረስላችሁ፡ ለሁላችሁ፡ በክርስቶስ፡ የሱስ፡ ላላችሁ። አሜን። *፩፡ ቆሮ፡ ፲፮፡ ፳፡፡

# የሐዋርያ ፡ የጴጥሮስ ፡ መልእክት ፡ ከቶሊካዊት ፡ ሁለተኛይቱ።

ምዕራፍ፡ ፩፡

፩፥ ከስምዖን፡ ጴጥሮስ፡ ከየሱስ፡ ክርስቶስ፡ ባርያ፡ ከሐዋርያም፡ ተካክሎ፡ የከበረውን፡ ሃይማኖት፡ ከኛ፡ ጋራ፡ ወደ፡ ተቀበሉት፡ ባምላካችን፡ ጽድቅ፡ በመድኃኒታችንም፡ በየሱስ፡ ክርስቶስ።

፪፥ ጸጋ፡ ደህንነትም፡ ይብዛላችሁ፡ በእግዚአብሔር፡ እውቀት፡ በጌታችንም፡ በየሱስ፡ ክርስቶስ።

፫፥ ያምላክነቱ፡ ኃይል፡ ለሕይወትና፡ ለመልካም፡ አምልኮ፡ የምንሻውን፡ ነገር፡ ሁሉ፡ ከሰጠን፡ እርሱን፡ በማወቅ፡ በክብሩና፡ በበጐነቱ፡ *የጸራን። *፩፡ ጴጥ፡ ፪፡ ፱፡፡

፬፥ በዚህም፡ እጅግ፡ ታላቅ፡ ተስፋ፡ የከበረም፡ ተሰጠን፡ የእግዚአብሔርን፡ባሕርይ፡ ተካፋዮች፡ ትሆኑ፡ ዘንድ፡ ከሽታችሁ፡ በዓለም፡ ካለው፡ ጥፋት፡ በሥጋ፡ ፍትወት።

፭፥ ስለዚህም፡ ጥረትን፡ ሁሉ፡ አቅርባችሁ፡ *በሃይማኖታችሁ፡ በጐነትን፡ ጨምሩ። ፀበጐነትም፡ እውቀትን። ገላ፡ ፭፡ ፮፡ ፳፪፡፡

፮፥ በውቀትም፡ መሻትን፡ መግዛት። በመሻትንም፡ መግዛት፡ ትዕግሥትን። በትዕግሥትም፡ አምልኮን።

፯፥ በአምልኮም፡ ወንድሞችን፡ መውደድን። ወንድሞችንም፡ በመውደድ፡ ፍቅርን። ገላ፡ ፮፡ ፲፡፡

፰፥ ይህ፡ በላንት፡ ቢሆን፡ ቢበዛም፡ ታካቾችና፡ ያለፍሬ፡ አያደርጋችሁም፡ ጌታችን፡ የሱስ፡ ክርስቶስን፡ በማወቅ።

፱፥ ይህም፡ እንደሁ፡ የሌለበት፡ እርሱ፡ ዕውር፡ ነው፡ ጭፍንም፡ የቀደመውንም፡ ኃጢአቱን፡ ማንጻት፡ የረሳ። ፩፡ ዮሐ፡ ፪፡ ፱፡ ፲፩፡፡

፲፥ ስለዚህም፡ እላንት፡ ወንድሞች፡ አብዝታችሁ፡ ተጠበቁ፡ መጸራታችሁ፡ መመረጻችሁም፡ ትጸና፡ ዘንድ። ይህነን፡ ብታደርጉት፡ ከቶ፡ አትሰናከሉም።

፲፩፥ እንደሁም፡ በባለጠግነት፡ መግቢያው፡ ይሰጣችኋል፡ ወደ፡ ጌታችንና፡ ወደ፡ መድኃኒታችን፡ ወደ፡ የሱስ፡ ክርስቶስ፡ ወደ፡ ዘላለሙ፡ መንግሥት።

፲፪፡ *ስለዚህም፡እኔ፡ቸል፡አልልም፡ ሁልጊዜ፡ ሊያሳስባችኋለሁ፡ ስለዚህች፡ ሁሉ፡ ምንስ፡ ብታውቋት፡ ደግሞ፡በሆነውም፡ እውነት፡ የጸናችሁ፡ ብትሆኑ።
*ሮሜ፡ ፲፭፡ ፲፬፡ ፲፭።

፲፫፡ እኔም፡ የሚገባኝ፡ ይመስለኛል፡ በዚህ፡ ማደሪያ፡ ባለሁበት፡ ዘመን፡ በማሳሰብ፡ ላስነሣችሁ።
፪፡ ቆሮ፡ ፭፡ ፩።

፲፬፡ አውቃለሁና፡ ከዚህ፡ማደሪያ፡መለየቴ፡ *ፈጥኖ፡እንዲሆን። ጌታችን፡ የሱስ፡ ክርስቶስ፡ ደግሞ፡ እንደ፡ገለጠልኝ።
*ዮሐ፡ ፳፩፡ ፲፰፡ ፲፱።

፲፭፡ እኔም፡ እጣጣራለሁ፡ ይህቸን፡ነገር፡ሁልጊዜ፡ የምታስቡ፡ ትሆኑ፡ ዘንድ፡ ከመውጣቴ፡ በኋላ።

፲፮፡ *ያስተን፡ጥበብ፡ነገር፡ተከትለንን። የጌታችን፡ የየሱስ፡ ክርስቶስን፡ ኃይልና፡ መገለጥ፡ †አላስታወቅናችሁምና፡ የርሱን፡ታላቅነት፡ አይተን፡ እንጂ።
*፩፡ ቆሮ፡ ፩፡ ፲፯። †፩፡ ቆሮ፡ ፪፡ ፬።

፲፯፡ ክብርና፡ምስጋና፡ ከእግዚአብሔር፡ አብ፡ ወሰደዋልና፡ድምጽም፡እንደሁ፡ መጣለት፡ ከገነነው፡ ክብር፡ እንደህ፡ ሲል። *ይህ፡ ነው፡ልጄ፡ የተወደደው፡ ደስ፡የምልበት።
ማቴ፡ ፫፡ ፲፯። ፕ፡ ፲፯፡ ፭።
ሉቃ፡ ፱፡ ፴፭። ኤፌ፡ ፩፡ ፮።

፲፰፡ ይህነንም፡ድምጽ፡እኛ፡ሰማነው፡ከሰማይ፡የመጣለት፡እኛ፡ ከርሱ፡ጋራ፡ሳለን፡ በተቀደሰ፡ ተራራ።
ማቴ፡ ፲፯፡ ፩።

፲፱፡ ከኛ፡ጋራም፡እጅግ፡ የሚጸና፡ የትንቢት፡ ነገር፡ አለን፡ በጎም፡ ታደርጋላችሁ፡ ብትመለከቱት፡ እንደ፡ *መብራት፡ በጨለማ፡ ስፍራ፡ የሚያበራ፡ እስኪጸባ፡ድረስ፡ የንጋትም፡ ኮከብ፡ በልባችሁ፡ እስኪወጣ፡ ድረስ።
*መዝ፡ ፻፲፱፡ ፻፭። ፪፡ ቆሮ፡ ፬፡ ፮።

፳፡ ይህነንም፡ አስቀድማችሁ፡ እወቁ፡ *የመጽሐፍ፡ትንቢት፡ሁሉ፡ትርጓሜዋ፡ ከራስዋ፡ እንዳይደለ።
*ሮሜ፡ ፲፪፡ ፮። ፪፡ ጢሞ፡ ፫፡ ፲፮።

፳፩፡ ትንቢት፡ከቶ፡ በሰው፡ ፈቃድ፡ አልመጣችምና፡ነገር፡ግን፡ ከመንፈስ፡ ቅዱስ፡ ተመርተው፡ የእግዚአብሔር፡ቅዱሳን፡ ሰዎች፡ ተናገሩ።

## ምዕራፍ፡ ፪፡

፩፡ ነገር፡ግን፡ አሰተኞች፡ ነቢያት፡ በሕዝብ፡ ነበሩ፡በላንትም፡እንደሁ፡*አስተኞች፡መምህራን፡ይሆናሉ፡ የጥፋትን፡ ኑፋቄ፡ በሰውር፡ የሚያገቡ፡ የገዛቸውንም፡ጌታ፡ የሚክዱ፡ ፈጥነውም፡ በራሳቸው፡ ላይ፡ ጥፋት፡ የሚያመጡ።
*ማቴ፡ ፳፬፡ ፲፩።
፩፡ ጢሞ፡ ፬፡ ፩።

፪፡ *ብዙም፡ ሰዎች፡ ይከተሉዋቸዋል፡ በርኩስነታቸው፡ ከርሳቸውም፡ የተነሣ፡ የውነት፡ መንገድ፡ ይሰደባል።
*፪፡ ጢሞ፡ ፬፡ ፫፡ ፬።

፫፡ ኩብትንም፡በመውደድ፡በምናምንም፡ነገር፡ይረቡባችኋል።እሌህ፡ ፍርዳቸው፡ከብዙ፡ ዘመን፡ጀምሮ፡ የማይዘገይም፡ ጥፋታቸውም፡ አይተኛም።

፬፡ እግዚአብሔር፡ ያላዘነ፡ ከሆነ፡ ስለ፡ በደሉት፡ *መላእክት። ነገር፡ ግን፡ ወደ፡ ጨለማ፡ በታች፡ አወረዳቸው፡ በሰንሰለትም፡ ታሠረው፡ ለፍርድ፡ ሊጠበቁ፡ አሳልፎ፡ሰጣቸው።
*ይሁዳ፡ ቍ፡ ፮።

፭፡ ለቀደመውም፡ ዓለም፡ አልራራለትም፡ ስምንተኛውን፡ኖህን፡ጠበቀው፡እንጂ፡ የጽድቅን፡ አስተማሪ፡የጥፋትንም፡ ውኃ፡ አመጣ፡ በኃጢአተኞች፡ ዓለም፡ላይ።
ም፡ ፫፡ ፮። ዘፍ፡ ፯፡ ፲፯።

፮፡ *የሶደምንና፡የገሞራንም፡አገር፡ በእሳት፡ አቃጥሎ፡ †ለጥፋት፡ ፈረደባት፡ ለሚመጡ፡ ዓመጸኞችም፡ ምሳሌ፡ አደረጋት።
*ዘፍ፡ ፲፱፡ ፳፬።
†ዕብ፡ ፲፩፡ ፯።

፯፡ ሎጥንም፡ጻድቁን፡ አዳነው፡ ከክፉ፡ ስራቸው፡ ካባሔዷቸውም፡ ርኩስነት፡ አዝኖ፡ የነበረውን።

፰፡ በርሳቸው፡ መካከል፡ ጻድቁ፡ ተቀምጦ፡ ሳለ፡ በየቀኑ፡ጻድቅ፡ነፍሱን፡ በኃጢአት፡ነገር፡ *ያሳዝን፡ ነበረና፡ በማየትም፡ በመስማትም።
*መዝ፡ ፻፲፱፡ ፻፶፰። ሕዝ፡ ፱፡ ፬።

፱፡ እግዚአብሔር፡ ያውቃል፡ የሚያመልኩትን፡ ከመከራ፡ያድን፡ዘንድ፡ ኃጢአተኞችን፡ግን፡ ለፍርድ፡ቀን፡ሊሣቀዩ፡ይጠብቃቸዋል።
፩፡ ቆሮ፡ ፲፡ ፲፫።
ራእ፡ ፫፡ ፲።

፲፡ ይልቁንም፡ ከሥጋ፡በኋላ፡ የሚሔዱ፡ በርኩሰት፡መመኘት። ጌትነትንም፡ ይንቃሉ። እርሳቸውም፡ ደፋሮች፡ ናቸው። ትቢተኞች። የሥልጣኑንም፡ ገናንነት፡ሲሰድቡ፡ አይፈሩም።

፲፩፡ መላእክትም፡ ከርሳቸው፡ በኃይል፡ በችሎትም፡የሚበልጡ፡ የስድቡን፡ ፍርድ፡ አያመጡባቸው፡ በእግዚአብሔር፡ ፊት።

፲፪፡ እሌህ፡ ግን፡ *አእምሮ፡ እንደሌላቸው፡ የፍጥረታቸውንም፡ ዝንባሌ፡ እንደሚከተሉና፡ ለመጸመድና፡ለጥፋት፡እንደተፈጠሩ፡እንስሶች፡ ናቸው፡ የማያውቁትን፡ይሰድባሉ፡በጥፋታቸውም፡ ይጠፋሉ፡ የኃጢአታቸውንም፡ዋጋ፡ ይወስዳሉ።
*ኤር፡ ፲፪፡ ፫።
ይሁዳ፡ ቍ፡ ፲።

፲፫፡ ደስታቸውን፡በቀን፡ መቀማጠል፡ ይቈጥሩታል። እርሳቸውም፡ ርኩሶች፡ ነውረኞች። በመታለላቸው፡ራሳቸውን፡ የሚያወፍሩ፡ከላንት፡ጋራ፡ በተከማቹ፡ጊዜ፡ በምሳ።

፲፬፡ ለርሳቸውም፡ ምንዝር፡ የመላበት፡ ዓይን፡ አላቸው። ከኃጢአት፡ የማይጸግቡ፡ ናቸው፡ ያልጸኑትንም፡ነፍስ፡ያታላሉ።ከብትን፡ በመውደድ፡ የለመደ፡ልብ፡ አላቸው። የተረገሙ፡ ልጆች።

፲፭፡ የቀናውን፡ መንገድ፡ ትተው፡ ጠፉ። *የበለዓምንም፡ የቦሶርን፡ልጅ፡መንገድ፡ ተከተሉ። ይህ፡ የግፍ፡ዋጋ፡ የወደደ።
*ዘኍል፡ ፳፪፡ ፯። ራእ፡ ፪፡ ፲፬።

፲፮፡ የጥማምምናቱንም፡ ዘለፋ፡ ተቀበለ፡ ከማትናገር፡ አህያ፡ በሰው፡ ቃል፡ የተናገረች፡ የነቢዩንም፡ ስንፍና፡ የከለከለች።
ዘኍል፡ ፳፪፡ ፳፰።

፲፯፤ እሌህ፡ውኃ፡የሌለባቸው፡ ምንጮች፡ናቸው። ጭጋግም፡ከዐርፋት፡የሚነዳው። ጥቁር፡ጨለማ፡ ለዘላለም፡የተጠበቀላቸው።

፲፰፤ የተንበርጣጭና፡ የከንቱ፡ ነገር፡ ሲናገሩ፡ በስሕተት፡ከሚሔዱ፡በውነት፡ ያመለጡን፡ ሰዎች፡በሥጋ፡ መመኘት፡ በሴሰኝነትም፡ ያገብላሉ።

፲፱፤ የሰው፡ ልጅነት፡ ተስፋ፡ ያደርጋሉ፡ እርሳቸውም፡ የጥፋት፡ገሮች፡ናቸው። ሰው፡ከማንም፡ ቢሸነፍ፡ ለርሱ፡ እንደ፡ ገርያው፡ ደግሞ፡ ይገዛዋልና።

ዮሐ፡ ፰፡ ፴፬።

፳፤ በጌታችንና፡ በመድኃኒታችን፡ በየሱስ፡ ክርስቶስ፡እውቀት፡ ከዓለም፡ርኩሰት፡ካመለጡ፡ በርሱዋ፡ ደግሞ፡ ቢያዙና፡ቢገለበጡ፡*የኋለኛዪቱ፡ ከፊተኛዪቱ፡የምትከፋ፡ ትሆንላቸዋለች። *ማቴ፡ ፲፪፡ ፵፭።

፳፩፤ ይሻላቸው፡ ነበርና፡ የጽድቅን፡ መንገድ፡ ባያውቁ፡ኪያውቋት፡ ከተሰጠቻቸውም፡ ከተቀደሰች፡ ትእዛዝ፡*ኪወጡ። *ሉቃ፡ ፲፪፡ ፵፯፡ ፵፰።

፳፪፤ እውነተኛ፡ ምሳሌም፡ ይመጣባቸዋል። *ውሻ፡ ወደ፡ ትፋቱ፡ ተመለሰ። እርያም፡ ታጥባ፡ ባዛባ፡ለመንከባለል፡ተመለሰች። *ምሳ፡ ፳፮፡ ፲፩።

ምዕራፍ፡ ፫፡

፩፤ ይህቺን፡ ሁለተኛ፡ መልእክት፡ ጻፍሁላችሁ፡ወዳጆቼ፡ ሆይ፡ በርሱዋ፡ ንጹሕ፡ ልባችሁን፡ የማነቃባት፡ በማሳሰብ። ም፡ ፩፡ ፲፫።

፪፤ ከቅዱሳን፡ነቢያት፡ ቀድሞ፡ የተባለውን፡ ነገር፡ ታስቡ፡ ዘንድ፡ የጌታችነንም፡ የየሱስ፡ ክርስቶስን፡ ትእዛዝ፡ በኛ፡ በሐዋርያቱ፡ የተሰጣችሁን።

፫፤ አስቀድማችሁ፡ ግን፡ ይህነን፡ እወቁ፡ በኋለኛው፡ዘመን፡ፌዘኞች፡ ይመጣሉና፡ በፈቃዳቸው፡ የሚሔዱ፡ የሚሉም። ፩፡ ጢሞ፡ ፬፡ ፩።

፬፤ ወዴት፡ አለ፡ የመምጣቱ፡ ተስፋ። አባቶች፡ ከሞቱ፡በኋላ፡ ሁሉ፡እንደ፡ህ፡ ነው፡ ከቀደመ፡ ፍጥረት፡ ጀምሮ። ኢሳ፡ ፭፡ ፲፱። ሕዝ፡ ፲፪፡ ፳፪።

ማቴ፡ ፳፬፡ ፵፰።

፭፤ ይህነን፡ አያውቁትምና፡ በራሳቸው፡ ፈቃድ፡ *ሰማይ፡ከጥንት፡እንደ፡ነበረ፡ †ምድርም፡ ከውኃ፡ በውኃም፡ ጸንታ፡ በእግዚአብሔር፡ ቃል።

*ማቴ፡ ፳፬፡ ፴፰። †ዘፍ፡ ፩፡ ፪፡ ፮። መዝ፡ ፳፬፡ ፪።

፮፤ በርሱዋም፡በዚያን፡ጊዜ፡ የነበረው፡ ዓለም፡ ሠጠመ፡ጠፋም። ም፡ ፪፡ ፭። ዘፍ፡ ፯፡ ፳፩።

፯፤ ዛሬም፡ የሚሆኑ፡ ሰማያት፡ ምድር፡ በዚች፡ ቃል፡ጸንተዋል፡ለሳት፡ ተጠብቀው፡እስከ፡ ፍርድ፡ ቀን፡ እስከ፡ ኃጢአተኞችም፡ጥፋት፡ ቀን። ቍ፡ ፲።

፰፤ ነገር፡ ግን፡ይህ፡ነገር፡ ከላንት፡ አይሰወር፡ ወዳጆቼ፡ሆይ፡ አንድ፡ቀን፡ በእግዚአብሔር፡ ዘንድ፡ እንደ፡ ሺህ፡አመት፡ ነውና፡ ሺህም፡ አመት፡ እንደንድ፡ ቀን።

መዝ፡ ፺፡ ፬።

፱፤ *የእግዚአብሔር፡ተስፋ፡አይዘገይም፡ ሰዎች፡ ይዘገያል፡ እንዲመስላቸው፡ ነገር፡ ግን፡ እርሱ፡ ይታገሥልናል፡ ማንም፡ ቢጠፋ፡ አይወድምና፡ ሁሉም፡ ወደ፡ ተንስሐ፡ ይመጡ፡ ዘንድ፡ ይወዳል፡ እንጂ።

*እንባ፡ ፪፡ ፫። †፩፡ ጢሞ፡ ፪፡ ፬።

፲፤ የእግዚአብሔር፡ *ቀን፡እንደ፡ሌባ፡ ይመጣልና፡ †ሰማያት፡ በታላቅ፡ መንቃቃት፡ የሚያልፉበት፡ የፍጥረትም፡ ሁሉ፡ሥር፡ በሳት፡ ይፈታል፡ ምድርም፡ በርስዋም፡ያለ፡ ሥራ፡ ሁሉ፡ የሚቃጠልበት።

፪፡ ተሰ፡ ፭፡ ፪፡ ፫። †ቍ፡ ፯። ማቴ፡ ፳፬፡ ፳፱።

ራእ፡ ፳፡ ፲፩፤

፲፩፤ ይህም፡ ሁሉ፡ እንዲህ፡ የሚፈታ፡ ሲሆን፡ እንደ፡ምን፡ይገባችኋል፡ ትሆኑ፡ ዘንድ፡ በተቀደሰች፡ አካሔድ፡ በመልካምም፡ አምልኮት።

፲፪፤ የአምላክን፡ ቀን፡ መምጣት፡ ስትጠብቁ፡ ወደርሱም፡ስትቸኩሉ።ስለርሱ፡ሰማዮች፡ተቃጥለው፡ ይፈታሉ፡የፍጥረትም፡ሥር፡ ይቀልጣል፡ በትኩሳት።

፲፫፤ እኛ፡ግን፡እንደ፡ ተስፈው፡ *አዲሱን፡ ሰማይ፡ አዲሲቱንም፡ምድር፡ እንጠብቃለን፡ †ጽድቅ፡ የሚኖርባትን። *ኢሳ፡ ፷፭፡ ፲፯። ፷፮፡ ፳፪።

†ራእ፡ ፳፩፡ ፩፡ ፳፯።

፲፬፤ ስለዚህም፡ወንድሞቼ፡ ሆይ፡ ይህነን፡ ተስፋ፡ ብታደርጉ፡ ተጣንቀቁ፡ ከርሱ፡ በሰላም፡ያለ፡ ነውር፡ያለ፡ ርኩሰትም፡ ትገኙ፡ ዘንድ።

፲፭፤ የጌታችነንም፡ *ትዕግሥት፡ መድኃኒት፡ ቍጠሩት፡ ጳውሎስ፡ ደግሞ፡ የተወደደው፡ ወንድማችን፡ በተሰጠቸው፡ ብልሃት፡ እንደ፡ ጻፈላችሁ።

*ሮሜ፡ ፪፡ ፬።

፲፮፤ እንደላችም፡ በመልእክቱ፡ ሁሉ፡ ስለዚህ፡ ነገር፡ሲናገርባት። መታወቋ፡ የጸና፡ነገር፡ ያለባት፡ የሚያጣምዋት፡ እሊያ፡ እውቀትና፡ ጽናት፡ የሌላቸው፡ ሌሎችን፡ መጻሕፍት፡ እንዲያጣሙ፡ ደግሞ፡ ወደ፡ ጥፋታቸው።

፲፯፤ እላንት፡ግን፡ ወዳጆቼ፡ ሆይ፡ ይህችን፡ ነገር፡ አስቀድማችሁ፡ አውቃችኋልና፡ *ተጠበቁ፡ በሰነፎች፡ ስሕተት፡ተወስዳችሁ፡ከጽናታችሁ፡ እንዳትወድቁ።

*ማር፡ ፲፫፡ ፭፡ ፱። ፴፫።

፲፰፤ ነገር፡ ግን፡ በጸጋ፡ ብዙ፡ በጌታችንም፡ በመድኃኒታችንም፡ በየሱስ፡ ክርስቶስ፡ እውቀት። ለርሱ፡ ምስጋና፡ ይሁን፡ዛሬ፡ እስከ፡ ዘላለምን፡ ቀን፡ ድረስ። አሜን።

# የሐዋርያ ፡ የዮሐንስ ፡ መልእክት ፡ ከቶሊካዊት ፡ መጀመርያይቱ።

ምዕራፍ፡ ፩፤

፩፤ *ከመጀመርያ፡ ጀምሮ፡ የነበረ፡ የሰማነውም፡ ባይኖቻችንም፡ ያየነው፡ የተመለከትነውም፡ †እጆቻችንም፡ የዳሰሰችው፡ ስለ፡ ሕይወት፡ ቃል።
*ዮሐ፡ ፩፤ ፩፤ ፲፬፡፡ †ሉቃ፡ ፳፬፤ ፴፱፡፡

፪፤ *ሕይወትም፡ ተገለጸች፡ አየነም፡ እንመሰክር ማለን፡ በዘላለሙም፡ ሕይወት፡ እናስታውቃችኋለን፡ †በአብ፡ ዘንድ፡ በነበረች፡ ለኛም፡ በተገለጸች።
*ዮሐ፡ ፩፤ ፬፡፡ †ዮሐ፡ ፩፤ ፩፡፡

፫፡ ያየነውንም ፡ የሰማነውም ፡ እርሱን፡ እናስታውቃችኋለን፡ ለእናንተ፡ ደግሞ፡ ከኛ፡ ጋራ፡ አንድነት፡ ትሆንላችሁ፡ ዘንድ፡ የኛ፡ አንድነት፡ ግን፡ ከአብ፡ ጋራ፡ ናት፡ ከልጁ፡ም፡ ከየሱስ፡ ክርስቶስ፡ ጋራ።

፬፤ ይህችንም፡ ነገር፡ እንጽፋላችኋለን፡ *ደስታችሁ፡ ትፈጽም፡ ዘንድ።   *ዮሐ፡ ፲፭፤ ፲፩፡፡ ና፡ ፲፮፤ ፳፬፡፡

፭፤ ከርሱም፡ የሰማናት፡ የነገርናችኋትም፡ መልእክት፡ ይህች፡ ናት። *እግዚአብሔር፡ ብርሃን፡ እንደ፡ ሆነ፡ ከቶም፡ ጨለማ፡ እንደ፡ ሌለበት። *መዝ፡ ፻፬፤ ፪፡፡
ዮሐ፡ ፰፤ ፲፪፡፡

፮፤ ከርሱ፡ ጋራ፡ አንድነት፡ አለን፡ ብንል፡ በጨለማ፡ ብንመላለስ፡ እንዋሻለን፡ እውነትንም፡ አናደርግም።
ም፡ ፪፤ ፬፡፡

፯፤ በብርሃን፡ ግን፡ ብንመላለስ፡ እርሱ፡ በብርሃን፡ እንዳለ፡ ለኛ፡ አንድነት፡ አለን፡ እርሱ፡ በርሳችን፡ የልጁ፡ም፡ የየሱስ፡ ክርስቶስ፡ ደም፡ ከኃጢአት፡ ሁሉ፡ ያነጻናል።

፰፤ ኃጢአት፡ የሌብነም፡ ብንል፡ እኛ፡ ራሳችነን፡ እናስታለን፡ እውነትም፡ የለችነም።

፱፤ በኃጢአታችን፡ *ብንናዘዝ፡ እርሱ፡ †የታመነና፡ ጻድቅ፡ ነው፡ ኃጢአታችነን፡ ይቅር፡ ይለን፡ ዘንድ፡ ከግፍም፡ ሁሉ፡ ያነጻን፡ ዘንድ።   *ም፡ ፳፰፤ ፲፫፡፡
†፩፤ ተሳ፡ ፭፤ ፳፬፡፡

፲፤ ኃጢአት፡ አልሰራነም፡ ብንል፡ አስተኛ፡ እናደርገዋለን፡ ቃሉም፡ በኛ፡ የልነም።

ምዕረፍ፡ ፪፤

፩፤ ልጆቼ፡ ሆይ፡ ይህችን፡ ነገር፡ እጽፋላችኋለሁ፡ ኃጢአት፡ እንደሰሩ። ከላንትም፡ ማንም፡ ኃጢአት፡ ቢሰራ፡ ከአብ፡ ዘንድ፡ *አማላጅ፡ አለነ፡ የሱስ፡ ክርስቶስ፡ ጻድቅ።   *ሮሚ፡ ፰፤ ፴፬፡፡ ዕብ፡ ፯፤ ፳፭፡፡

፪፤ እርሱም፡ የኃጢአታችን፡ *መታረቅ፡ ነው፡ ግን፡ ስለ፡ ኃጢአታችን፡ ብቻ፡ አይደለም፡ ስለ፡ ዓለም፡ ሁሉ፡ ኃጢአት፡ እንጂ።   *ቆላ፡ ፩፤ ፳፡፡

፫፤ በዚህም፡ እናውቃለን፡ እንድናውቀው፡ ትእዛዙን፡ ብንጠብቅ።

፬፤ አውቀዋለሁ ፡ *የሚል፡ ትእዛዙንም ፡ የማይጠብቅ፡ እርሱ፡ አስተኛ፡ ነው፡ እውነትም፡ የለበትም።
*ም፡ ፩፤ ፮፡፡ ና፡ ፬፤ ፳፡፡

፭፤ ቃሉን፡ ግን፡ *የሚጠብቅ፡ በዚህ፡ የእግዚአብሔር፡ ፍቅር፡ በውነት፡ ተፈጸመች፡ በዚህም፡ እናውቃለን፡ እኛ፡ በርሱ፡ እንዳለነ።   *ዮሐ፡ ፲፬፤ ፳፩፤ ፳፫፡፡

፮፤ እኔ፡ በርሱ፡ *እኖራለሁ፡ የሚል፡ ይሔድ፡ ዘንድ፡ ይገባዋል፡ እርሱ፡ እንደ፡ ሔደ።   *ዮሐ፡ ፲፭፤ ፬፤ ፭፡፡

፯፤ ወንድሞቼ፡ ሆይ፡ አዲስ፡ ትእዛዝ፡ የምጽፋላችሁ፡ አይደለሁም፡ ነገር፡ ግን፡ አሮጌይቱን፡ ትእዛዝ፡ ከጥንት፡ ከላንት፡ ጋራ፡ የነበረችውን። አሮጌይቱም፡ ትእዛዝ፡ እርስዋ፡ ናት፡ ከጥንቱ፡ የሰማችሁት፡ ነገር።

፰፤ ደግሞ፡ አዲስ፡ ትእዛዝ፡ እጽፋላችኋለሁ። ይህም፡ እውነት፡ ነው፡ በርሱ፡ በላንትም። *ጨለማ፡ አልፋዋልና፡ የውነትም፡ ብርሃን፡ ከዚህ፡ ወዲህ፡ ያበራል።
*ሮሚ፡ ፲፫፤ ፲፪፡፡

፱፤ እኔ፡ በብርሃን፡ አለሁ፡ የሚል፡ ወንድሙንም፡ *የሚጸላ፡ እርሱ፡ እስከ፡ ዛሬ፡ በጨለማ፡ ነው።
*ም፡ ፫፤ ፲፭፡፡ ና፡ ፬፤ ፳፡፡

፲፤ *ወንድሙን፡ የሚወድ፡ እርሱ፡ በብርሃን፡ ይኖራል፡ ማሰነከልም፡ የለበትም።   *ም፡ ፫፤ ፲፬፡፡

፲፩፤ ወንድሙን፡ ግን፡ የሚጸላ፡ እርሱ፡ በጨለማ፡ ነው፡ በጨለማም፡ ይመላለሳል፡ የሚሔድበትንም፡ አያውቅም፡ ጨለማ፡ ዓይኑን፡ አሳውሮታልና።

፲፪፤ እጽፋላችኋለሁ፡ እላንተ፡ ልጆች፡ ኃጢአታችሁ፡ *ተሰረየችላችሁና፡ ስለ፡ ስሙ።   *ሉቃ፡ ፳፬፤ ፵፯፡፡
የሐዋ፡ ፬፤ ፲፪፡፡

፲፫፤ እጽፋላችኋለሁ፡ እላንተ፡ አባቶች፡ ከጥንት፡ የነበረውን፡ አውቃችኋልና። እጽፋላችኋለሁ፡ እላንተ፡ ጐበዛዝት፡ ክፉውን፡ አሸንፋችኋልና። እጽፋላችኋለሁ፡ እላንተ፡ ሕፃናት፡ አብን፡ አውቃችኋልና።

፲፬፤ ጻፍሁላችሁ፡ እላንተ፡ አባቶች፡ ከጥንት፡ ጀምሮ፡ የነበረውን፡ አውቃችኋልና። ጻፍሁላችሁ፡ እላንተ፡ ጐበዛዝት፡ እላንተ፡ *በርትታችኋልና፡ የእግዚአብሔርም፡ ነገር፡ ጸንቶባችኋል፡ ክፉውንም፡ ድል፡ ነሥታችኋል።   *ኤፌ፡ ፮፤ ፲፡፡

፲፭፤ ዓለምን፡ አትውደዱ፡ በዓለምም፡ ያለውን። ዓለምን፡ በሚወድ፡ ሰው፡ የእግዚአብሔር፡ ፍቅር፡ የለበትም።   ያዕ፡ ፬፤ ፬፡፡

፲፮፤ በዓለም፡ ያለው፡ ሁሉ፡ የሥጋ፡ መመኛት፡ የዓይንም፡ መመኛት፡ የሰውም፡ ትምክሕት። ይህም፡ ከአብ፡ አይደለም፡ ከዓለም፡ እንጂ።

፲፯፡ ዓለሙም፡ ያልፋል፡ ምኞቱም። የእግዚአብሔርን፡ ፈቃድ፡ ግን፡ የሚያደርግ፡ እርሱ፡ ለዘላለሙ፡ ይኖራል።

፲፰፡ ልጆቼ፡ ሆይ፡ ይህች፡ የኋለኛዪቱ፡ ጊዜ፡ ናት። እንደ፡ ሰማችሁም፡ *ሐሳዊ፡ መሢሕ፡ እንዲመጣ። አሁንም፡አስተኞች፡ መሢሖች፡ እጅግ፡ ሆኑ። ከዚህም፡ የተነሣ፡ እናውቃለን፡ የኋለኛዪቱ፡ ጊዜ፡ እንደ፡ ሆነች።

*ማቴ፡ ፳፬፡ ፭፡ ፳፬፡፡

፲፱፡ ከኛ፡ *ወጡ፡ ነገር፡ግን፡ ከኛ፡ አልነበሩም። ከኛስ፡ ሁነው፡ በነበሩ፡ከኛ፡ጋራ፡ በጸኑ፡ነበር። ነገር፡ ግን፡ ወጡ፡ ይገለጡ፡ ዘንድ፡ ሁላቸው፡ ከኛ፡ እንዳልሆኑ።

*የሐዋ፡ ፳፡ ፴፡፡ ፩፡ ቆሮ፡ ፲፩፡ ፲፱፡፡

፳፡ እላንትም፡መቅባት፡ አላችሁ፡ ከቅዱሱ፡ ሁሉንም፡ አውቃችኋል።

ቍ፡ ፳፯፡፡

፳፩፡ ወደላንት፡ አልጻፍሁም፡ እውነትን፡ ስላላወቃችሁ። ታውቁታላችሁና፡ እንጂ፡ አስትም፡ ሁሉ፡ ከውነት፡እንደይደለ።

፳፪፡ ማነው፡ አስተኛው፡ የሱስ፡ ክርስቶስ፡ እንደ ሆነ፡ከሚክድ፡በቀር። ይህ፡ ነው፡ ሐሳዊ፡ መሢሕ፡ አብንና፡ ወልድን፡ የሚክድ።

፳፫፡ *ወልድን፡ የሚክድ፡ ሁሉ፡ አብ፡ ከርሱ፡ ጋራ፡ የለም። በወልድ፡ የሚያምን፡ አብም፡ ደግሞ፡ ከርሱ፡ ጋራ፡ ነው።

*ም፡ ፬፡ ፲፭፡፡

፳፬፡ እላንት፡ግን፡ከጥንቱ፡ የሰማችሁት፡ በላንት፡ ይጽና። ከጥንት፡ የሰማችሁት፡ በላንት፡ ቢጸና፡ እላንትም፡ ደግሞ፡ በአብና፡ በወልድ፡ ትጸናላችሁ።

፳፭፡ ይህም፡ተስፋው፡እርሱ፡ የሰጠን፡ ነው፡ የዘላለም፡ሕይወት።

፳፮፡ ይህችን፡ ነገር፡ ጻፍሁላችሁ፡ ስለሚያስቱዋችሁ።

፳፯፡ ከርሱ፡የወሰዳችኋትም፡*መቅባት፡ በላንት፡ ትጸናባችኋለች፡ማንም፡ ያስተምራችሁ፡ ዘንድ፡አትሹም። እንደዚሁ፡ መቅባት፡ ያስተምራችኋል፡ እንጂ፡ ስለ፡ ሁሉ። እርሱም፡ እውነተኛ፡ ነው፡ አስትም፡ አይደለም። እንደስተማራችሁም፡ ትጸኑበታል።

*ዮሐ፡ ፲፬፡ ፳፮፡፡ ፫፡ ፲፮፡ ፲፫፡፡

፳፰፡ አሁንም፡ልጆቼ፡ ሆይ፡ ጽኑበት፡እርሱ፡ በተገለጠ፡ጊዜ፡ድፍረት፡ይሆንልን፡ዘንድ፡ እኛም፡ ከፊቱ፡ እናፍርም፡ በመገለጡ።

ም፡ ፫፡ ፳፩፡፡

፳፱፡ ጻድቅ፡ እንደሆነ፡ ካወቃችሁ፡ እወቁ፡ *ጽድቅ፡ የሚሰራ፡ ሁሉ፡ ከርሱ፡ የተወለደ፡ እንደሆነ።

*ም፡ ፫፡ ፯፡ ፲፡፡

ምዕራፍ፡ ፫፡

፩፡ እዩ፡እንዴት፡ያለውን፡ፍቅር፡ሰጠን፡ አብ፡ *የእግዚአብሔር፡ ልጆች፡ እንባል፡ ዘንድ። ስለዚህ፡ ዓለም፡ †አያውቅነም፡ እርሱን፡ አላወቀምና።

*ዮሐ፡ ፩፡ ፲፪፡ ፲፫፡፡ †ዮሐ፡ ፲፮፡ ፫፡፡

፪፡ ወደጆቼ፡ ሆይ፡ እኛ፡ አሁን፡ የእግዚአብሔር፡ ልጆች፡ነን። *ገናም፡ምን፡ እንሆናለን፡ አልተገለጠም፡ ነገር፡ ግን፡ እርሱ፡ በተገለጠ፡ጊዜ፡ እንደርሱ፡ እንድን ሆን፡አወቅነ። እናየዋለንና፡ እርሱ፡ እንዳለ።

*ሮሜ፡ ፰፡ ፲፯፡፡ ቈላ፡ ፫፡ ፬፡፡

፫፡ ይህችም፡ተስፋ፡ያለችው፡ሁሉ፡ራሱን፡ያነጻል፡ እርሱም፡ንጹሕ፡እንደ፡ሆነ።

፬፡ ኃጢአትን፡የሚያደርግ፡ ሁሉ፡ ሕግንም፡ መተላለፍ፡ ያደርጋል። ኃጢአትም፡ እርሱ፡ ሕግን፡ መተላለፍ፡ ነው።

፭፡ እላንትም፡ ታውቃላችሁ፡ ያ፡ እንደ፡ ተገለጠ፡ ኃጢአታችንን፡ ሊያስወግድ። ኃጢአትም፡ በርሱ፡ የለም።

ኢሳ፡ ፶፫፡ ፬፡ ፭፡፡ ፩፡ጴጥ፡ ፪፡ ፳፬፡፡

፮፡ በርሱ፡ የሚኖር፡ሁሉ፡ ኃጢአት፡ አይሰራም። ኃጢአት፡ የሚሰራ፡ ሁሉ፡ አላየውም፡ አላወቀውምም።

ሮሜ፡ ፮፡ ፲፬፡፡

፯፡ ልጆቼ፡ ሆይ፡ ማንም፡ አያስታችሁ። ጽድቅ፡ የሚያደርግ፡ ጻድቅ፡ነው፡ ያም፡ ጻድቅ፡ እንደ፡ ሆነ።

ም፡ ፪፡ ፳፱፡፡

፰፡ ኃጢአትም፡ የሚያደርግ፡ እርሱ፡ ከሰይጣን፡ ነው፡ ሰይጣኑ፡ ከጥንት፡ ኃጢአትን፡ አድርጓልና። ስለዚህ፡ተገለጠ፡ የእግዚአብሔር፡ ልጅ፡ የሰይጣንን፡ ስራ፡ ሊሽር።

ዮሐ፡ ፰፡ ፵፬፡፡

፱፡ ከእግዚአብሔር፡ የሚወለድ፡ ሁሉ፡ ኃጢአት፡ አያደርግም። ዘሩ፡ጸንቶበታልና፡ ኃጢአትም፡ይሰራ፡ ዘንድ፡ አይችልም። ከእግዚአብሔር፡ የተወለደ፡ ነውና።

ቍ፡ ፱፡ ም፡ ፭፡ ፲፰፡፡

፲፡ በዚህ፡ ይታወቃሉ፡ የእግዚአብሔር፡ ልጆች፡ የሰይጣንም፡ልጆች። ጽድቅ፡ የማያደርግ፡ ሁሉ፡ ከእግዚአብሔር፡ አይደለም፡ ወንድሙንም፡ የማይወድ፡ እንደሁ፡ ነው።

፲፩፡ ይህ፡ ነው፡ ከቀደመው፡ የሰማችሁት፡ ትእዛዝ፡እርሱ፡ በርሳችን፡እንዋደድ፡ ዘንድ።

ዮሐ፡ ፲፫፡ ፴፬፡፡

፲፪፡ ከክፉ፡ እንደ፡ ሆነ፡እንደ፡ *ቃየል፡ አይደለም፡ ወንድሙንም፡ገደለው። ለምንስ፡ገደለው። ስራው፡ ክፉ፡ ነበረና፡ የወንድሙ፡ ግን፡ መልካም፡ ነበር።

ዘፍ፡ ፬፡ ፰፡፡ ማቴ፡ ፳፫፡ ፴፭፡፡ ይሁ፡ ቍ፡ ፲፩፡፡

፲፫፡ አታድንቁ፡ ወንድሞቼ፡ ሆይ፡ ዓለም፡ ቢጸላችሁ።

ማቴ፡ ፭፡ ፲፩፡፡ ዮሐ፡ ፲፭፡ ፲፰፡ ፲፱፡፡

፲፬፡ እኛ፡ከሞት፡ወጥተን፡ ወደ፡ ሕይወት፡ እንደ፡ ደረስነ፡ *እናውቃለን። ወንድሞችን፡ እንወዳለንና። †ወንድሙን፡ የማይወድ፡ በሞት፡ ይኖራል።

*ዮሐ፡ ፭፡ ፳፬፡፡ ም፡ ፪፡ ፲፩፡፡ †ዘሌዋ፡ ፱፡ ፲፯፡፡

፲፭፡ ወንድሙን፡የሚጸላ፡ሁሉ፡ነፍስ፡ገዳይ፡ነው። እላንትም፡ ታውቃላችሁ፡ ነፍስ፡ ገዳይ፡ ሁሉ፡ የዘላለም፡ሕይወት፡ እንደሌለው።

ማቴ፡ ፭፡ ፳፩፡ ፳፪፡፡

፲፮፡ በዚህ፡ ፍቅሩን፡ አወቅነ፡ ስለኛ፡ ራሱን፡ ለውጦታልና። ለኛም፡ይገባል፡ራሳችንን፡ስለ፡ ወንድሞች፡ እንለውጥ፡ ዘንድ።

፲፯፡ የዚህ፡ዓለም፡ጥሪት፡ያለው፡ ወንድሙንም፡
አንዳች፡ሲሻ፡ የሚያየው፡ ርኅራኄውንም፡ የሚከለ
ክልበት፡ የእግዚአብሔር፡ ፍቅር፡ እንዴት፡ ይኖርበ
ታል። ም፡ ፬፡ ፳።
፲፰፡ ልጆቼ፡ ሆይ፡ አንውደድ፡ በቃል፡ በመላስም፡
በሥራ፡በውነት፡እንጂ። ያዕ፡ ፩፡ ፳፪። ፕ፡ ፪፡ ፲፭።
፲፱፡ በዚህም፡ እናውቃለን፡ እኛ፡ ከውነት፡ እንደ
ሆነ፡ በፊቱም፡ ልባችነን፡ እናሳርፋለን።
፳፡ ልባችን፡ ቢነቅፈን፡ እግዚአብሔር፡ ከልባችን፡
ይበልጣልና፡ ሁሉንም፡ ያውቃል።
፳፩፡ ወዳጆቼ፡ ሆይ፡ልባችንስ፡ባይነቅፈን፡ *ድፍረ
ት፡አለነ፡ወደ፡እግዚአብሔር። *ም፡ ፪፡ ፳፰።
ፕ፡ ፬፡ ፲፯። ሮሚ፡ ፭፡ ፩፡ ፪። ዕብ፡ ፬፡ ፲፮።
፳፪፡ የምንለምነውንም፡ ሁሉ፡ ከርሱ፡ እንወስደ
ለን፡ ትእዛዙንም፡ እንጠብቃለንና፡ በፊቱም፡ ደስ፡
የሚያሰኘውን፡ነገር፡እናደርጋለንና። ማር፡ ፲፩፡ ፳፬።
፳፫፡ *ትእዛዙም፡ ይህች፡ ናት፡ እናምን፡ ዘንድ፡በ
ልጁ፡ በየሱስ፡ ክርስቶስ፡ ስም፡ እርሱ፡ በርሳችንም፡
†እንዋደድ፡ዘንድ፡ትእዛዙን፡ እንደ፡ ሰጠ።
*ዮሐ፡ ፮፡ ፳፱። †ማር፡ ፲፪፡ ፴፩።
፳፬፡ ትእዛዙንም፡ *የሚጠብቅ፡ በርሱ፡ ይኖራል፡
እርሱም፡ ደግሞ፡ በርሱ፡ ይኖራል። በዚህም፡ እናው
ቃለን፡ እርሱ፡ በኛ፡ እንዲኖር፡ ለኛ፡ ከሰጠው፡ ከመን
ፈሱ። *ዮሐ፡ ፲፬፡ ፳፫።

ምዕራፍ፡ ፬፡

፩፡ ወዳጆቼ፡ ሆይ፡ መንፈስን፡ ሁሉ፡ አትመኑ። መ
ናፍስትን፡ ፈትኑ፡ እንጂ፡ ከእግዚአብሔር፡ እንደ፡ሆ
ኑ፡ ብዙ፡ ሐሰት፡ ነቢያት፡ ወደ፡ ዓለም፡ ወጥተዋልና።
፪፡ በዚህ፡የእግዚአብሔርን፡ መንፈስ፡ታውቃላች
ሁ።የሚያምን፡መንፈስ፡ሁሉ፡የሱስ፡ክርስቶስ፡ በሥ
ጋ፡ እንደ፡ መጣ፡ እርሱ፡ ከእግዚአብሔር፡ ነው።
፩፡ ቆሮ፡ ፲፪፡ ፫።
፫፡ የማያምንም፡መንፈስ፡ሁሉ፡ የሱስ፡ክርስቶስ፡
በሥጋ፡ እንደ፡ መጣ፡እርሱ፡ ከእግዚአብሔር፡ አይደ
ለውም። ይህም፡ የሐሳዊ፡ መሢሕ፡ መንፈስ፡ ነው፡
እንዲመጣ፡ የሰማችሁት፡ አሁንም፡ እርሱ፡ በዓለ
ም፡ ነው።
፬፡ እላንተ፡ከእግዚአብሔር፡ ናችሁ፡ ልጆቼ፡ ሆይ፡
አሸንፋችኋቸውማል፡ በላንተ፡ ያለው፡ ይበልጣልና፡
በዓለም፡ካለው። ፪፡ ነገሥ፡ ፮፡ ፲፮። ፩፡ ዜና፡ ፴፪፡ ፯።
፭፡ እርሳቸው፡ ከዓለም፡ ናቸው። ስለዚህ፡ ከዓለ
ም፡ ይናገራሉ፡ ዓለምም፡ ይሰማቸዋል።
ዮሐ፡ ፫፡ ፴፩። ፕ፡ ፲፭፡ ፲፱።
፮፡ እኛ፡ ከእግዚአብሔር፡ ነን። እግዚአብሔርን፡
የሚያውቅ፡ ይሰማናል። ከእግዚአብሔር፡ ያልሆነ፡
አይሰማነም። በዚህ፡ እናውቃለን፡ የውነቱን፡ መን
ፈስና፡ የስሕተቱን፡መንፈስ። ዮሐ፡ ፰፡ ፵፯።
፯፡ ወዳጆቼ፡ ሆይ፡ እርሱ፡ በርሳችን፡ እንዋደድ፡ ፍ
ቅር፡ ከእግዚአብሔር፡ናትና። የሚወድም፡ ሁሉ፡ ከ
እግዚአብሔር፡ የተወለደ፡ ነው፡ እግዚአብሔርንም፡
ያውቃል።
፰፡ የማይወድም፡ እግዚአብሔርን፡ አላወቀም።
እግዚአብሔር፡ ፍቅር፡ ነውና።
፱፡ በዚህ፡ ተገለጠ፡ የእግዚአብሔር፡ ፍቅር፡ ወደ
ኛ፡ እግዚአብሔር፡ አንድ፡ ልጁን፡ ወደ፡ ዓለም፡ ልኳ
ልና፡ በርሱ፡ እንድንበት፡ ዘንድ። ዮሐ፡ ፫፡ ፲፮።
ቲቶ፡ ፪፡ ፲፩።
፲፡ ፍቅርም፡ በዚህ፡ ናት። እኛ፡ እግዚአብሔርን፡ እ
ንደ፡ ወደድነው፡ አይደለም፡ እርሱ፡ እንደ፡ ወደደነ፡
እንጂ። ልጁንም፡ እንደ፡ ላከ፡ ማስተስረያ፡ ይሆን፡
ዘንድ፡ ስለ፡ ኃጢአታችን። ሮሜ፡ ፭፡ ፲።
፪፡ ቆሮ፡ ፭፡ ፲፱። ቆላ፡ ፩፡ ፳።
፲፩፡ ወዳጆቼ፡ ሆይ፡ እግዚአብሔር፡ እንደዚህ፡ የወ
ደደነ፡ ከሆነ፡ ለኛም፡ እርሱ፡ በርሳችን፡ እንዋደድ፡ ዘ
ንድ፡ ይገባናል። ማቴ፡ ፲፰፡ ፴፫።
፲፪፡ እግዚአብሔርን፡ ማንም፡ ከቶ፡ አላየውም።
እርሱ፡ በርሳችን፡ ብንዋደድ፡ እግዚአብሔር፡ ይኖር
ብናል። ፍቅሩም፡ በኛ፡ የተፈጸመች፡ ናት።
*ዘፀአ፡ ፴፫፡ ፳። ዮሐ፡ ፩፡ ፲፰። ፩፡ ጢሞ፡ ፮፡ ፲፮።
፲፫፡ በዚህ፡ እናውቃለን፡ እኛ፡ በርሱ፡ እንድንኖር፡
እርሱም፡ በኛ፡ ከመንፈሱ፡ ሰጥቶናልና።
፲፬፡ እኛም፡አይተናል፡እንመሰክርማለን፡ አብ፡ ል
ጁን፡እንደ፡ላከ፡የዓለም፡መድኃኒት፡ ይሆን፡ ዘንድ።
፲፭፡ የሱስ፡የእግዚአብሔር፡ልጅ፡ እንደ፡ሆነ፡ የሚ
ያምን፡ እግዚአብሔር፡ ይኖርበታል፡ እርሱም፡ በእግ
ዚአብሔር፡ ይኖርበታል፡ እርሱም፡በእግዚአብሔር።
ም፡ ፭፡ ፭።
፲፮፡ እግዚአብሔርም፡ ወደኛ፡ ያለችውን፡ ፍቅር፡
እኛ፡ አወቅነ፡ አመንነም። እግዚአብሔር፡ ፍቅር፡
ነው። በፍቅርም፡ የሚኖር፡ በእግዚአብሔር፡ ይኖራ
ል፡ እግዚአብሔርም፡ በርሱ።
፲፯፡ በዚህ፡ ፍቅሩ፡ ከኛ፡ ጋራ፡ ተፈጸመች፡ ድፍረ
ት፡ ትሆንልን፡ዘንድ፡ በፍርድ፡ቀን። እርሱ፡እንደሆነ፡
እንደሁም፡ እኛ፡ በዚህ፡ ዓለም፡ ነን። ም፡ ፫፡ ፳፩።
፲፰፡ በፍቅር፡ ፍርሃት፡ የለም። የተፈጸመች፡ ፍቅ
ር፡ፍርሃትን፡ወደ፡ሚደ፡አውጥታ፡ትጥላለች፡እንጂ።
በፍርሃት፡ ሥቃይ፡ነውና። የሚፈራም፡ በፍቅር፡ አል
ተፈጸመም።
፲፱፡ እኛ፡እንወደዋለን፡ እርሱ፡አስቀድሞ፡ወደና
ልና።
፳፡ እግዚአብሔርን፡ እወደለሁ፡ ብሎ፡ ወንድሙ
ን፡ የሚጸላ፡አስተኛ፡ነው። ያየውን፡ ወንድሙን፡ ያ
ልወደደ፡ ያላየውን፡እግዚአብሔርን፡ ይወድ፡ዘንድ፡
እንዴት፡ ይችላልና። *ም፡ ፪፡ ፬፡ ፲፩።
፳፩፡ ይህችንም፡ ትእዛዝ፡ ከርሱ፡ ተቀበልነ። እግ
ዚአብሔርን፡ የሚወድ፡ ወንድሙን፡ ደግሞ፡ እንዲ
ወድ። ማር፡ ፲፪፡ ፴፩።

ምዕራፍ፡ ፭፡

፩፤ የሚያምን፡ ሁሉ፡ የሱስ፡ ክርስቶስ፡ እንደ፡ ሆነ፡ እርሱ፡ ከእግዚአብሔር፡ የተወለደ፡ ነው። ወላጁን ም፡ የሚወድ፡ ሁሉ፡ ከርሱ፡ የተወለደውን፡ ደግሞ፡ ይወደል። ዮሐ፡ ፩፤ ፲፪፤ ፲፫።

፪፤ *በዚህ፡ እናውቃለን፡ እኛ፡ የእግዚአብሔርን፡ ልጆች፡ እንደ፡ ወደድን፡ እግዚአብሔርን፡ ብንወድ፡ ትእዛዙንም፡ ብንጠብቅ። *ም፡ ፫፤ ፲፬።

፫፤ የእግዚአብሔር፡ ፍቅር፡ ይህች፡ ናትና፡ *ትእዛዙን፡ እንጠብቅ፡ ዘንድ፡ ትእዛዙም፡ †የከበደች፡ አይደለችም። *ዮሐ፡ ፲፬፤ ፲፭፤ ፳፫፤ ፳፬። †ማቴ፡ ፲፩፤ ፴።

፬፤ ከእግዚአብሔር፡ *የተወለደ፡ ሁሉ፡ ዓለምን፡ ያሸንፈልና። ዓለምንም፡ †የምናሸንፍበት፡ ማሸነፊ፡ ሃይማኖታችን፡ ናት። *ዮሐ፡ ፩፤ ፲፫። †ዮሐ፡ ፲፮፤ ፴፫።

፭፤ ማነው፡ *ዓለምን፡ የሚያሸንፍ፡ የሱስ፡ የእግዚአብሔር፡ ልጅ፡ እንደ፡ ሆነ፡ ከሚያምን፡ እንጂ። *ም፡ ፬፤ ፬። ፩፡ ቆሮ፡ ፲፭፤ ፶፯።

፮፤ ይህ፡ ነው፡ በውኃና፡ በደም፡ የመጣው፡ እርሱም፡ የሱስ፡ ክርስቶስ። *በውኃ፡ ብቻ፡ አይደለውም፡ በውኃና፡ በደም፡ እንጂ። መንፈስም፡ የሚመሰክር፡ ነው። መንፈስ፡ እርሱ፡ እውነት፡ ነውና። †ዮሐ፡ ፲፱፤ ፴፬፤ ፴፭።

፯፤ በሰማይ፡ የሚመሰክሩ፡ *ሦስት፡ ናቸውና፡ እርሳቸውም፡ አብ፡ ቃልም፡ መንፈስ፡ ቅዱስም። እሌህ፡ ሦስትም፡ አንድ፡ ናቸው። *ማቴ፡ ፳፰፤ ፲፱።

፰፤ በምድርም፡ የሚመሰክሩ፡ ሦስት፡ ናቸው፡ እርሳቸውም፡ መንፈስ፡ ውኃም፡ ደምም። ሦስቱም፡ ባንድ፡ ይገድማሉ።

፱፤ የሰውን፡ ምስክር፡ ብንቀበል፡ የእግዚአብሔር፡ ምስክር፡ እጅግ፡ ይበልጣል። ይህች፡ የእግዚአብሔር፡ ምስክር፡ ናትና፡ ስለ፡ ልጁ፡ የመሰከረባት፡ ዮሐ፡ ፰፤ ፲፯፤

፲፤ በእግዚአብሔር፡ ልጅ፡ የሚያምን፡ ምስክር፡ በነፍሱ፡ አለው። ለእግዚአብሔር፡ የማያምን፡ አስተኛ፡ አደረገው፡ እግዚአብሔር፡ ስለ፡ ልጁ፡ በመሰከረባት፡ ምስክር፡ አላመነምና። ሮሚ፡ ፰፡ ፲፮። ዮሐ፡ ፫፤ ፴፮።

፲፩፤ ምስክሪቱም፡ ይህች፡ ናት። እግዚአብሔር፡ የዘላለምን፡ ሕይወት፡ እንደ፡ ሰጠነ። ይህችም፡ ሕይወት፡ በልጁ፡ አለች። ዮሐ፡ ፭፤ ፬።

፲፪፤ ወልድ፡ ያለው፡ ሕይወት፡ አለችው። የእግዚአብሔር፡ ልጅም፡ የሌለው፡ ሕይወት፡ የለችውም።

፲፫፤ ይህችን፡ ነገር፡ ጻፍሁላችሁ፡ እላንተ፡ በእግዚአብሔር፡ ልጅ፡ ስም፡ ያመናችሁ፡ ታውቁ፡ ዘንድ፡ የዘላለም፡ ሕይወት፡ እንደላችሁ።

፲፬፤ ይህችም፡ *ድፍረት፡ ናት፡ በኛ፡ ያለችው፡ ከርሱ፡ ዘንድ፡ እንደ፡ ፈቃዱ፡ አንዳችን፡ ብንለምነው፡ እርሱ፡ ሊሰማነ። *ም፡ ፪፤ ፳፰። ፫፤ ፳፩። ኤፌ፡ ፫፤ ፲፪። ዕብ፡ ፬፤ ፲፮።

፲፭፤ ብናውቅም፡ የለመነውን፡ እንዲሰማነ፡ እናውቃለን፡ ከርሱ፡ የለመናውን፡ ልመና፡ እንድንወስድ።

፲፮፤ ማንም፡ ወንድሙን፡ሞት፡ የማይገባት፡ ኃጢአት፡ ሲሰራ፡ ቢያየው፡ ይለምን፡ እግዚአብሔርም፡ ሕይወት፡ ይሰጠዋል። ሞት፡ የማይገባት፡ ኃጢአት፡ ለሚሰሩ። ሞት፡ የሚገባት፡ ኃጢአት፡ አለች። ስለ ርስዋ፡ የምል፡ አይደለሁም፡ ለርሱ፡ ይለምን፡ ዘንድ። ማቴ፡ ፲፪፤ ፴፩።

፲፯፤ ግፍ፡ ሁሉ፡ ኃጢአት፡ ነው፡ ለሞትም፡ የማት ሆን፡ ኃጢአት፡ አለች።

፲፰፤ *እናውቃለን፡ ከእግዚአብሔር፡ የተወለደ፡ ሁሉ፡ ኃጢአት፡ እንደ፡ ይሰራ፡ ከእግዚአብሔር፡ የተወለደ፡ ራሱን፡ ይጠብቃል፡ እንጂ፡ ክፉም፡ አይነካውም። *ም፡ ፫፤ ፱። ፪፡ ተስ፡ ፫፤ ፫።

፲፱፤ እኛም፡ እናውቃለን፡ ከእግዚአብሔር፡ እንደ፡ ሁነ፡ ዓለሙም፡ ሁሉ፡ በክፉ፡ ተይዝዋል። ገላት፡ ፩፤ ፬።

፳፤ እናውቃለን፡ ግን፡ የእግዚአብሔር፡ ልጅ፡ እንደ፡ መጣ፡ እውቀትንም፡ ሰጠነ። እውነተኛው፡ የሚሆነውን፡ እናውቅ፡ ዘንድ። እኛም፡ በውነተኛው፡ እንኖራለን፡ በልጁ፡ በየሱስ፡ ክርስቶስ። ይህ፡ ነው፡ *እውነተኛ፡ አምላክ፡ የዘላለሙም፡ ሕይወት። *ዮሐ፡ ፲፯፤ ፫። ሮሚ፡ ፱፤ ፭። ፩፡ ጢሞ፡ ፫፤ ፲፮። ዕብ፡ ፩፤ ፰።

፳፩፤ ልጆቼ፡ ሆይ፡ ከጣዖታት፡ ተጠበቁ። አሜን። ዘፀአ፡ ፳፤ ፫። ፩፡ ቆሮ፡ ፲፡ ፲፬።

# የሐዋርያ ፡ የዮሐንስ ፡ መልእክት ፡ ሁለተኛይቱ።

፩፤ ከሽማግሌው፡ ወደ፡ ተመረጠች፡ *እመቤትና፡ ልጆችዋ፡ እኔ፡ †ወደምወደቸው፡ በውነት። እኔም፡ ብቻ፡ አይደለሁም፡ እውነትን፡ የሚያውቁ፡ ሁሉ፡ እንጂ። *፩፡ ጴጥ፡ ፭፤ ፲፫። †፫፤ ዮሐ፡ ፩።

፪፤ ስለ፡ እውነት፡ ስለሚጸና፡ ለዘላለሙም፡ ከኛ፡ ጋራ፡ ይኖራል።

፫፤ ጸጋ፡ ምህረትም፡ ሰላምም፡ ከላንተ፡ ጋራ፡ ይሆኑ፡ ከእግዚአብሔር፡ አብ። ከጌታችንም፤ ከየሱስ፡ ክርስቶስ፡ ከአብ፡ ልጅ፡ በውነት፡ በፍቅርም።

፬፤ እጅግ፡ ደሳለኝ፡ ከልጆችሽ፡ አግኝቻለሁና፡ በውነት፡ የሚሔዱ፡ ከአብ፡ ትእዛዝ፡ እንደ፡ ወሰድናት።

፭፤ አሁንም፡ እኔ፡ እለምንሻለሁ፡ እመቤቴ፡ ሆይ፡

እዲስ፡ ትእዛዝ፡ እንደሚጽፍልሽ፡ አይደለም፡ ከጥንቱ፡ በኛ፡ የነበረችውን፡ ትእዛዝ፡ እንጂ። እርሱ፡ በርሳችን፡ እንዋደድ፡ ዘንድ። ፩፤ ዮሐ፡ ፪፤ ፫።

፮፤ ፍቅርም፡ ይህች፡ ናት፡ በትእዛዙ፡ እንሔድ፡ ዘንድ። ይህች፡ ትእዛዝ፡ ናት፡ ከጥንት፡ እንደ፡ ሰማችሁ፡ ትሔዱባት፡ ዘንድ።

፯፤ ብዙ፡ አሳቾች፡ ወደ፡ ዓለም፡ ገብተዋልና፡ የማያምኑ፡ የሱስ፡ ክርስቶስ፡ በሥጋ፡ እንደ፡ መጣ። ይህ፡ ነው፡ አሳች፡ ሐሳዊም፡ መሢሕ። ፩፤ ዮሐ፡ ፪፤ ፲፰። ፫፡ ፬፤ ፩—፫።

፰፤ ተጠበቁ፡ በራሳችሁ፡ ምግባራችነን፡ እንደናጠፋ፡ ፍጹምን፡ ዋጋ፡ እንድንወስድ፡ እንጂ። ገላት፡ ፬፤ ፲፩።

፱፤ የሚወጣ፡ ሁሉ፡ በክርስቶስ፡ ትምህርትም፡ የማይጸና፡ አምላክ፡ የለውም። በክርስቶስ፡ ትምህርት፡ የሚጸና፡ ለዚያ፡ አብና፡ ወልድ፡ አለው። ፩፤ ዮሐ፡ ፪፤ ፳፪፤ ፳፫።

፲፤ ማንም፡ ወደላንት፡ ቢመጣ፡ ይህነንም፡ ትምህርት፡ ባያመጣ፡ በቤታችሁ፡ አትቀበሉት፡ አትሳለሙት። ፪፤ ተሰ፡ ፫፤ ፮።

፲፩፤ እርሱን፡ የሚሳለመው፡ በክፉ፡ ስራው፡ ይገናኛዋልና።

፲፪፤ እጅግ፡ ነገር፡ አለኝ፡ የምጽፍላችሁ፡ ነገር፡ ግን፡ አልወደድሁም፡ በወረቀትና፡በቀለም፡እጽፍላችሁ፡ ዘንድ፡ ተስፋ፡ አደረጋለሁ፡እንጂ፡ወደላንት፡ እመጻ፡ ዘንድ፡ አፍ፡ላፍም፡ እነግራችኋለሁ፡ደስታችሁ፡ ፍጹም፡ ይሆን፡ ዘንድ። ፫፤ ዮሐ። ቍ፡ ፲፫።

፲፫፤ እንደትነሽ፡ ይሉኻል፡የተመረጠችው፡የትሽ፡ ልጆች። አሚን።

# የሐዋርያ ፡ የዮሐንስ ፡ መልእክት ፡ ሶስትኛዪቱ ።

፩፤ ከሽማግሌው፡ ወደ፡ ጋዮስ፡ወደ፡ ወዳጅ፡እኔ፡ *የምወደው፡ በውነት። *፪፤ ዮሐ። ቍ፡ ፩።

፪፤ ወዳጄ፡ ሆይ፡ ከሁሉ፡ በፊት፡ ደህና፡ ገላ፡ ጤናም፡ ትሆን፡ ዘንድ፡ እመኝልሃለሁ፡ ነፍስህ፡ ደህና፡ እንደ፡ ሆነች።

፫፤ እጅግ፡ ደስ፡ብሎኛልና፡ወንድሞች፡መጥተው፡ ስለ፡ እውነትህ፡ በመሰከሩ፡ ጊዜ፡ አንተ፡ በውነት፡ እንድትሔድ። ፪፤ ዮሐ፡ ፬።

፬፤ ከዚህ፡የበለጠ፡ ደስታ፡የለኝም፡እሰማ፡ዘንድ፡ ልጆቼ፡በውነት፡ እንዲሔዱ።

፭፤ ወዳጄ፡ ሆይ፡ መልካም፡ ስራ፡ ነው፡የምትሰራው፡ ሁሉ፡ በወንድሞች፡ በስደተኞችም።

፮፤ ስለ፡ ፍቅርህ፡ የመሰከሩ፡ በቤተ፡ ክርስቲያን፡ ፊት። መልካም፡ ትሰራለህ፡ በሰደድሃቸው፡ ጊዜ፡ ለ እግዚአብሔር፡ እንዲገባ። ቲቶ፡ ፫፤ ፲፫።

፯፤ ስለ፡ ስሙ፡ ወጥተዋልና፡ ከአሕዛብም፡ አንዳች፡ አልወሰዱም። ማቴ፡ ፲፤ ፰። ፪፤ ቆሮ፡ ፱፤ ፲፪፤ ፲፭።

፰፤ ለኛም፡ይገባናል፡እንደለዚህ፡ያሉትን፡እንቀበል፡ ዘንድ፡ የስራ፡ ባልንጀሮች፡ ከውነት፡ ጋራ፡ እንድን ሆን። ዕብ፡ ፲፫፤ ፪።

፱፤ ለቤተ፡ ክርስቲያን፡ ጻፍሁ፡ ነገር፡ ግን፡ ድዮትሬፍስ፡ በርሳቸው፡ ላይ፡ አለቅነት፡ የወደደ፡ አልተቀበለነም።

፲፤ ስለዚህም፡ በመጣሁ፡ ጊዜ፡ ባደረጋት፡ ስራ፡አሳስበዋለሁ፡ በክፉም፡ በኛ፡ ላይ፡ በሚናገርብን። በዚህም፡ ብቻ፡ አይበቃውም፡ ወንድሞችንም፡ አይቀበልምና። ይቀበልዋቸው፡ ዘንድ፡ የሚወዱንም፡ አይተውም፡ ከቤተ፡ ክርስቲያንም፡ ያወጣቸዋል።

፲፩፤ ወዳጅ፡ ሆይ፡ በክፉ፡ አትከተል፡ በመልካም፡ እንጂ፡ መልካም፡ የሚያደርግ፡ እርሱ፡ ከእግዚአብሔር፡ ነው። ክፉን፡ የሚያደርግ፡ እግዚአብሔርን፡ አላየውም። ፩፤ ዮሐ፡ ፫፤ ፮—፱።

፲፪፤ ድሜጥርስ፡ ከሁሉ፡ ተመስክሮለታል፡ ከእውነትም፡ ደግሞ። እኛም፡ደግሞ፡እንመሰክርለታለን፡ ምስክርነታችንም፡ *እውነት፡ እንደ፡ ሆነች፡ ታውቃላችሁ። *ዮሐ፡ ፲፱፤ ፴፭። ፫፡ ፳፩፤ ፳፬።

፲፫፤ እጅግ፡ ነገር፡ አለኝ፡ የምጽፍልህ፡ ነገር፡ ግን፡ አልሻሁም፡ በቀለምና፡ በብርዕ፡ እጽፍልህ፡ ዘንድ። ፪፤ ዮሐ፡ ቍ፡ ፲፪።

፲፬፤ ፈጥኜ፡ አይህ፡ ዘንድ፡ ተስፋ፡አደርጋለሁ፡ እንጂ፡ አፍ፡ ላፍም፡ እንናገራለን።

፲፭፤ ሰላም፡ላንተ፡ይሁን። ወዳጆቻችን፡እንደትነህ፡ ይሉሃል። አንተም፡ ወዳጆችን፡ እንደትናችሁ፡ በል፡ስሙን፡ ጠርተህ፡ በያንዳንዱ።

# የሐዋርያ ፡ የይሁዳ ፡ መልእክት ፡ ከቶሊካዊት ።

፩፤ ከይሁዳ፡ ከየሱስ፡ክርስቶስ፡ባርያ፡*ከያዕቆብ፡
ወንድም፡ በእግዚአብሔር፡ አብ፡ ወደ፡ ተጸሩት፡ በየ
ሱስ፡ ክርስቶስም፡ ወደ፡ ተጠበቁ፡ወደ፡ ተቀደሱ።
*ማቴ፡ ፲፫፡ ፶፭።

፪፤ ምህረት፡ሰላምም፡ፍቅርም፡ ትብዛላችሁ።
፫፤ ወዳጆቼ፡ ለሁላችን፡ ስላለ፡ ስለ፡ደህንነት፡እጽ
ፍላችሁ፡ ዘንድ፡ እጅግ፡ ታግሬ፡ ሳለሁ፡ እንዲገድ፡
አየሁት፡ ጽፌ፡ እመክራችሁ፡ ዘንድ፡ ለቅዱሳን፡ አን
ድ፡ ጊዜ፡ ለተሰጠችው፡ *ሃይማኖት፡ እንድትጋደሉ።
*፩፤ ጢሞ፡ ፩፤ ፲፰።

፬፤ ሰዎች፡ ቀስ፡ ብለው፡ ገብተዋልና፡ አስቀድሞ፡
ለዚህ፡ ፍርድ፡ የተጻፉ። እርሳቸውም፡እግዚአብሔ
ርን፡*የማይፈሩ፡ ያምላካችንንም፡ ጸጋ፡ በርኩሰት፡
የለወጡ፡ አንዱንም፡ አምላካችንንና፡ ጌታችንን፡የሱ
ስ፡ክርስቶስ፡ የካዱት። *ቲቶ፡ ፩፡ ፲፮።
፭፤ አሳስባችሁም፡ዘንድ፡ እወዳለሁ፡ ምንስ፡ አን
ደግዜ፡ ይህነን፡ ብታውቁት፡ እግዚአብሔር፡ ሕዝቡ
ን፡ ከግብጽ፡ ምድር፡ እንዳዳነ፡ ሁለተኛም፡ ያላመኑ
ትን፡ ፈጽሞ፡ እንደጠፋ። ዘኁል፡ ፲፬፡ ፴፭።
፩፡ ቆሮ፡ ፲፡ ፭።

፮፤ አለቅነታቸውንም፡ ያልጠበቁትን፡ ስፍራቸው
ንም፡ የተው፡ እንጂ፡ *መላእክት፡ በጨለማ፡ ውሥ
ጥ፡ ጠበቃቸው፡ በዘላለም፡ እሥራት፡ እስከ፡ ታላቁ፡
ቀን፡ ፍርድ። *ዮሐ፡ ፰፡ ፵፬።
፯፤ እንደ፡ሶዶምና፡እንደ፡ገሞራ፡በዙርያቸውም፡
እንደ፡ነበሩ፡አገሮች፡ዝሙት፡ያደረጉ፡እንደርሳቸው፡
ከሌላ፡ ሥጋም፡ በኋላ፡ የሔዱ፡ እርሳቸውም፡ ምሳ
ሌ፡ ሆኑ፡ሲሣቀዩ፡ በዘላለም፡እሳት።ዘፍ፡ ፲፱፡ ፳፬።
፰፤ እንደሁም፡ ደግሞ፡ እለዚህ፡ ሕልማሞች፡ሥ
ጋቸውን፡ያረክሳሉ፡ጌትነትንም፡ያቃላሉ፡ክብርንም፡
ይሰድባሉ።
፱፤ *ሚካኤል፡ ግን፡ የመላእክት፡ አለቃ፡ ከሰይጣ
ን፡ ጋራ፡ በተከራከረ፡ጊዜ፡ ስለ፡ ሙሴ፡ ሥጋ፡ ቢናገር።
በፍርዲ፡ ይሰድበው፡ ዘንድ፡ አልደፈረም፡ ነገር፡ ግን፡
አለው፡ እግዚአብሔር፡ †ይቈጣህ።
*ዳን፡ ፲፪፡ ፩። †ዘካ፡ ፫፡ ፪።
፲፤ እለዚህ፡ ግን፡ በማያውቁት፡ ነገር፡ይሳደባሉ፡ በ
ባሕርይም፡ የሚያውቁትን፡ ነገር፡ እእምሮ፡ እንደሌ
ለበት፡ እንስሳ፡ በርሱ፡ ይጠፋሉ። ፪፡ ጴጥ፡ ፪፡ ፲፪።
፲፩፤ ወዮላቸው። *በቃየል፡ መንገድ፡ ሒደዋልና፡
ስለ፡ ዋጋም፡ ራሳቸውን፡ †ለበለዓም፡ ስህተት፡አሳል
ፈው፡ ሰጡ፡ **በቆሬም፡ ክሕደት፡ አለቁ።
*ዘፍ፡ ፬፡ ፰። †ራእ፡ ፪፡ ፲፬። **ዘኁል፡ ፲፮፡ ፩፡፴፩።
፲፪፤ እሌህ፡በፍቅር፡ ምሳችሁ፡ ነውር፡ ናቸው፡ ከላ
ንት፡ ጋራ፡ ሲበሉ፡ ያለ፡ ፍርሃት፡ ራሳቸውን፡ ሲያሰማ
ሩ፡ ውኃ፡ እንደሌለባት፡ ደመና፡ ነፋስ፡ የምትነዳው፡
እንደ፡ጸደይም፡ዛፎች፡ የማያፈሩ። ሁለተ፡ ጊዜም፡
የሞቱ፡ ከሥራቸውም፡ የተነቀሉ።
፲፫፤ የሚተም፡ የባሕር፡ሞገድ፡ *ኃፍረቱን፡የሚያ
ረፍርፍ፡ ያለ፡ ሥርዓት፡የሚዞሩ፡ ከዋክብት፡ የዘላለ
ምም፡ ጽኑ፡ ጨለማ፡ ተጠብቆላቸዋል።
*ኢሳ፡ ፶፯፡ ፳።

፲፬፤ ከአዳም፡ ሰባተኛው፡ *ሄኖክ፡ በለዚህ፡ ትንቢ
ት፡ ተናግሮባቸዋል፡ እንደህ፡ ሲል። እነሆ፡እግዚአብ
ሔር፡ ይመጣል፡ከአእላፍ፡ ቅዱሳን፡ ጋራ።
*ዘፍ፡ ፭፡ ፳፩።

፲፭፤ በሁሉ፡ *ይፈርድ፡ ዘንድ፡ ዓመጸኞችንም፡ ሁ
ሉ፡ ስለ፡ ተጠራጠሩበት፡ ጥረጣሬ፡ ሁሉ፡ ይገሥጽ፡ ዘ
ንድ፡ ኃጢአተኞችም፡ መናፍቃን፡ በተናገሩበት፡ጽኑ፡
ነገር፡ ሁሉ። *ማቴ፡ ፳፭፡ ፴፩።
፲፮፤ እሌህ፡የሚያንጐረጕሩና፡የሚነቀፉ፡ናቸው፡
በመመኞታቸው፡ የሚሔዱ። አፋቸውም፡በትዕቢ
ት፡ ይናገራል። ለሰው፡ ፊትም፡ ያደላሉ፡ ሊረቡ።
፲፯፤ እላንተ፡ ግን፡ ወዳጆቼ፡ከጌታችን፡ ከየሱስ፡ ክ
ርስቶስ፡ሐዋርያት፡ቀድሞ፡የተባለውን፡ነገር፡አስቡ።
፲፰፤ ነግረዋችኋልና፡ እንደህ፡ ሲሉ። *በኋለኛው፡
ዘመን፡ይመጣሉ፡ የሚያፌዙ፡ እንደ፡መመኞታቸው
ም፡ በክሕደት፡ ይሔዳሉ። *፩፡ ጢሞ፡ ፬፡ ፩።
፪፡ ጴጥ፡ ፫፡ ፫።

፲፱፤ እርሳቸው፡የተለዩ፡ ናቸው። የሥጋ፡ወገን፡ መ
ንፈስ፡ የሌለባቸው። ፩፡ ቆሮ፡ ፪፡ ፲፬።
፳፤ እላንተ፡ ግን፡ ወዳጆቼ፡ ሆይ፡እጅግ፡ በተቀደሰ
ች፡ በሃይማኖታችሁ፡ ተሠሩ፡ በመንፈስ፡ ቅዱስም፡
ጸልዩ። ቆላ፡ ፪፡ ፯። ፩፡ ተሰ፡ ፭፡ ፲፩።
፳፩፤ በእግዚአብሔርም፡ ፍቅር፡ ተጠበቁ፡ የጌታ
ችንን፡ የየሱስ፡ ክርስቶስን፡ ምህረት፡ ተስፋ፡ ስታደር
ጉ፡ ለዘላለም፡ ሕይወት።
፳፪፤ እኩሉንም፡ ማሩ፡ ስትለያዩ።
፳፫፤ እኩሉን፡ ግን፡ *በፍርሃት፡ አድንዋቸው፡ ከእ
ሳት፡ ነበልባልም፡ ስትነጥቋቸው፡ ደግሞም፡ ከሥጋ፡
የረከሰችውን፡ †ልብስ፡ ስትጠሉ። *ያዕ፡ ፭፡ ፲፱፡ ፳።
†ራእ፡ ፫፡ ፬።

፳፬፤ ይጠቅቃችሁ፡ ዘንድ፡ ግን፡ ለሚችለው፡ እን
ደትወድቁ፡ በክብሩ፡ ፊትም፡ ያቀማችሁ፡ ዘንድ፡ ያ
ለ፡ ነውር፡ ደስ፡ ብልዋችሁ። ፩፡ ተሰ፡ ፭፡ ፳፫።
ፊል፡ ፩፡ ፲።

፳፭፤ እርሱም፡ አንዲ፡ እግዚአብሔር፡መድኃኒታ
ችን። ለርሱ፡ ምስጋና፡ ይሁን፡ ታላቅነትም፡ ግዛትም፡
ኃይልም፡ ዛሬ፡ እስከ፡ ዘላለምም፡ ድረስ። አሜን።
ሮሜ፡ ፲፮፡ ፳፯። ፩፡ ጢሞ፡ ፩፡ ፲፯።

# የዮሐንስ ፡ ራእይ ።

## ምዕራፍ፡ ፩፤

፩፤ የየሱስ፡ ክርስቶስ፡ ራእይ፡ እግዚአብሔር፡ የሰ
ጠው፡*ፈጥኖ፡ የሚሆነውን፡ ነገር፡ ለባሮቹ፡ ይገልጥ፡
ዘንድ፡ አመለከታትም፡ በመልኩ፡ እጁም፡ ወደ፡ ባር
ያው፡ ወደ፡ ዮሐንስ፡ ላካት። *ቍ፡ ፲፱፡፡
ም፡ ፳፪፡ ፮፡ ፯፡፡
፪፤ ለእግዚአብሔር፡ ቃል፡*የመሰከረ፡ ለየሱስ፡ ክ
ርስቶስም፡ ምስክር፡ ባየው፡ ሁሉ፡ ነገር።
*ቍ፡ ፱፡፡ ም፡ ፮፡ ፱፡፡
፫፤ ምስጋና፡ይገባዋል፡ ለሚያነብ፡ የዚህንም፡ ትን
ቢት፡ ነገር፡ ለሚሰሙ፡ በርሱ፡ የተጻፈውንም፡ ለሚ
ጠብቁ። *ዘመን፡ ቀርብዋልና። *ም፡ ፳፪፡ ፯፡፡
†ም፡ ፳፪፡ ፲፡፡
፬፤ ከዮሐንስ፡ በእስያ፡ ወደሉት፡ ወደ፡ሰባቱ፡ አብ
ያተ፡ ክርስቲያናት። ለላንት፡ጸጋ፡ይሁንላችሁ፡ሰላም
ም፡ *ከያለው፡ከነበረውም፡ ከሚመጣውም። በዙ
ፋኑ፡ ፊት፡ ካሉም፡ *ከሰባቱ፡ መናፍስት።
*ዘፀአ፡ ፫፡ ፲፬፡ ፲፭፡፡ ዕብ፡ ፲፫፡ ፰፡፡ †ም፡ ፫፡ ፩፡፡
ኢሳ፡ ፲፩፡ ፪፡፡
፭፤ ከየሱስ፡ ክርስቶስም፡ ከታመነው፡ *ምስክር።
የሙታን፡ †በኵር፡ የምድር፡ ነገሥታትም፡ አለቃ።
**ለወደደን፡ ከኃጢአታችንም፡ በደሙ፡ ††ላጸበን።
*ም፡ ፫፡ ፲፬፡፡ ዮሐ፡ ፲፰፡ ፴፯፡፡ †ቍ፡ ፲፰፡፡
ቆላ፡ ፩፡ ፲፰፡፡ **ም፡ ፲፱፡ ፲፮፡፡ ††ም፡ ፯፡ ፲፬፡፡
ዕብ፡ ፱፡ ፲፬፡፡
፮፤ ነገሥታትና፡ ካህናት፡ *ያደረገን፡ ላባቱ፡ ለእግዚ
አብሔር። †ለርሱ፡ ክብር፡ይሁን፡ ቸሉትም፡ ከዘላለ
ም፡ እስከ፡ ዘላለም፡ ድረስ፡ አሜን። *ም፡ ፭፡ ፲፡፡
፩፡ ጴጥ፡ ፪፡ ፭—፱፡፡ †ዘፀአ፡ ፲፱፡ ፮፡፡
፯፤ እነሆ፡ እርሱ፡ በደመና፡ ይመጣል፡ዓይንም፡ ሁ
ሉ፡ *ታየዋለች፡የወጉትም፡ደግሞ፡የምድርም፡ነገድ፡
ሁሉ፡ያለቅሱለታል። አዎን። አሜን።
*ዘካ፡ ፲፪፡ ፲፡፡ ዮሐ፡ ፲፱፡ ፴፯፡፡
፰፤ እኔ፡ ነኝ፡ አልፋና፡ ዖሜጋ። መጀመርያ፡ መጨ
ረሻም፡ እግዚአብሔር፡ ይላል፡ ያለ፡ የነበረም፡ የሚ
መጣም፡ ሁሉን፡ ቻይ። ም፡ ፳፪፡ ፲፫፡፡ ኢሳ፡ ፵፩፡ ፬፡፡
ና፡ ፵፬፡ ፮፡፡ ና፡ ፵፰፡ ፲፪፡፡
፱፤ እኔ፡ ዮሐንስ፡ወንድማችሁ፡በኃዘንም፡ደግሞ፡
*ባልንጀራችሁ፡ በመንግሥትም፡ በየሱስ፡ ክርስቶስ
ም፡ ትዕግሥት፡ ጽጥሞ፡ በምትባል፡ ደሴት፡ ነበርሁ፡
ስለ፡ እግዚአብሔር፡ ቃል፡ ስለ፡ የሱስ፡ ክርስቶስም፡
ምስክር። *ሮሚ፡ ፰፡ ፲፯፡፡
፲፤ በመንፈስም፡ ሆንሁ፡ በጌታ፡ ቀን። በኋላዬም፡
ታላቅ፡ ድምጽ፡ ሰማሁ፡ እንደ፡ መለከት፡ ያለ።
ቍ፡ ፲፭፡፡

፲፩፤ እንደሁ፡ ሲል። እኔ፡ ነኝ፡ አልፋ፡ ዖሜጋ፡ የፊ
ተኛው፡ የኋለኛውም። የምታየውንም፡ በመጽሐ
ፍ፡ ጻፈው፡ በእስያ፡ ወደሉት፡ ሰባቱ፡ አብያተ፡ ክርስ
ቲያናትም፡ ስደደው። ወደ፡ ኤፌሶን። ወደ፡ ስሚር
ናም። ወደ፡ ጴርጋሞስም። ወደ፡ ቲያቲራም። ወደ፡
ሰርዴስም። ወደ፡ፊላድልፊያም፡ ወደ፡ላዶቅያም።
*ም፡ ፳፪፡ ፲፫፡፡
፲፪፤ የሚናገረኝንም፡ ድምጽ፡ አይ፡ ዘንድ፡ተመለ
ስሁ። በተመለስሁም፡ ጊዜ፡ሰባት፡ የወርቅ፡ መቅረዞ
ች፡ አየሁ።
፲፫፤ በሰባቱም፡ መቅረዝ፡ *መካከል፡ አንድ፡ †የሰ
ው፡ ልጅ፡ የሚመስል፡ ነበረ፡ ልብስ፡ ለብሶ፡ እስከ፡ግር
ቹ፡ በደረቱም፡ በወርቅ፡ መታጠቅያ፡ የታጠቀ።
*ም፡ ፪፡ ፩፡፡ †ዳን፡ ፯፡ ፲፫፡፡
፲፬፤ ራሱ፡ ግን፡ጸጕሩም፡እንደ፡ *ነጭ፡የበግ፡ጸጕር፡
ነበር። እንደ፡ ባዘቶ፡ የነጻ። †ዓይኖቹም፡ እንደ፡ እሳ
ት፡ ነበልባል። *ዳን፡ ፯፡ ፱፡፡ †ም፡ ፪፡ ፲፰፡፡
፲፭፤ እግሮቹም፡ እንደ፡ ሊባኖስ፡ *ብረት፡ በእቶን፡
እንደ፡ ጋሉ። ድምጹም፡ እንደ፡ ብዙ፡ ውኆች፡ ድ
ምጽ። *ም፡ ፪፡ ፲፰፡፡
፲፮፤ በቀኝ፡ እጁም፡ *ሰባት፡ ከዋክብት፡ ነበር። ካ
ፉም፡ ይወጣ፡ ነበረ፡ ሁለት፡ ልሳን፡ ያለው፡ †የተሳለ፡
ሰይፍ፡ ፊቱም፡ ያበራል፡ እንደ፡ ጸሓይ፡ በኃይልዋ።
*ቍ፡ ፳፡፡ ም፡ ፪፡ ፩፡፡ †ም፡ ፪፡ ፲፪፡ ፲፮፡፡ ና፡ ፲፱፡ ፲፭፡፡
፲፯፤ ባየሁትም፡ ጊዜ፡ በግሩ፡ ወደቅሁ፡ እንደ፡ ሞ
ተ። በላዬም፡ ቀኝ፡ እጁን፡ ጫነብኝ፡ እንደሁ፡ ሲል።
አትፍራ፡ እኔ፡ ነኝ፡ የፊተኛው፡ የኋለኛውም።
ዳን፡ ፰፡ ፲፰፡፡
፲፰፤ ሕያውም፡ ሙቼም፡ ነበርሁ። እነሆም፡ ሕያ
ው፡ ነኝ፡ ለዘላለሙ። አሜን። የሲኦልና፡ የሞት፡ መ
ክፈቻም፡ ከኔ፡ ጋራ፡ ነው። ሮሚ፡ ፮፡ ፱፡፡
፲፱፤ ያየኸውን፡ *ጻፍ፡ የሚሆነውንም፡ከዚህም፡
ተበኋላ፡ ይሆን፡ ዘንድ፡ ያለውን። *ም፡ ፲፬፡ ፲፫፡፡
†ም፡ ፬፡ ፩፡፡
፳፤ በቀኜ፡ ያየሃት፡ የሰባቱ፡ ከዋክብት፡ ምሥጢ
ር፡ የሰባቱም፡ የወርቅ፡ መቅረዞች። ሰባቱ፡ ከዋክብ
ት፡ የሰባቱም፡ የወርቅ፡ መቅረዞች። ሰባቱ፡ ከዋክብ
ት፡ የሰባቱ፡ አብያተ፡ ክርስቲያናት፡ መላእክት፡ ናቸ
ው። ያየሃቸውም፡ ሰባቱ፡ መቅረዞች፡ ሰባት፡ አብያ
ተ፡ ክርስቲያናት፡ ናቸው። መልክ፡ ፪፡ ፯፡፡

## ምዕራፍ፡ ፪፤

፩፤ ወደ፡ ኤፌሶን፡ቤተ፡ክርስቲያን፡መልአክ፡ጻፍ።
እንደሁ፡ይላል፡በቀኙ፡ *ሰባት፡ ከዋክብት፡ የያዘው።
በሰባቱ፡ በወርቅ፡ መቅረዞች፡ መካከል፡ የሚሔድ።
*ም፡ ፩፡ ፲፫፡፡ ፲፮፡ ፳፡፡

፪፤ ሥራህን፡ አወቅሁ፡ ድካምህንም፡ ትዕግሥትህ
ንም። ክፉችንም፡ ትታገሣቸው፡ዘንድ፡እንደትችል፡
*ፈትነሃቸዋልና፡ ሐዋርያት፡ ነን፡ የሚሉን፡ እንደሁ
ም፡ አይደሉም፡ አስተኞችም፡ ሆነው፡ አገኘሃቸው።
*፩፡ዮሐ፡ ፬፡ ፪፡ ፫።

፫፤ ቻልህም፡ ትዕግሥትም፡አለህ።ስለ፡ስሜም፡ደ
ከምህ፡ አልሰለቸህምም። ገላ፡ ፮፡ ፱።
ዕብ፡ ፲፪፡ ፭፡ ፲፪፡ ፲፭።

፬፤ ነገር፡ ግን፡ ጥቂት፡አግኝቼብሃለሁ፡የቀደመዪቱ
ን፡ ፍቅርህን፡ ትተሃልና። ም፡ ፫፡ ፫፡ ፲፱።

፭፤ አሁንም፡ ከወደት፡ወደቅህ፡አስብ፡ንስሐም፡
ግባ፡ የቀደመውንም፡ ሥራ፡ ሥራ። ያለዚያ፡ እኔ፡ ፈጥ
ኜ፡እመጣብሃለሁ፡ መቅረዝህንም፡ ከስፍራዋ፡አስ
ወግደታለሁ፡ ንስሐ፡ ባትገባ።

፮፤ ነገር፡ ግን፡ ይህ፡ አለህ። እርሱም፡ *የኒቆላውያ
ንን፡ ሥራ፡ ተጸልተሃልና፡ እኔ፡ ደግሞ፡ የምጸላትን።
*ቍ፡ ፲፭። †መዝ፡ ፻፴፱፡ ፳፩።

፯፤ ጆሮ፡ ያለው፡ ይስማ፡ መንፈስ፡ ለአብያተ፡ ክር
ስቲያናት፡የሚለውን። ድል፡ ለነሣው፡ እኔ፡ እሰጠዋ
ለሁ፡ ይበላ፡ ዘንድ፡ በእግዚአብሔር፡ ገነት፡ ውሥጥ፡
ካለው፡ †ከሕይወት፡ ዛፍ። *ቍ፡ ፲፩፡ ፲፯፡ ፳፮።
ም፡ ፫፡ ፭፡ ፲፪፡ ፳፩። †ም፡ ፳፪፡ ፪። ዘፍ.ጥ፡ ፪፡ ፱።

፰፤ ለሰሚርና፡ ቤት፡ክርስቲያንም፡መልአክ፡ጻፍ።
ይህ፡ ነው፡የሚለው፡የፊተኛው፡የኋለኛውም። ሙ
ተ፡ የነበረው፡ ሕያውም፡ የሆነው። *ም፡ ፩፡ ፲፯።
ፍ፡ ፳፪፡ ፲፫።

፱፤ ሥራህን፡ አውቃለሁ፡ አዘንህንም፡ ድኅነትህን
ም። (ነገር፡ ግን፡ አንተ፡ *ባለጠጋ፡ ነህ፡) †አይሁድ፡ ነን፡
የሚሉትንም፡ ስድብ፡ አወቅሁ፡ እርሳቸውም፡ አይ
ደሉም፡ **የሰይጣን፡ ማኅበር፡ ናቸው፡ እንጂ።
*ያዕ፡ ፪፡ ፭። ም፡ ፫፡ ፱። **፪፡ ቆሮ፡ ፲፩፡ ፲፬፡ ፲፭።

፲፤ ያገኝህ፡ ዘንድ፡ ካለው፡ሁሉ፡ መከራ፡ አትፍራ።
እነሆ፡ ሰይጣን፡ ከላንት፡ ወገን፡በግዞት፡ያኖር፡ ዘንድ፡
ጊዜ፡ አለው፡ ትፈተኑ፡ ዘንድ። አዘንም፡ ይደርስባች
ኋል፡ አሥር፡ ቀን፡ እስከ፡ ሞት፡ድረስ፡ የታመንህ፡ ሁ
ን። እኔም፡ የሕይወት፡ *አክሊል፡ እሰጥሃለሁ።
*ማቴ፡ ፲፡ ፳፪። ፪፡ ጢሞ፡ ፬፡ ፰።

፲፩፤ ጆሮ፡ ያለውን፡ይስማ፡መንፈስ፡ ለአብያተ፡ ክ
ርስቲያናት፡የሚለውን። ድል፡ የነሣ፡ ከሁለተኛዪቱ፡
ሞት፡ አይጐዳም። ም፡ ፳፡ ፲፬።

፲፪፤ ለጴርጋሞስም፡ ቤት፡ክርስቲያን፡ መልአክ፡ ጻ
ፍ፡ ሁለት፡ ልሳን፡ ያለው፡ የተሳለ፡ ሰይፍ፡ በእጁ፡ ያለ
ው፡ የሚለው፡ ይህ፡ ነው። ም፡ ፩፡ ፲፮።

፲፫፤ እኔ፡ሥራህን፡አውቃለሁ፡ወደትስ፡ትኖራለህ።
*የሰይጣን፡ ዙፋን፡ ወደለበት። አንትም፡ †ስሜን፡
ይዘሃል፡ ሃይማኖቴንም፡ አልካድህም፡ ደግሞም፡ የ
ታመነ፡ ምስክሬ፡ አንቲጳስ፡ በነበረባት፡ ቀን፡ በላንት፡
ዘንድ፡ የገደሉት፡ ሰይጣን፡ ባለበት፡ ዘንድ።
*ም፡ ፲፫፡ ፪። †ም፡ ፫፡ ፰።

፲፬፤ ነገር፡ ግን፡ ጥቂት፡ ለኔ፡ አለኝ፡ በላይህ። ላንት፡
ከዚያ፡ ሰዎች፡ አሉልህና፡ *በበለዓም፡ ትምህርት፡ የ
ተያዙ፡ ባላቅን፡ያስተምር፡የነበረ፡ በእሥራኤል፡ልጆ
ች፡ ፊት፡ መሰናክያ፡ለመጣል፡ለጣዖታት፡የታረደው
ን፡ ይበሉ፡ ዘንድ፡ ያመነዝሩም፡ ዘንድ።
*ዘኍል፡ ፴፩፡ ፲፮። ይሁድ፡ ፲፩።

፲፭፤ እንደሁም፡ ላንት፡ ሰዎች፡ አሉህ፡ በኒቆላው
ያን፡ ትምህርት፡ የተያዙ፡ እኔ፡ የምጸላው።
ቍ፡ ፮።

፲፮፤ ንስሐ፡ ግባ። ያለዚያ፡ እኔ፡ ፈጥኜ፡ እመጣብ
ሃለሁ፡ ባፉ፡ *ሰይፍም፡ እጣላቸዋለሁ።
*ም፡ ፩፡ ፲፮። ፍ፡ ፲፱፡ ፲፭፡ ፳፩።

፲፯፤ ጆሮ፡ ያለው፡ ይስማ፡ መንፈስ፡ ለአብያተ፡ ክ
ርስቲያናት፡ የሚለውን። ድል፡ ለነሣ፡ እሰጠዋለሁ፡
ከተሰወረው፡ መና፡ ይበላ፡ ዘንድ። ነጭ፡ ደንጊያም፡
እሰጠዋለሁ። በደንጊያውም፡ ላይ፡ አዲስ፡ ስም፡ ተ
ጽፎበታል፡ ማንም፡ የማያውቀው፡ ከተሰጠው፡ በ
ቀር። ም፡ ፫፡ ፲፪።

፲፰፤ለቲያቲራም፡ቤት፡ክርስቲያን፡መልአክ፡ጻፍ።
ይህ፡ ነው፡ የእግዚአብሔር፡ ልጅ፡ ያለው። እንደ፡ እ
ሳት፡ ነበልባል፡ ያሉ፡ *ዓይኖች፡ ያሉት፡ እግሮቹም፡ እ
ንደ፡ ሊባኖስ፡ ብረት። *ም፡ ፩፡ ፲፬። ፍ፡ ፲፱፡ ፲፪።

፲፱፤ ሥራህን፡ አወቅሁ፡ ፍቅርህንም፡ መገዛትህን
ም፡ ሃይማኖትህንም፡ትዕግሥትህንም፡ማድረግህን
ም። የኋለኛዪቱም፡ ከፊተኛዪቱ፡ እንድትበልጥ።

፳፤ ነገር፡ ግን፡ ጥቂት፡ አግኝቼብሃለሁ። ያችን፡ ቤ
ት፡ *ኢሳቤልን፡ትተሃልና፡ነቢይት፡ነኝ፡የምትለውን።
ታስተምር፡ ዘንድ፡ ባሮቼንም፡ታስታቸው፡ ዘንድ፡እን
ደ፡ያመነዝሩ፡ለጣዖታትም፡ የታረደውን፡እንዲበሉ፡
ቍ፡ ፬። *፩፡ ነገሥ፡ ፲፮፡ ፴፩።

፳፩፤ ጊዜም፡ ሰጠኋት፡ ንስሐ፡ ትገባበት፡ ዘንድ፡ አ
ልገባችም።

፳፪፤ እነሆ፡ እኔ፡ ባልጋ፡ ላይ፡ እጥላታለሁ፡ ከርስዋ
ም፡ ጋራ፡ የሚያመነዝሩን፡ በታላቅ፡ አዘን፡ ከሥራቸ
ው፡ ባይመለሱ።

፳፫፤ ልጆችዋንም፡በሞት፡ እገላለሁ። ቤት፡ ክርስ
ቲያኒቱም፡ሁሉ፡ ታውቃለች፡ እኔ፡ እንደ፡ሆንሁ፡ †ኩ
ላሊትንና፡ ልብን፡ የምመረምር። ከላንትም፡ ለሁላ
ችሁ፡እንደ፡ ሥራችሁ፡ እከፍላችኋለሁ።
*መዝ፡ ፯፡ ፲። ኤር፡ ፲፯፡ ፲።

፳፬፤ ለላንት፡ ግን፡ እላለሁ፡ ለቀሩትም፡ በቲያቲ
ራ፡ ላሉት። ይህ፡ ትምህርት፡ ከርሳቸው፡ዘንድ፡ የሌ
ለውን፡ ሁሉ፡ የሰይጣንንም፡ ጥልቅ፡ የማያውቁን፡
ሁሉ። እርሳቸው፡ እንደ፡ናገሩ። ሌላ፡ የከበደ፡ ነገር፡
አልጭንባችሁም።

፳፭፤ ነገር፡ ግን፡ ከላንት፡ጋራ፡ ባለው፡ ተያዙ፡እስክ
መጣ፡ ድረስ። ም፡ ፫፡ ፲፩።

፳፮፤ ድል፡ የነሣውም፡ሥራዬንም፡ እስከ፡ ፍጻሜ፡
የሚጠብቅ፡ሥልጣን፡እሰጠዋለሁ፡በአሕዛብ፡ላይ።

፳፯፡ በብረት፡ በትርም፡ ይጠብቃቸዋል፡ እንደ፡ ሸክላም፡ እቃ፡ ይቀጠቀጣሉ። ም፡ ፲፪፡ ፭።

፳፰፡ እኔ፡ ደግሞ፡ ካባቴ፡ እንደ፡ወሰድሁ። የንጋትን፡ ኮከብ፡ እሰጠዋለሁ። መዝ፡ ፪፡ ፰።

፳፱፡ ጆሮ፡ ያለው፡ ይስማ፡ መንፈስ፡ የአብያተ፡ ክርስቲያናት፡ የሚለውን። ም፡ ፫፡ ፮።

## ምዕራፍ፡ ፫፡

፩፡ በሰርዲስ፡ላለችውም፡ ቤተ፡ ክርስቲያን፡ መልአክ፡ ጻፍ። ይህ፡ ነው፡ የሚለው፡ *ሰባቱ፡ የእግዚአብሔር፡ መናፍስት፡ ከርሱ፡ ጋራ፡ ያሉት፡ †ሰባትም፡ ከዋክብት። ስራህን፡ አወቅሁ፡ ስም፡እንዳለህ፡ሕያው፡ እንደ፡ ሆንህ፡ አንተ፡ የሞትህ፡ ስትሆን። *ም፡ ፭፡ ፮። †ም፡ ፩፡ ፲፮።

፪፡ *የነቃህ፡ ሁን፡ ይሞቱ፡ ዘንድ፡ ያላቸውንም፡ የቀሩትን፡ †አጽና፡ ስራህን፡ መልታ፡ አላገኘሁምና፡ በእግዚአብሔር፡ ፊት። *ቈ፡ ፲፱። †ሕዝ፡ ፴፬፡ ፬።

፫፡ አሁንም፡ አስብ፡ እንዴት፡ ተቀበልህ፡ እንዴትስ፡ ሰማህ፡ ጠብቅም፡ ንስሐም፡ ግባ። ባተጋም፡ እኔ፡ *እመጣብሃለሁ፡ እንደ፡ሌባ። የምመጣብህንም፡ ሰዓት፡ አታውቅም። ፩፡ ተሰ፡ ፭፡ ፪።

፬፡ ነገር፡ ግን፡ ጥቂት፡ ስሞች፡ አሉህ፡በሰርዲስ፡ደግሞ፡ ልብሳቸውን፡ ያላረከሱ። ከኔ፡ ጋራም፡ ነጭ፡ ለብሰው፡ ይሔዳሉ፡ ይገባቸዋልና። ይሁዳ፡ ፳፫።

፭፡ ድል፡የነሣ፡ይህ፡*ነጭ፡ልብስ፡ይለብሳል። ስሙንም፡ †ከሕይወት፡ መጽሐፍ፡ አላጠፋውም፡ ስሙንም፡ **አምንበታለሁ፡ ባባቴ፡ ፊት፡በመላእክቱም። *ም፡ ፬፡ ፬። ና፡ ፮፡ ፲፩። ፯፡ ፱። †ፊል፡ ፬፡ ፫። **ማቴ፡ ፲፡ ፴፪።

፮፡ ጆሮ፡ ያለው፡ ይስማ፡ መንፈስ፡ ለአብያተ፡ ክርስቲያናት፡ የሚለውን።

፯፡ በፊላድልፊያም፡ ላለችው፡ ቤተ፡ ክርስቲያን፡ መልአክ፡ ጻፍ። ይህ፡ ነው፡ የሚለው፡ ቅዱሱ፡ እውነተኛው፡ *የዳዊት፡መክፈቻ፡ያለው። የሚከፍት፡ማንም፡የማይዘጋ። የሚዘጋም፡ማንም፡የማይከፍት። *ኢሳ፡ ፳፪፡ ፳፪።

፰፡ ስራህን፡ አወቅሁ። እነሆ፡ *የተከፈተ፡ደጅ፡ በፊትህ፡ አደረግሁ፡ ማንም፡ ይቈልፈው፡ ዘንድ፡ አይችልም፡ ጥቂት፡ ኃይል፡ አለህና፡ ቃሌንም፡ ጠበቅህ፡ ስሜንም፡ አልካድህም። *፩፡ ቆሮ፡ ፲፮፡ ፱።

፱፡ እነሆ፡እሰጥሃለሁ፡ ከሰይጣን፡ ማኅበር፡ ያሉትን፡ *አይሁድ፡ ነን፡ የሚሉን፡ እርሳቸውም፡ ያይደሉ። ነገር፡ግን፡ አሰት፡ይናገራሉ። እነሆ፡†አደርጋቸዋለሁ፡ መጥተው፡ ከግርህ፡ በታች፡ ይሰግዱ፡ ዘንድ። እኔም፡ እንደ፡ ወደድሁህ፡ ያውቃሉ። †ም፡ ፪፡ ፱። ኢሳ፡ ፵፱፡ ፳፫። ና፡ ፳፡ ፲፬።

፲፡ የትዕግሥቴን፡ *ቃል፡ ጠብቀሃልና፡ እኔም፡ ከፈተና፡ ጊዜ፡ የጠብቅሃለሁ፡ በዓለሙ፡ ሁሉ፡ ትመጣ፡ ዘንድ፡ ካላት፡ በምድር፡ ላይ፡ የሚኖሩት፡ ይፈትኑ፡ ዘንድ። *ም፡ ፲፫፡ ፲። ዕብ፡ ፲፡ ፴፪።

፲፩፡ እነሆ፡ፈጥኜ፡እመጣለሁ። የያዝህውን፡ጠብቅ። ማንምም፡ አክሊልህን፡ እንዳይወስድብህ። ም፡ ፩፡ ፫። ፪፡ ፭፡ ፲።

፲፪፡ ድል፡ የነሣውን፡ *ዓምድ፡ አደርገዋለሁ፡ ባምላኬ፡ መቅደስ። ወደ፡ ሜደም፡ ደግሞ፡ አይወጣም። ያባቴንም፡ †ስም፡ እጽፍበታለሁ፡ ያምላኬንም፡ አገር፡ስም። እርሱዋም፡ አዲሲቱ፡ የሩሳሌም፡ከሰማይ፡ የምትወርድ፡ **ከአምላኬ፡ ዘንድ። አዲሱንም፡ ስሜን፡ እጽፍበታለሁ። *ገላት፡ ፪፡ ፱። †ም፡ ፲፬፡ ፩። ፳፪፡ ፬። **ም፡ ፲፱፡ ፲፪። ና፡ ፳፩፡ ፪።

፲፫፡ ጆሮ፡ያለው፡ ይስማ፡መንፈስ፡ ለአብያተ፡ ክርስቲያናት፡ ምን፡ አለ።

፲፬፡ ለላዶቅያም፡ ቤተ፡ ክርስቲያን፡ መልአክ፡ ጻፍ። ይህ፡ነው፡ያለው፡*አሜን፡የሚሆን። የታመነው፡ ምስክር፡ እውነተኛውም። የእግዚአብሔር፡ ፍጥረት፡ †መጀመርያ። *ም፡ ፩፡ ፭። †ዮሐ፡ ፩፡ ፫። ቆላ፡ ፩፡ ፲፭።

፲፭፡ ስራህን፡ አወቅሁ፡ ብርድ፡ ትኩስም፡ እንዳይደለህ፡ምነው፡ ብርድ፡ በሆንህ፡ ወይስ፡ ትኩስ። ም፡ ፪፡ ፪፡ ፱።

፲፮፡ ነገር፡ግን፡ለብ፡ ያልህ፡ነህና፡ የበረድህ፡ ያይደለህ፡ የተኩስህም። እኔ፡ ካፌ፡ እተፋህ፡ ዘንድ፡ አለኝ።

፲፯፡ ትላለህና፡ ባለ፡ ጠጋ፡ ነኝ፡ እጅግም፡ *መልቻለሁ፡ከማንም፡ አልሻም። ከቶም፡ አታውቅም፡ ጉስቋላ፡እንደሆንህ፡ምስኪንም፡ድኻም፡ ዕውርም፡ ዕራቁትህም፡ እንደሆንህ። *፩፡ ቆሮ፡ ፫፡ ፲፰። ና፡ ፬፡ ፰።

፲፰፡ እኔ፡ እመክርሃለሁ፡ በእሳት፡ የተፈተነውን፡ *ወርቅ፡ ከኔ፡ ትገዛ፡ ዘንድ፡ ባለ፡ ጠጋ፡ ትሆን፡ ዘንድ። ነጭ፡ልብስም፡ ትለብሳት፡ዘንድ፡ †የራቁትህም፡ ኃፍረት፡እንዳትገለጥ። ዓይንህንም፡በኩል፡ ተኳል፡ እንድታይ። *ኢሳ፡ ፶፭፡ ፩። መልክ፡ ፫፡ ፫። †ራእ፡ ፲፮፡ ፲፭።

፲፱፡ እኔ፡የምወደውን፡ሁሉ፡እዘልፈዋለሁ፡እገሥጻውማለሁ። አሁንም፡ ቅና፡ ንስሐም፡ ግባ። ምሳ፡ ፫፡ ፲፪። ፩፡ ቆሮ፡ ፲፩፡ ፴፪። ዕብ፡ ፲፪፡ ፮።

፳፡ እነሆ፡እኔ፡ *በደጅ፡ ቁሚያለሁ፡ ደጅም፡ እመታለሁ። ማንም፡ድምጼን፡ ቢከፍትልኝም፡ ወደርሱ፡ †እገባለሁ። ከርሱም፡ ጋራ፡ እራቴን፡ እበላለሁ፡ እርሱም፡ከኔ፡ጋራ። *ሉቃ፡ ፲፪፡ ፴፮። †ዮሐ፡ ፲፬፡ ፳፫።

፳፩፡ ድል፡ለነሣው፡እሰጠዋለሁ፡ከኔ፡ጋራ፡ ይቀመጥ፡ዘንድ፡ በዙፋኔ፡ላይ። እኔ፡ ደግሞ፡ ድል፡እንደ፡ ነሣሁ፡ካባቴም፡ ጋራ፡ እንደ፡ ተቀመጥሁ፡ በዙፋኑ፡ላይ። ማቴ፡ ፲፱፡ ፳፰።

፳፪፡ ጆሮ፡ያለው፡ ይስማ፡ መንፈስ፡ ለአብያተ፡ ክርስቲያናት፡ ምን፡አለ።

## ምዕራፍ፡ ፬፡

፩፡ ከዚያ፡ወዲያም፡ አየሁ፡ በሰማይም፡ እነሆ፡ደጅ፡ ተከፈተ። የፊተኛውም፡ ድምጽ፡ እንደ፡ መለከት፡ ድምጽ፡ የሰማሁት፡ ተናገረኝ፡ እንደዚህ፡ ሲል። ወደዚህ፡ውጣ፡ ከዚህም፡ በኋላ፡ይሆን፡ ዘንድ፡ ያለውን፡ አሳይሃለሁ።

ም፡ ፩፡ ፲።

፪፡ የዚያን፡ ጊዜውም፡ በመንፈስ፡ ነበርሁ። እነሆም፡ *ዙፋን፡ በሰማይ፡ ቈምዋል።

*ሕዝ፡ ፩፡ ፳፮። ሕዝ፡ ፲፡ ፩። ኢሳ፡ ፮፡ ፩።

፫፡ በዙፋኑም፡ላይ፡ተቀማጭ፡የተቀመጠበትም፡ በማየት፡የኢያስጲድን፡ደንጊያ፡ መሰለ፡ ሰርዲኖስንም፡የደመና፡ ቀስትም፡ በዙፋኑ፡ ዙርያ፡ ነበረ፡ በማየት፡የመረግድን፡ደንጊያ፡የሚመስል። ሕዝ፡ ፩፡ ፳፰።

፬፡ በዙፋን፡ዙርያም፡ሀያ፡አራት፡ ዙፋኖች፡ ነበሩ። በዙፋኖችም፡ ላይ፡ ሀያ፡አራት፡ *ሽማግሌዎች፡ ተቀምጠው፡ ነጭ፡ ልብስንም፡ ለብሰው፡ አየሁ፡ በራሳቸውም፡ላይ፡የወርቅ፡ አክሊል፡ ነበረ።

*ኢሳ፡ ፳፬፡ ፳፫። ም፡ ፫፡ ፬። ፍ፡ ፭፡ ፲።

፭፡ ከዙፋኑም፡ ወጣ፡*መብረቅ፡ ነጐድጓድም፡ድምጽም። ሰባትም፡የሳት፡መብራቶች፡ በዙፋኑ፡ ፊት፡ የተቃጠሉ። እርሳቸውም፡ የእግዚአብሔር፡ ሰባት፡ መናፍስት፡ናቸው።

*ም፡ ፰፡ ፭። ፲፩፡ ፲፱። ፲፮፡ ፲፰። †ዘካ፡ ፬፡ ፪፡ ፲።

፮፡ በዙፋኑም፡ፊት፡ *የብርጭቆ፡ ባሕር፡ ቢረሌን፡ የሚመስል፡ ነበረ። በዙፋኑም፡ ውሥጥ፡ በዙፋኑም፡ ዙርያ፡አራት፡ እንስሶች፡ ነበሩ፡ ዓይን፡ የመላባቸው፡ በፊትና፡በኋላ። *ዘፀአ፡ ፳፬፡ ፲። ሕዝ፡ ፩፡ ፭፡ ፳፪።

፯፡ የፊተኛውም፡ እንስሳ፡ አንበሳውን፡ መሰለ። ሁለተኛውም፡ እንስሳ፡ ጥጃውን፡ መሰለ። ሦስተኛውም፡እንስሳ፡ፊት፡ ነበረለት፡እንደ፡ ሰው። አራተኛውም፡ እንስሳ፡ የሚበረውን፡ ንስር፡ መሰለ።

ሕዝ፡ ፩፡ ፲። ፍ፡ ፲፡ ፲፬።

፰፡ አራት ፡ እንስሶችም ፡ ለያንዳንዱ፡ በዙርያቸው፡ ስድስት፡ ክንፎች፡ ነበሩላቸው። በውሥጣቸውም፡ዓይን፡መልተባቸዋል፡ዕረፍትም፡አልነበረላቸውም፡ሌትና፡ቀን፡እንደዚህ፡ሲሉ።ቅዱስ፡ቅዱስ፡ቅዱስ፡እግዚአብሔር፡አምላክ፡ሁሉን፡የያዘ። የነበረና፡ያለ፡የሚመጣም። ኢሳ፡ ፮፡ ፫።

፱፡ እንስሶችም፡ ክብር፡ ገናንነትም፡ ምስጋናም፡ በሰጡ፡ጊዜ፡በዙፋን፡ላይ፡ ለተቀመጠ፡ ለዘላለሙ፡ ሕያው፡ ሁና፡ለሚኖር።

፲፡ ሀያ፡አራቱ፡ሽማግሌዎች፡በዙፋን፡ላይ፡ በተቀመጠው፡ፊት፡ይወድቃሉ፡ ለዘላለሙም፡ ሕያው፡ ሁና፡ ለሚኖር፡ ይሰግዳሉ፡ አክሊላቸውንም፡ በዙፋኑ፡ ፊት፡ ይጥላሉ፡እንደዚህ፡ ሲሉ። ም፡ ፭፡ ፲፬።

፲፩፡ ላንተ፡ ይገባል፡ ጌታ፡ ሆይ፡ምስጋና፡ ክብርም፡ ችሎትም፡ተቀበል፡ዘንድ።አንተ፡ ሁሉን፡ፈጥረሃልና፡ ሁሉም፡ በፈቃድህ፡ ሁንዋልና፡ ተፈጠረም።

## ምዕራፍ፡ ፭፡

፩፡ *በዙፋን፡ላይ፡ በተቀመጠውም፡ በቀኙ፡ መጽሐፍ፡አየሁ፡ በውሥጥና፡በሚደ፡ †የተጻፈበት፡ በሰባት፡ ማሕተም፡ የታተመ። *ም፡ ፬፡ ፪።

†ሕዝ፡ ፪፡ ፱፡ ፲።

፪፡ ብርቱም፡ መልአክ፡ አየሁ፡ በታላቅ፡ ቃል፡ ሲጸራ። ማነው፡ የሚገባው፡ መጽሐፉን፡ ይከፍት፡ ዘንድ፡ማሕተሙንስ፡ ይፈታ፡ ዘንድ።

፫፡ ለማንም፡አልተቻለውም፡በሰማይ፡ ላለ፡ በምድርም፡ላለ፡ ከምድር፡ በታችም፡ ላለ፡ መጽሐፉን፡ይከፍት፡ ዘንድ፡ ያየውም፡ ዘንድ።

፬፡ እኔም፡እጅግ፡ አለቅስ፡ ነበርሁ፡ አንድ፡ የሚገባው፡አልተገኘምና፡ መጽሐፉን፡ ገልጦ፡ የሚያነበው፡ የሚያየውም።

፭፡ ከሽማግሌዎቹም፡ አንዱ፡ አለኝ። አታልቅስ። እነሆ፡ አንበሳው፡ *ከይሁዳ፡ ወገን፡ †የዳዊት፡ ሥር፡ አሸነፈ፡መጽሐፉን፡ ይከፍት፡ ዘንድ፡ ሰባቱንም፡ ማሕተም፡ይፈታ፡ ዘንድ። *ዘፍ፡ ፵፱፡ ፱፡ ፲።

†ኢሳ፡ ፲፩፡ ፩። ራእ፡ ፳፪፡ ፮።

፮፡ በዙፋኑና፡ ባራቱ፡ እንስሶች፡ መካከልም፡ በሀያ፡ አራቱም፡ ሽማግሌዎች፡ መካከል፡*በግ፡ አየሁ፡እንደ፡ ታረደ፡ ሰባት፡ ቀንዶችም፡ ነበሩት፡ ሰባት፡ ዓይኖችም። እርሳቸውም፡ †ሰባቱ፡ የእግዚአብሔር፡ መናፍስት፡ናቸው፡በምድር፡ሁሉ፡የተላኩ። *ኢሳ፡ ፶፫፡ ፯።

ዮሐ፡ ፩፡ ፳፱፡ ፴፮። ዘካ፡ ፬፡ ፲።

፯፡ መጣም፡ መጽሐፉንም፡ ወሰደው፡ ብዙፋን፡ ላይ፡ከተቀመጠው፡ከቀኙ።

፰፡ መጽሐፉንም፡በተቀበለ፡ጊዜ፡ አራቱ፡ እንስሶች፡ሀያ፡አራቱም፡ ሽማግሌዎች፡ በበጉ፡ፊት፡ወደቁ። ከሁሉ፡ ጋራም፡ ኢያንዳንዱ፡ *መሰንቀ፡ ነበራቸው። የወርቅም፡ ጽና፡ ዕጣን፡ የመላባት። እርሱዋም፡ †የቅዱሳን፡ ጸሎት። *ም፡ ፲፬፡ ፪። ፍ፡ ፲፭፡ ፪።

**ም፡ ፰፡ ፫፡ ፬።

፱፡ አዲስ፡ ምስጋናም፡ ያመሰግኑ፡ ነበር፡ እንደዚህ፡ ሲሉ። ላንተ፡ ይገባል፡ መጽሐፉን፡ ትወስድ፡ ዘንድ፡ ማሕተሙንም፡ ትፈታ፡ ዘንድ። ታርደሃልና፡ በደምህም፡ ለእግዚአብሔር ፡ ገዝተህናልና ፡ ከዘመድ፡ ሁሉ፡ ከቋንቋንም፡ ከወገንም፡ ከሕዝብም።

፲፡ ነገሥታትና፡ ካህናትም፡ ለአምላካችን፡ አድርገህናል፡ በምድርም፡ላይ፡እንነግሣለን። ም፡ ፩፡ ፮።

ፍ፡ ፳፡ ፮። ፍ፡ ፳፪፡ ፭።

፲፩፡ አየሁም፡ የብዙም፡ መላእክት፡ ድምጽ፡ ሰማሁ ፡ በዙፋኑና ፡ በእንስሶች ፡ ዙርያ ፡ በሽማግሌዎችም። ቍጥራቸውም፡ የብዙ፡ ብዙ፡ *እልፍ፡ አእላፋትም፡ ነበር። *ደን፡ ፯፡ ፲።

፲፪፡ በታላቅ፡ቃል፡እንደዚህ፡ ሲሉ። የታረደው፡ በግ፡ ይገባዋል፡ *ኃይል፡ ባለጠግነትም፡ ይወስድ፡ ዘንድ፡ ጥበብም፡ችሎትም፡ክብርም፡ምስጋናም፡ በረከትም።

*፩፡ ዜና፡ ፳፱፡ ፲፩። ፊል፡ ፪፡ ፱፡ ፲።

፲፫፡ በሰማይና፡ በምድርም፡ ያሉ፡ ፍጥረት፡ ሁሉ፡ በምድርም፡ታች፡ በባሕርም፡ በርሰዋም፡ ያሉ፡ ሁሉ። ሁሉን፡ሰማኋቸው፡ ሲሉ። በረከትና፡ክብር፡ ምስጋና ም፡ችሎትም፡ በዙፋን፡ ላይ፡ ለተቀመጠው፡ ይገባዋ ል፡ ለበጉም፡ ለዘላለሙ።

፲፬፡ አራቱም፡ እንስሶች፡ ይሉ፡ ነበር። አሜን። ሀ ያ፡አራቱም፡ ሽማግሎች፡ ወደቁ፡ ለዘላለሙም፡ ሕያ ው፡ ሁኖ፡ ለሚኖረው፡ ሰገዱ። ም፡ ፲፱፡ ፬።

## ምዕራፍ፡ ፮፡

፩፡ አየሁም፡በጉ፡ አንዱን፡ ከሰባቱ፡ ማሕተም፡ በ ከፈተ፡ ጊዜ፡ ካራቱ፡ እንስሶችም፡ አንዱን፡ ሰማሁ፡ እንደህ፡ሲል፡እንደ፡ ነጐድጓድ፡ ድምጽ። ና፡እይም። ም፡ ፬፡ ፯። ና፡ ፭፡ ፮፡ ፳።

፪፡ አየሁም፡እነሆ፡ነጭ፡ፈረስ፡ከተቀመጠበትም፡ ጋራ፡ቀስት፡ነበረ፡ አክሊልም፡ ተሰጠው፡ አሸንፎም፡ ወጣ፡ ያሸንፍም፡ ዘንድ። ዘካ፡ ፩፡ ፰፡—፲፯። ዘካ፡ ፮፡ ፩፡—፰።

፫፡ ሁለተኛውንም፡ ማሕተም፡በከፈተ፡ጊዜ፡ሁለ ተኛው፡እንስሳ፡ሲል፡ሰማሁ። ና፡ እይም።ም፡ ፬፡ ፯።

፬፡ ሌላ፡ ቀይ፡ ፈረስም፡ ወጣ፡ ለተቀመጠበትም፡ ተሰጠው፡ ሰላም፡ ከምድር፡ ያስወግድ፡ ዘንድ፡ እር ሱ፡ በርሳቸውም፡ እንዲጋደሉ፡ ታላቅ፡ ሰይፍም፡ ተሰ ጠው።

፭፡ ሶስተኛውንም፡ ማሕተም፡ በከፈተ፡ጊዜ፡ ሶስ ተኛው፡እንስሳ፡ ሲል፡ ሰማሁ። ና፡ እይም። አየሁም፡ እነሆ፡ ጥቍር፡ ፈረስ፡ በላዩ፡ በተቀመጠበትም፡ እጅ፡ ሚዛን፡ነበረ። ም፡ ፬፡ ፯።

፮፡ ድምጽም፡ ሰማሁ፡ ባራቱ፡ እንስሳ፡ መካከል፡ እንደህ፡ ሲል። አንድ፡ መስፈርያ፡ ስንዴ፡ በድሪም። ሶስት፡ መስፈርያ፡ ገብስም፡ በድሪም። ቅባኑ፡ግንና፡ጸ ጁንም፡አትጉዳቸው።

፯፡ አራተኛውንም ፡ ማሕተም፡ በከፈተ፡ ጊዜ፡ ያ ራተኛውን፡እንስሳ፡ ድምጽ፡ ሰማሁ፡ እንደህ፡ ሲል። ና፡እይም።

፰፡ አየሁም፡እነሆ፡ ቡላ፡ ፈረስ፡ በላዩም፡ የተቀመ ጠበት፡ ስሙ፡ ሞት፡ነው። ሲኦልም፡ ተከተለው፡ ከ ምድርም፡ ባራተኛው፡ ክፍል፡ ላይ፡ ሥልጣን፡ ተሰጣ ቸው፡ በሰይፍ፡ ሊገልዋቸው፡ በራብም፡ በሞትም፡በ ምድርም፡አራዊት። ኤር፡ ፲፭፡ ፫። ሕዝ፡ ፲፬፡ ፳፩።

፱፡ አምስተኛውም፡ ማሕተምን፡ በከፈተ፡ ጊዜ፡ ከመሠውያው፡ በታች፡ አየሁ፡ ስለ፡ እግዚአብሔር፡ ቃል፡የሞቱትን፡ ነፍሳት፡ ከርሳቸውም፡ ዘንድ፡ ስለ፡ ነበረችው፡ምስክር። ም፡ ፰፡ ፫። ፲፬፡ ፲፰። ፲፮፡ ፯።

፲፡ በታላቅ፡*ቃልም፡ይጮሁ፡ነበሩ፡ እንደህ፡ ሲሉ። ጌታ፡ ሆይ፡ ቅዱሱ፡ እውነተኛውም፡ †እስከ፡ መቸ፡ አትፈርድም ፡ ለደማችንስ፡ እስከ፡ መቸ፡ አትበቀል ም፡ በምድር፡ ላይ፡ ከሚኖሩ። *ዘፍ፡ ፬፡ ፲። †ም፡ ፲፰፡ ፲።

፲፩፡ *ነጭም፡ ልብስ፡ ለያንዳንዱ፡ ተሰጣቸው፡ ተባ ለላቸውም፡ ጥቂት፡ሌላ፡ ዘመን፡ያርፉ፡ ዘንድ፡ እንደ ርሳቸው፡ ያሉት፡ ባሮች፡ ወንድሞቻቸውም፡ እስኪ ፈጸሙ፡ ድረስ፡ እንደርሳቸው፡ ይሞቱ፡ ዘንድ፡ ያላ ቸው። *ም፡ ፫፡ ፭። ፯፡ ፱። ፲፫፡ ፲፬።

፲፪፡ ስድስተኛውንም፡ ማሕተም፡ በከፈተ፡ ጊዜ፡ አየሁ፡እነሆ፡ታላቅ፡ መናወጥ። *ጸሓይም፡ ጠቍረች፡ እንደ፡ ጸጕር፡ ማቅ። ጨረቃም፡ እንደ፡ ደም፡ ሆነ። *ኢሳ፡ ፲፫፡ ፲። ኢዮ፡ ፫፡ ፫፡ ፬። ሉቃ፡ ፳፩፡ ፳፭።

፲፫፡ የሰማይም፡ ከዋክብት፡ በምድር፡ ላይ፡ ወደ ቁ፡ በለስ፡ ያልበሰለውን፡ ፍሬ፡ እንድትጥል፡ ጽኑ፡ነፋ ስ፡ በወዘወዛት፡ ጊዜ። ኢሳ፡ ፴፬፡ ፬።

፲፬፡ ሰማይም፡ተመለሰች፡ መጽሐፍ፡ እንደሚታ ጸፍ። ተራራም፡ ደሴትም፡ ሁሉ፡ ከስፍራቸው፡ ተን ቀሳቀሱ።

፲፭፡ የምድርም፡ ነገሥታት፡ ታላላቆችም፡ ባለጠጎ ችም፡ የጓለቆችም፡ ብርቱችም፡ ባርያም፡ ሁሉ፡ የሰ ው፡ ልጅም፡ ሁሉ፡ በዋሻና፡ በተራሮች፡ ሕንጾች፡ ራሳ ቸውን፡ሰወሩ። ኢሳ፡ ፪፡ ፲፡ ፲፱።

፲፮፡ ተራሮችንም፡ሕንጾችንም፡በላያችን፡ውደቁ፡ አሉ። ሰውሩንም፡በዙፋን፡ላይ፡ከተቀመጠው፡ፊት፡ ከበጉም፡ ቍጣ። ሉቃ፡ ፳፫፡ ፴።

፲፯፡ የታላቁ፡ የቍጣው፡ቀን፡ደርሰዋልና። ማንስ፡ ይችላል፡ ይጸና፡ ዘንድ። ሮሜ፡ ፪፡ ፭።

## ምዕራፍ፡ ፯፡

፩፡ ከዚህም፡ በኋላ፡ አራት፡መላእክት፡ አየሁ፡ *ባ ራቱ፡ ምድር፡ ማዝን፡ ቁመው፡ አራቱን፡ የምድርን፡ ነፋስ፡ ይዘው፡ ነፋስ፡ እንዳይነፍስ፡ በምድር፡ላይ፡ በ ባሕርም፡ ለይ፡ በዛፍም፡ ሁሉ፡ላይ። *ዳን፡ ፯፡ ፪። ዘካ፡ ፮፡ ፭። ማቴ፡ ፳፬፡ ፴፩።

፪፡ ሌላውንም፡ መልአክ፡ አየሁ፡ ከጸሓይ፡ መው ጫ፡ ሲወጣ፡ ለርሱም፡ የሕያው፡ እግዚአብሔር፡ ማ ሕተም፡ ነበረለት። በታላቅ፡ ቃልም፡ ምድርንና፡ ባሕ ርን፡ ይጐዱ፡ ዘንድ፡ የተሰጣቸውን፡ አራቱን፡ መላእ ክት፡ጸራ፡እንደህ፡ሲል።

፫፡ ምድርን፡አትጕዱ፡ባሕርንም፡ ዛፎችንም፡ የአ ምላካችነን፡ ባሮች፡ በማሕተም፡ በግምባራቸው፡ ላ ይ፡ *እስክናመለክት፡ድረስ። *ሕዝ፡ ፱፡ ፬፡ ፮።

፬፡ የታተሙትንም፡ቍጥር፡ ሰማሁ። መቶ፡ አርባ፡ አራት፡ ሺህ፡ ከእሥራኤል፡ ልጆች፡ ወገን፡ ሁሉ፡ የታ ተሙ። ም፡ ፲፬፡ ፩፡ ፫።

፭፡ ከይሁዳ፡ወገን፡አሥራ፡ሁለት፡ሺህ፡የታተሙ። ከሮቤል፡ ወገንም፡ አሥራ፡ሁለት፡ ሺህ፡ የታተሙ። ከ ጋድ፡ ወገንመ፡ አሥራ፡ ሁለት፡ ሺህ፡ የታተሙ።

፮፡ ከአሴር፡ ወገንም፡ አሥራ፡ ሁለት፡ ሺህ፡ የታተ ሙ። ከንፍታሌም፡ ወገንም፡ አሥራ፡ ሁለት፡ ሺህ፡ የ ታተሙ። ከምናሴ፡ ወገንም፡ አሥራ፡ ሁለት፡ ሺህ፡ የ ታተሙ።

፯፤ ከስምዖን፡ ወገንም፡ አሥራ፡ ሁለት፡ ሺህ፡ የታተሙ። ከሌዊ፡ ወገንም፡ አሥራ፡ ሁለት፡ ሺህ፡ የታተሙ። ከይሳኮር፡ ወገንም፡ አሥራ፡ ሁለት፡ ሺህ፡ የታተሙ።

፰፤ ከዛብሎን፡ ወገንም፡ አሥራ፡ ሁለት፡ ሺህ፡ የታተሙ። ከዮሴፍ፡ ወገንም፡ አሥራ፡ ሁለት፡ ሺህ፡ የታተሙ። ከብንያም፡ ወገንም፡ አሥራ፡ ሁለት፡ ሺህ፡ የታተሙ።

፱፤ ከዚህም፡ በኋላ፡ አየሁ፡ እነሆም፡ ታላቅ፡ ሕዝብ፡ ለማንም፡ ይቈጥራቸው፡ ዘንድ፡ የማይቻለው። ከአሕዛብ፡ ሁሉ፡ ከወገንም፡ ከነገድም፡ ከቋንቋችም፡ በዙፋኑ፡ ፊት፡ ቁመው፡ በበጉም፡ ፊት፡ ነጭ፡ ልብስ፡ ለብሰው፡ የሰሌንም፡ ዝንጣፊች፡ በጃቸው፡ ይዘው። ም፡ ፯፤ ፲፩፤

፲፤ በታላቅ፡ ቃልም፡ ጮሁ፡ እንደዚህ፡ ሲሉ። መድኃኒት፡ በዙፋን፡ ላይ፡ ለተቀመጠ፡ ለምላካችንና፡ ለበጉ። ም፡ ፲፪፤ ፲፤

፲፩፤ *መላእክትም፡ ሁሉ፡ በዙፋኑና፡ በሽማግሎች፡ ግራቱ፡ እንስሶችም፡ ዙርያ፡ ቀሙ ፡ †በዙፋኑም፡ ፊት፡ በግምባራቸው፡ ወደቁ፡ ለእግዚአብሔርም፡ ሰገዱ፡ እንደዚህ፡ ሲሉ። *ም፡ ፭፤ ፲፩፤ †ም፡ ፲፩፤ ፲፮፤

፲፪፤ አሜን። በረከት፡ ክብርም፡ ጥበብም ፡ ምስጋናም፡ ገናንነትም፡ ኃይልም፡ ችሎትም፡ ለምላካችን፡ ይሁን፡ ለዘላለም። አሜን። ም፡ ፭፤ ፲፪፤

፲፫፤ አንዱም፡ ከሽማግሎቹ፡ መለሰ፡ እንደዚህ፡ ሲለኝ። እሌህ፡ ነጭ፡ ልብስ፡ የለበሱት፡ እለማን፡ ናቸው። ከወዴትስ፡ መጡ።

፲፬፤ እኔም፡ አልሁት። ጌታዬ፡ ሆይ፡ አንተ፡ ታውቃለህ። እርሱም፡ አለኝ። *ከታላቅ፡ መከራ፡ የመጡ፡ እሌህ፡ ናቸው። ልብሳቸውንም፡ አጸቡ፡ አነጽዋትም፡ በበጉ፡ ደም። *ም፡ ፫፤ ፲፤ ማቴ፡ ፳፬፤ ፳፩፤—፶፩፤

፲፭፤ ስለዚህም፡ እርሳቸው፡ በእግዚአብሔር፡ ዙፋን፡ ፊት፡ ናቸው፡ በቀንና፡ በሌትም፡ ያመልኩታል፡ *በመቅደሱ፡ በዙፋን፡ ላይ፡ የተቀመጠውም፡ ያድርባቸዋል። *ም፡ ፲፩፤ ፲፱፤ ፲፬፤ ፲፭፤ ፲፯፤ ፲፭፤ ፭፤ ፰፤ ም፡ ፲፮፤ ፩፤ ፳፩፤ ፫፤ ፳፪፤

፲፮፤ ደግሞም፡ አይራቡም፡ ደግሞም፡ አይጸሙም፡ ጸሐይም፡ አትወርድባቸውም፡ ትኩሳትም፡ ሁሉ፡ አይወርድባቸውም። ኢሳ፡ ፵፱፤ ፲፤

፲፯፤ በዙፋኑ፡ መካከል፡ ያለው፡ *በግ፡ ያሰማራቸዋልና፡ †ወደ፡ ሕይወት፡ ውኃ፡ ምንጭም፡ ይመራቸዋልና፡ **እግዚአብሔርም፡ እንብን፡ ሁሉ፡ ካይናቸው፡ ያብሳል *ም፡ ፭፤ ፮፤ †መዝ፡ ፳፫፤ ፪፤ **ም፡ ፳፩፤ ፩፤ ኢሳ፡ ፳፭፤ ፰፤

## ምዕራፍ፡ ፰፤

፩፤ ሰባተኛውንም፡ ማሕተም፡ በከፈተ፡ ጊዜ፡ በሰማይ፡ ዝምታ፡ ሆነ፡ እኩል፡ ሰዓት፡ የሚሆን። ዘካ፡ ፱፤ ፲፫፤ አንባ፡ ፪፤ ፳፤

፪፤ ሰባቱንም፡ መላእክት፡ በእግዚአብሔር፡ ፊት፡ የቆሙት፡ አየሁ። ሰባት፡ መለከትም፡ ተሰጣቸው። ማቴ፡ ፳፬፤ ፴፩፤

፫፤ ሌላም፡ መልአክ፡ መጣ፡ በመሠውያውም፡ ላይ፡ ቆመ፡ ከርሱ፡ ጋራም፡ የወርቅ፡ ማዕጠን፡ ነበረ፡ ብዙ፡ ዕጣንም፡ ተሰጠው፡ ይጨምረው፡ ዘንድ፡ ከቅዱሳን፡ ሁሉ፡ ጸሎት፡ ጋራ፡ በዙፋኑ፡ ፊት፡ ባለው፡ በወርቁ፡ መሠውያ፡ ላይ። ም፡ ፭፤ ፰፤

፬፤ የዕጣኑም፡ ጢስ፡ ወጣ፡ ከቅዱሳን፡ ጸሎት፡ ጋራ፡ ከመልአኩ፡ እጅ፡ በእግዚአብሔር፡ ፊት። መዝ፡ ፻፵፩፤ ፪፤

፭፤ መልአኩም፡ ማዕጠንቱን፡ ወሰደ፡ የመሠውያውንም፡ እሳት፡ መላበት፡ በምድር፡ ላይም፡ ጣለው፡ ድምጽም፡ ሆነ፡ ነጐድጓድም፡ መብረቅችም፡ መናወጥም። ሕዝ፡ ፲፤ ፪፤

፮፤ ሰባት፡ መለከትም፡ ያላቸው፡ ሰባቱ፡ መላእክት፡ ሊነፉ፡ ተዘጋጁ።

፯፤ የፊተኛው፡ መልአክም፡ ነፋ፡ በረደና፡ እሳትም፡ ሆነ፡ በደም፡ ተቀላቅሉ፡ በምድርም፡ ወደቀ። የዛፉም፡ ሲሶ፡ ተቃጠለ፡ *የለመለመውም፡ ሣዕር፡ ሁሉ፡ ተቃጠለ። *ዘፀአ፡ ፱፤ ፳፫፤

፰፤ ሁለተኛውም፡ መልአክ፡ ነፋ፡ እንደ፡ *ታላቅ፡ ተራራም፡ ያለ፡ በእሳት፡ እንደ፡ ተቃጠለ፡ በባሕር፡ ወደቀ፡ የባሕሩም፡ ሲሶ፡ †ደም፡ ሆነ። *ኤር፡ ፶፩፤ ፳፭፤ †ዘፀአ፡ ፯፤ ፳፤ ፳፩፤

፱፤ በባሕርም፡ ያለው፡ ነፍስ፡ ያለው፡ ፍጥረት፡ ሲሶው፡ ሞተ። ሲሶውም፡ መርከብ፡ ጠፋ።

፲፤ ሶስተኛውም፡ መልአክ፡ ነፋ፡ *ታላቅ፡ ኮከብም፡ ከሰማይ፡ ወደቀ፡ እንደ፡ መብራት፡ ሲያበራ፡ በፈሳሹም፡ ሲሶ፡ ላይ፡ ወደቀ፡ በውኃውም፡ ምንጮች፡ ላይ። *ኢሳ፡ ፲፬፤ ፲፪፤ ይን፡ ፰፤ ፲፤

፲፩፤ ኮከቡም፡ አፍሰንቴን፡ ይባላል። የውኃውም፡ ሲሶ፡ አፍሰንቴን፡ ሆነ፡ ብዙ፡ ሰዎችም፡ ሞቱ፡ ከውኃው፡ የተነሣ፡ መራራ፡ ሁናለችና።

፲፪፤ አራተኛውም፡ መልአክ፡ ነፋ፡ *የጸሓዩ ቱም፡ ሲሶ፡ ተመታ፡ የጨረቃውም፡ ሲሶ፡ የከዋክብቱም፡ ሲሶ፡ ሲሰዋቸው፡ †ይጨልም፡ ዘንድ፡ ቀኑም፡ ሲሶው፡ እንደያበራ፡ ሌቱም፡ እንደሁ። *ም፡ ፮፤ ፲፪፤ †ዘፀአ፡ ፲፡ ፳፩፤

፲፫፤ አየሁም፡ ሰማሁም፡ *አንድ፡ መላእክት፡ በሰማይ፡ መካከል፡ የሚበር፡ በታላቅ፡ ቃል፡ ኢያለ። †ወዮ፡ ወዮ፡ ወዮ፡ በምድር፡ ለሚኖሩ፡ ከቀሩት፡ ከሶስቱ፡ መላእክት፡ መለከት፡ ድምጽ፡ ይነፉ፡ ዘንድ፡ ያላቸው። *ም፡ ፲፬፤ ፮፤ ም፡ ፱፤ ፲፪፤ ና፡ ፲፩፤ ፲፬፤ ና፡ ፲፪፤ ፲፪፤

## ምዕራፍ፡ ፱፤

፩፤ አምስተኛውም፡ መልአክ፡ ነፋ፡ *ኮከብም፡ ከሰማይ፡ በምድር፡ ላይ፡ ሲወድቅ፡ አየሁ፡ የጠለቀም፡ ጕድጓድ፡ †መክፈቻ፡ ተሰጠው። *ም፡ ፰፤ ፲፤ †ም፡ ፳፤ ፩፤

፪፤ የጠለቀውንም፡ ጕድጓድ፡ ከፈተው፡ ከጕድጓ
ዱም፡ ጢስ፡ ወጣ፡ እንደ፡ ታላቅ፡ እንደ፡እቶን፡ጢስ፡
ጸሐይም፡ *ጠቈረች፡ አየርም፡ ከጕድጓዱ፡ ጢስ፡ የ
ተነሣ። ኢዮ፡ ፪፡ ፪፡ ፲።

፫፤ ከጢሱም፡ አንበጣ፡ ወጣ፡ በምድር፡ ላይ፡ ሥል
ጣንም፡ ተሰጣቸው፡ እንደ፡ ምድር፡ ጊንጦች፡ ሥል
ጣን።

፬፤ ተባለላቸውም፡የምድሩን፡ሣር፡እንዳይጐዱ፡
ማናቸውንም፡ የለመለመውን፡ ሁሉ፡ ዛፉንም፡ ሁ
ሉ። ከሰዎች፡ በቀር፡ የእግዚአብሔር፡ *ማሕተም፡
በግምባራቸው፡ የሌለባቸውን። *ምዕ፡ ፯፡ ፫።

፭፤ እንዳይገልዋቸውም፡ ተሰጣቸው፡ አምስት፡
ወር፡ ሊሣቅዩዋቸው፡ እንጂ። ሥቃያቸውም፡ እን
ደ፡ ጊንጥ፡ ሥቃይ፡ ነው፡ ሰውን፡ በነደፈች፡ ጊዜ።

፮፤ በዚያም፡ ወራት፡ሰዎች፡ ሞት፡ ይሻሉ፡ አያገኙ
ትምም። ይሞቱ፡ ዘንድም፡ ይወዷሉ፡ ሞትም፡ ከር
ሳቸው፡ ይሸሻል። ሉቃ፡ ፳፫፡ ፴፡—፴፪።

፯፤ *ያንበጣውም፡ ምሳሌ፡ ለሰልፍ፡ እንደ፡ ተዘጋ
ጀ፡ ፈረስ፡ ይመስላል፡ በራስዋም፡ ላይ፡ ወርቅ፡ እንደ
ሚመስል፡አክሊል፡ አለ። ፊትዋም፡እንደ፡ሰው፡ ፊ
ት፡ ነው። *ኢዮ፡ ፪፡ ፬።

፰፤ ጸጕርም፡ አላት፡ እንደ፡ ሴት፡ ጸጕር። ጥርሰዋ
ም፡ እንደ፡ አንበሳ፡ ጥርስ፡ ነው።

፱፤ ጥሩርም፡ አላት፡ እንደ፡ብረት፡ ያለ። የክንፎቿ
ዋም፡ ድምጽ፡ እንደ፡ ብዙ፡ እንደ፡ ፈረስ፡ ሠረገላ፡
ድምጽ፡ ነው፡ ወደ፡ ሰልፍ፡ እንደምትሮጥ።

፲፤ ጅራትም፡አላት፡የጊንጥ፡*ጅራት፡የሚመስል።
በጅራትዋም፡ ኰሀ፡ አለበት። ሥልጣንዋም፡ አምስ
ት፡ ወር፡ ሰውን፡ ትሣቅይ፡ ዘንድ፡ ነው። *ቍ፡ ፲፱።

፲፩፤ ለርሳቸውም፡ ንጉሥ፡ አላቸው፡ የጥልቅ፡መላ
ክ። ስሙም፡ ብዕብራይስጥ፡ አባዶን፡ ነው፡ በፅርዕ
ም፡ ስሙ፡ አጶልዮን፡ ይባላል። ቍ፡ ፩።

፲፪፤ አንዱ፡ ወዮ፡ ሔደ፡ እነሆ፡ ደግሞ፡ *ሁለት፡ ወ
ዮ፡ይመጣል፡ከዚህ፡በኋላ። *ምዕ፡ ፰፡ ፲፫። ና፡ ፲፩፡ ፲፬።

፲፫፤ ስድስተኛውም፡መልአክ፡ነፋ፡አንድ፡ ድምጽ
ም፡ ሰማሁ፡ ከወርቁ፡ መሠውያ፡ ካራቱ፡ ቀንዶች፡ በ
እግዚአብሔር፡*ፊት፡ ካለው። *ምዕ፡ ፰፡ ፫።
ዘፀአ፡ ፴፡ ፩።

፲፬፤ እንዲህ፡ ሲል፡ለስድስተኛው፡ መልአክ፡ መለ
ከት፡ ለያዘው። *በታላቁ፡ ወንዝ፡ በኤፍራጥስ፡ የታ
ሠሩትን፡ አራቱን፡ መላእክት፡ ፍታ። ምዕ፡ ፲፮፡ ፲፪።

፲፭፤ አራቱ፡ መላእክትም፡ ተፈቱ፡ የተዘጋጁ፡ት፡ ለ
ሰዓት፡ ለቀንም፡ ለወርም፡ ለመትም፡ *ሲሶውን፡ሰ
ው፡ ይገሉ፡ ዘንድ። *ምዕ፡ ፰፡ ፯።

፲፮፤ ያርበኞችም፡ ጭፍራ፡ ቍጥር፡ ሁለት፡ እልፍ፡
አእላፋት፡ናቸው። ቍጥራቸውንም፡ ሰማሁ።

፲፯፤ እንዲሁም፡በራእይ፡ ፈረሱን፡አየሁ፡ በርሳቸ
ውም፡ የተቀመጡባቸውን። በርሳቸውም፡የእሳት፡
ጥሩር፡ አለባቸው፡ ያሰማንጉንም፡ የዲንም። የፈረ
ሱም፡ ራስ፡ እንደ፡ አንበሳ፡ራስ፡ነበር፡ካፋቸውም፡ይ
ወጣል፡ እሳት፡ ጢስም፡ ዲንም።

፲፰፤ ከዚህም፡ ከሦስቱ፡ የሰው፡ሲሶው፡ሞተ፡ከእ
ሳት፡ ከጢስም፡ ከዲንም፡ ካፋቸው፡ ከሚወጣው።

፲፱፤ የፈረሶች፡ ሥልጣን፡ ባፋቸው፡ ነውና፡ በጅራ
ታቸውም። ጅራታቸውም፡ እባብ፡ ይመስላል፡ ራስ
ም፡ አለው፡በርሱም፡ ይጐዳሉ።

፳፤ የቀሩትም፡ ሰዎች፡ በዚህ፡ መቅሠፍት፡ያልሞ
ቱ፡ ከጃቸው፡ ሥራ፡ *ንስሐ፡ አይገቡም፡ ነበር፡ ለሰይ
ጣናት፡ †እንዳይሰግዱ፡ለወርቅም፡ጣዖት፡ ለብርም፡
ለናስም፡ለድንጊያም፡ለንጨትም። የማትችል፡ታይ፡
ዘንድ፡ትሰማ፡ትሔድም፡ዘንድ። *ምዕ፡ ፲፮፡ ፲፩፡ ፳፩።
†፩፡ ቆሮ፡ ፲፡ ፳።

፳፩፤ ደም፡ ከማፍሰሳቸውም፡ አይመለሱም፡ ነበ
ሩ። አስማትም፡ከማድረጋቸው፡ከዝሙታቸውም፡
ከመስረቃቸውም።

ምዕራፍ፡ ፲፤

፩፤ ሌላ፡ *ብርቱ፡ መልአክም፡ አየሁ፡ ከሰማይ፡ ሲ
ወርድ፡ በደመና፡ ተጐናጽፎ፡ በራሱ፡ ላይም፡ *የደመ
ና፡ ቀስት፡ ነበረ፡ ፊቱም፡ እንደ፡ ጸሐይ፡ ነው፡ እግሮቹ
ም፡ እንደ፡ እሳት፡ ዓምድ፡ ናቸው። *ምዕ፡ ፭፡ ፪።
†ምዕ፡ ፬፡ ፫።

፪፤ *በጁም፡ታናሽ፡መጽሐፍ፡የተዘረጋ፡ ነበረ፡ቀኝ፡
እግሩንም፡ በባሕር፡ ላይ፡ አደረገ፡ ግራውንም፡ በም
ድር፡ ላይ። *ምዕ፡ ፭፡ ፩።

፫፤ በታላቅ፡ ቃልም፡ ጮኸ፡ እንደሚጮህ፡ *አንበ
ሳ። በጮኸም፡ ጊዜ፡ ሰባቱ፡ ነጐድጓዶች፡ በቃላቸው፡
ተናገሩ። *ኤር፡ ፳፭፡ ፴። ሆሴ፡ ፲፩፡ ፲። አሞ፡ ፩፡ ፪።

፬፤ ሰባቱ፡ ነጐድጓዶችም፡ በቃላቸው፡ በተናገሩ፡ ጊ
ዜ፡ እጽፍ፡ ብዬ፡ ነበርሁ። ከሰማይም፡ ድምጽ፡ ሰማ
ሁ፡ እንዲህ፡ የሚለኝ። ተወው፡ ሰባቱ፡ ነጐድጓድ፡ የ
ተናገሩትን፡ አጻፈውም። ዳን፡ ፰፡ ፳፮።
ምዕ፡ ፲፪፡ ፬፡ ፱።

፭፤ በምድርና፡ በባሕር፡ ላይም፡ ቁሞ፡ያየሁት፡ መ
ልአክ፡ እጁን፡ ወደ፡ሰማይ፡አነሣ። ዘፍ፡ ፲፬፡ ፳፪።

፮፤ በዘላለሙ፡ ሕያውም፡ *ማለ፡ሰማይን፡ በፈጠ
ረ፡ በርስዋም፡ ያሉትን፡ ባሕርንም፡ በርሱም፡ ያሉት
ን። †እንግዲህ፡ ዘመን፡ እንዳይሆን።
*ዳን፡ ፲፪፡ ፯። †ምዕ፡ ፮፡ ፲፩።

፯፤ ነገር፡ ግን፡ *በሰባተኛው፡ መልአክ፡ ድምጽ፡ ወ
ራት፡ ይነፋ፡ ዘንድ፡ ባለው፡ ጊዜ፡ የእግዚአብሔር፡
†ምሥጢር፡ ይጨረሳል፡ ለባሮቹ፡ ለነቢያት፡ እንደ፡ተ
ናገረ። *ምዕ፡ ፲፩፡ ፲፭። †፩፡ ቆሮ፡ ፲፭፡ ፶፩።

፰፤ ከሰማይም፡ ሰምቸው፡ የነበርሁ፡ቃል፡ ደግሞ፡
ከኔ፡ ጋራ፡ ተናገረ፡ አለም። ሒድና፡ ታናሹን፡ መጽሐ
ፍ፡ የተከፈተውን፡ ውሰድ፡በምድር፡ ላይና፡ በባሕር፡
ላይ፡ በቆመው፡ በመልአኩ፡ እጅ፡ ያለውን።

፱፤ ወደ፡ መልአኩም፡ ሔድሁ፡ አልሁትም። ታና

ሹን፡ መጽሐፍ፡ ስጠኝ። አለኝም። *ውሰደው፡ ብላውም፡ ሆድህንም፡ ያምረረው፡ ባፍህ፡ ግን፡ ጸፋጭ፡ ይሆን፡ እንደ፡ ማር። ሕዝ፡ ፫፡ ፩፡—፫፡፡

፲፡ ታናሹንም፡ መጽሐፍ፡ ወሰድሁ፡ ከመልአኩ፡ እጁ፡ በላሁትም፡ ባፌም፡ እንደ፡ ማር፡ ጸፋጭ፡ ሆነ። ብበላሁትም፡ ጊዜ፡ ሆዴን፡ አመረረው።

፲፩፡ አለኝም። ይገባሃል፡ ትንቢት፡ ትናገር፡ ዘንድ፡ ደግሞ፡ በሕዝብና፡ በአሕዛብ፡ ላይ፡ በቋንቋችም፡ በብዙም፡ ነገሥታት፡ ላይ።

ምዕራፍ፡ ፲፩፡

፩፡ *ዘንግም፡ ተሰጠኝ፡ እንደ፡ በትር፡ ያለ። መልአኩም፡ ቆመ፡ እንዲህ፡ሲለኝ። ተነሣ፡ የእግዚአብሔርንም፡ መቅደስ፡ ስፈር፡ መሠውያውንም፡ በርሱ፡ የሚሰግዱትንም። *ሕዝ፡ ፵፡ ፫፡፡ ዘካ፡ ፪፡ ፩፡ ፪፡፡

፪፡ ከመቅደሱ፡ በሚደ፡ያለውን፡ ወለሉን፡ ግን፡ ተወው፡ አትለካውም፡ *ለአሕዛብ፡ ተሰጥቶዋልና፡ የተቀደሰችውንም፡ አገር፡ ይረግጥዋታል፡ †አርባ፡ ሁለት፡ ወር። *ሉቃ፡ ፳፩፡ ፳፬፡፡ †ም፡ ፲፩፡ ፫፡፡ ፍ፡ ፲፪፡ ፮፡ ፲፬፡፡ ፍ፡ ፲፫፡ ፭፡፡

፫፡ ሥልጣንም፡ እሰጣለሁ፡ ለሁለቱ፡ ሰማዕታቴ፡ ሺህ፡ ከሁለት፡ መቶ፡ ስድሳ፡ ቀንም፡ ትንቢት፡ ይናገራሉ፡ ማቅ፡ ለብሰው። ቀ፦ ፬፡፡

፬፡ እሌህ፡ ሁለቱ፡ ዘይቶች፡ ሁለቱም፡ መቅረዞች፡ በእግዚአብሔር፡ ፊት፡ በምድር፡ጌታ፡ ፊት፡ የቆሙ፡ ናቸው። ዘካ፡ ፬፡ ፫፡ ፲፩፡ ፲፬፡፡

፭፡ ማንም፡ ይጉዳቸው፡ዘንድ፡ቢወድ፡ ካፋቸው፡ እሳት፡ትወጣለች፡ጸላቶቻቸውንም፡*ታቃጥላቸዋለች። ማንም፡ደግሞ፡ ሊበድላቸው፡ቢወድ፡ እንዲሁ፡ ይሞት፡ ዘንድ፡ ይገባል። *፪፡ ነገሥ፡ ፩፡ ፲፡፡

፮፡ እሌህ፡ ሥልጣን፡ አላቸው፡ *ሰማይን፡ ይዘጉ፡ ዘንድ፡ ዝናም፡ እንዳታዘንም፡ ትንቢት፡ በሚናገሩበት፡ ወራት። ለርሳቸውም፡ ሥልጣን፡ አላቸው፡ በውኆች፡ላይ፡ ለደም፡ሊመልስዋቸው፡ ምድርንም፡ይቀሥፉ፡ ዘንድ፡ በመቅሠፍቱ፡ ሁሉ፡ በሚሹት፡ ጊዜ፡ ሁሉ። *፩፡ ነገሥ፡ ፲፯፡ ፩፡፡ †ዘፀአ፡ ፯፡ ፲፱፡ ፳፡፡

፯፡ ሰማዕትነታቸውንም፡በፈጸሙ፡ጊዜ፡ ከቀላይ፡ የወጣው፡ አርዌ፡ ከርሳቸው፡ ጋራ፡ ሰልፍ፡ ያደርጋል፡ ያሸነፋቸውማል፡ ይገላቸውማል። ም፡ ፲፫፡ ፩፡ ፯፡፡ ፍ፡ ፲፯፡ ፰፡፡

፰፡ ሬሳቸውም፡ ትቀመጣለች፡ *በታላቂቱ፡አገር፡ አደባባይ፡ በመንፈሳዊ፡ ነገር፡ ሶዶምና፡ ምሥር፡ የምትባል፡ ጌታችን፡ ወደ፡ ተሰቀለባት። *ም፡ ፲፮፡ ፲፱፡፡ ሉቃ፡ ፲፫፡ ፴፬፡፡

፱፡ ሬሳቸውንም፡ ያዩታል፡ ሕዝብና፡ አሕዛብ፡ ቋንቋችም፡ ወገኖችም፡ ሦስት፡ ቀንና፡ እኩል፡ ሬሳቸውንም፡ ወደ፡ መቃብር፡ ትገባ፡ ዘንድ፡ አይተውም።

፲፡ በምድርም፡ የሚኖሩ፡ በርሳቸው፡ ላይ፡ ደስ፡ ይላቸዋል፡ ገጸ፡ በረከትም፡ ይቀባበላሉ፡ እርሱ፡በርሳቸው። እሌህ፡ ሁለቱ፡ ነቢያት፡ በምድር፡ የሚኖሩን፡ ያሠቃዩ፡ ነበሩና።

፲፩፡ ከሦስት፡ ቀንና፡እኩል፡ በኋላም፡ በእግዚአብሔር፡የሕይወት፡ መንፈስ፡ገባባቸው፡ በግራቸውም፡ ቆሙ፡ባዩዋቸውም፡ ላይ፡ታላቅ፡ ፍርሃት፡ ወደቀባቸው።

፲፪፡ ታላቅ፡ ቃልም፡ ሰሙ፡ ከሰማይ፡እንዲህ፡ ሲላቸው። ወደዚህ፡ ውጡ። *ወደ፡ሰማይም፡ በደመና፡ ወጡ፡ጸላቶቻቸውም፡አዩዋቸው። *፪፡ ነገሥ፡፪፡፲፩፡፡

፲፫፡ በዚያችም፡ ሰዓት፡ታላቅ፡ መናወጥ፡ሆነ። የከተማዪቱም፡አሥረኛ፡ ወደቀ። በመናወጥም፡ሰባት፡ ሺህ፡ የሰው፡ ስም፡ሞተ። የቀሩትም፡ ፈሩ፡ለሰማይ፡ አምላክም፡ ምስጋና፡ ሰጡ።

፲፬፡ *ሁለተኛው፡ ወዮ፡ ሔደ። †ሦስተኛውም፡ ወዮ፡ እነሆ፡ ፈጥኖ፡ይመጣል። *ም፡ ፱፡ ፲፪፡፡ †ቀ፦ ፲፭፡፡ ም፡ ፲፪፡ ፲፪፡፡

፲፭፡ ሰባተኛውም፡ መልአክ፡ ነፋ። በሰማይም፡ ታላቅ፡ ድምጽ፡ ሆነ፡ እንዲህ፡ ሲል። *የዓለሙ፡ መንግሥት፡ለጌታችንና፡ለመሢሑ፡ ሆነች፡†ለዘላለሙም፡ ይነግሣል። *ዳን፡ ፪፡ ፵፬፡፡ ፍ፡ ፯፡ ፳፯፡፡ †ዘካ፡ ፲፬፡ ፱፡፡

፲፮፡ ሀያ፡ አራቱም፡ *ሽማግሎች፡ በእግዚአብሔር፡ ፊት፡ ተቀምጠው፡የነበሩት፡ በወንበራቸው፡ላይ፡ በግምባራቸው፡ †ወደቁ፡ለእግዚአብሔርም፡ሰገዱ፡ እንዲህ፡ ሲሉ። *ም፡ ፬፡ ፬፡ ፲፡፡ †ም፡ ፯፡ ፲፩፡፡

፲፯፡ እናመሰግንሃለን፡እግዚአብሔር፡አምላክ፡ሆይ፡ ሁሉን፡ የሚይዝ፡ የነበረ፡ያለም፡የሚመጣም፡ታላቂቱን፡ ኃይልህን፡ ወስደህ፡ ነግሠሃልና። ም፡ ፬፡ ፰፡፡

፲፰፡ አሕዛብም፡ ተቈጡ፡ ቍጣህም፡መጣ፡የሙታንም፡ ዘመን፡ ሊኰነኑ፡ ለባሮችህም፡ ዋጋቸውን፡ ትሰጥ፡ዘንድ፡ለነቢያት፡ለቅዱሳንም፡ስምህንም፡ለሚፈሩ፡ ለታናሾች፡ ለታላቆችም፡ ምድርንም፡ የሚያጠፉን፡ ታጠፋለህ። ም፡ ፲፭፡ ፩፡፡ መዝ፡ ፪፡ ፩፡፡ ፍ፡ ፭፡ ፲፪፡፡

፲፱፡ የእግዚአብሔርም፡ *መቅደስ፡በሰማይ፡ ተከፈተ፡ በመቅደሱም፡የኪዳኑ፡ ታቦት፡ ተገለጠ፡መብረቅም፡ ሆነ፡ ድምጽም፡ ነጐድጓድም፡ መናወጥም፡ ታላቅም፡ በረደ። *ም፡ ፲፭፡ ፭፡፡

ምዕራፍ፡ ፲፪፡

፩፡ ታላቅም፡ መልክት፡ በሰማይ፡ ታየ። ሴት፡ ጸሓይ፡ ተጐናጽፋ፡ ጨረቃም፡ ከግርዋ፡ በታች። በራስዋም፡ ላይ፡ ያሥራ፡ ሁለት፡ ከዋክብት፡ ዘውድ።

፪፡ እርስዋም፡ የጸነሰች፡ ነበረች፡ ትጮኽማለች፡ ምፅም፡ ተይዛለች፡ *ተጨንቃማለች፡ ትወልድ፡ ዘንድ። *ሚካ፡ ፬፡ ፲፡፡

፫፡ ሌላም፡ ምልክት፡ በሰማይ፡ ተገለጠ። እነሆት፡ ታላቅ፡ ቀይ፡ ዘንደ፡ለርሱም፡ ሰባት፡ራሶች፡ አሉት፡ አሥርም፡ ቀንዶች፡ በራሶቹም፡ ላይ፡ ሰባት፡ ዘውዶች። ቀ፦ ፱፡፡

፬፡ ጅራቱም፡ የሰማይን፡ *ከዋክብት፡ ሲሶውን፡ ጐተተ፡ በምድርም፡ ጣላቸው። ዘንደውም፡ ቀመ፡ ትወልድ፡ ዘንድ፡ ባለችው፡ በሴቲቱ፡ፊት፡ በወለደች፡ ጊዜ፡ ልጅዋን፡ይውጠው፡ ዘንድ። *ዳን፡ ፰፡ ፲፡፡

፭፡ ወንድ፡ ልጅም፡ ወለደች፡ አሕዛብን፡ ሁሉ፡ *በብረት፡በትር፡ይጠብቅ፡ዘንድ፡ያለውን፡ ልጅዋም፡ ወደ፡እግዚአብሔር፡ ወደ፡ ዙፋኑም፡ ተነጠቀ።
*መዝ፡ ፪፡ ፱፡፡ ራእ፡ ፲፱፡ ፲፭፡፡

፮፡ ሴቲቱም፡ ወደ፡ በረሃ፡ *ኰበለለች፡ ከእግዚአብሔር፡ ዘንድ፡ ተዘጋጅቶላት፡ ወደለው፡ ስፍራ፡ ከዚያ፡ይመግብዋት፡ዘንድ፡†ሽህ፡ከሁለት፡ መቶ፡ ስድሳ፡ ቀን። *መቴ፡ ፪፡ ፲፫፡፡ †ራእ፡ ፲፩፡ ፫፡፡

፯፡ በሰማይም፡ ሰልፍ፡ ሆነ። *ሚካኤልና፡ መላእክቱ፡ዘንደውን፡ተዋጉ። ዘንደውም፡ ተዋጋው፡ ከመላእክቱ፡ጋራ። *ዳን፡ ፲፡ ፲፫፡ ፳፩፡፡ ና፡ ፲፪፡ ፩፡፡

፰፡ አላሸነፈምም።ከዚያ፡ ወዲያም፡ በሰማይ፡ ስፍራ፡ አልተገኘላቸውም።

፱፡ ታላቁም፡ ዘንዶ፡ *ተጣለ፡ እርሱም፡ †የቀደመው፡እባብ፡ዲያብሎስ፡ የሚባል፡ ሰይጣንም፡ ዓለሙን፡ ሁሉ፡ የሚያስት። በምድር፡ ላይም፡ ተጣለ፡ መላእክቱም፡ ከርሱ፡ ጋራ፡ ተጣሉ። *ሉቃ፡ ፲፡ ፲፰፡፡
ዮሐ፡ ፲፪፡ ፴፩፡፡ †ዘፍ፡ ፫፡ ፩፡ ፲፬፡፡

፲፡ በሰማይም፡ታላቅ፡ ቃልን፡ ሰማሁ፡እንዲህ፡ ሲል። *አሁን፡ ያምላካችን፡ መድኃኒት፡ ቸሉቱም፡ መንግሥቱም፡ የመሢሑ፡ ሥልጣንም፡ ሆነች። ወንድሞቻችነን፡ የሚያሳጣቸው፡ ወድቋልና፡ ባምላካችን፡ ፊት፡ †ያሳጣቸው፡የነበረ፡ ሌትና፡ ቀን።
*ም፡ ፲፩፡ ፲፭፡፡ †ኢዮብ፡ ፩፡ ፲፩፡፡ ዘካ፡ ፫፡ ፩፡፡
ሉቃ፡ ፳፪፡ ፴፩፡፡

፲፩፡ እርሳቸውም፡*ድል፡ነሡበት፡በበጉ፡ †ደም፡በምስክርነታቸውም፡ **ቃል፡ ነፍሳቸውንም፡ አልወደዱም፡ እስከ፡ ሞት፡ ድረስ። *ሮሜ፡ ፰፡ ፴፯፡፡
†ም፡ ፮፡ ፲፬፡፡ **ቍ፡ ፲፯፡፡

፲፪፡ ስለዚህ፡ ደስ፡ ይበላችሁ፡ እላንተ፡ ሰማዮች፡ በርሳቸውም፡ ያላችሁ። በምድርና፡ በባሕር፡ ለምትኖሩ፡ግን፡ ወዮላችሁ። ዲያብሎስ፡ ወርዶባችኋልና፡ በርሱም፡ታላቅ፡ቍጣ፡ አለበት፡ ጥቂት፡ ዘመን፡ እንደ፡ ቀረላት፡ያውቃልና።

፲፫፡ ዘንደውም፡ ወደ፡ ምድር፡ እንደ፡ ተጣለ፡ ባየ፡ ጊዜ፡ ወንድ፡ ልጅ፡ የወለደችውን፡ ሴት፡ አሳደደ።

፲፬፡ ለሴቲቱም፡ የታላቅ፡ ንስር፡ ሁለት፡ ክንፍ፡ ተሰጣት፡ወደ፡ በረሃ፡ ትበር፡ ዘንድ፡ ወደ፡ ስፍራዋ፡ ከዚያ፡ወደምትመገብበት፡ ስፍራ፡*አንድ፡ ዘመን፡ሁለትም፡ዘመን፡ የዘመን፡ እኩሌታም፡ ከእባቡ፡ፊት።
*ዳን፡ ፯፡ ፳፭፡፡ ና፡ ፲፪፡ ፯፡፡

፲፭፡ እባቢቱም፡ ካፉዋ፡ ውኃ፡ ተፋች፡ እንደ፡ ፈሳሽ፡ወንዝ፡ከሴቲቱ፡ በኋላ፡ከውኃ፡ እንደ፡ ተወሰደች፡ ሊያደርጋት።

፲፮፡ ምድሪቱም፡ ሴቲቱን፡ ረዳቻት፡ ምድሪቱም፡ አፏዋን፡ከፈተች፡ ዘንደው፡ካፉ፡ የተፋውንም፡ ፈሳሽ፡ወንዝ፡ ዋጠችው።

፲፯፡ ዘንደውም፡ በሴቲቱ፡ ላይ፡ ተቈጣ፡ ከቀረትም፡ ዘርዋ፡ጋራ፡ ሰልፍ፡ያደርግ፡ ዘንድ፡ ሔደ፡ *የእግዚአብሔርን፡ ትእዛዝ፡ ከሚጠብቁ፡ የየሱስ፡ ክርስቶስም፡ ምስክር፡ ካላቸው። *ም፡ ፲፬፡ ፲፪፡፡ ና፡ ፲፱፡ ፲፡፡
፩፡ዮሐ፡ ፭፡ ፲፡፡

ምዕራፍ፡ ፲፫፡

፩፡ በባሕርም፡ አሸዋ፡ ላይ፡ ቆምሁ። *አርዌም፡ ከባሕር፡ሲወጣ፡አየሁ፡ ለርሱም፡አሥር፡ ቀንዶች፡ አሉት፡ ሰባትም፡ ራሶች፡ በቀንዶቹም፡ ላይ፡ አሥር፡ አክሊሎች፡ በራሶቹም፡ላይ፡ የስድብ፡ ስም።
*ም፡ ፲፩፡ ፯፡፡ ና፡ ፲፯፡ ፫፡፡ ዳን፡ ፯፡ ፯፡ ፰፡፡

፪፡ ያየሁትም፡አርዌ፡ነምር፡ ይመስላል፡ እግሩም፡ እንደ፡ድብ፡እግር፡ ነው፡ አፉም፡ እንደ፡ አንበሳ፡ አፍ፡ ነው።*ዘንደውም፡ ኃይሉን፡ ሰጠው፡ዙፋኑንም፡ታላቅም፡ ሥልጣን። *ም፡ ፲፪፡ ፫፡፡

፫፡ አንድ፡ራሱንም፡ አየሁ፡ ለሞት፡ እንደ፡ ታረደ፡ የሞቱም፡ ቍስል፡ ዳነ፡ *ምድር፡ ሁሉም፡ ተደነቀች፡ ከአርዌው፡በኋላ። *ም፡ ፲፯፡ ፰፡፡

፬፡ ለአርዌው፡ሥልጣን፡ ለሰጠውም፡ ለዘንደው፡ ሰገዱ፡ ለአርዌውም፡ ሰገዱ፡ እንዲህ፡ ሲሉ። አርዌውን፡ማን፡ይመስለዋል። ማን፡ ይችላል፡ ከርሱ፡ ጋራ፡ ይዋጋ፡ ዘንድ።

፭፡ *አፍም፡ተሰጠው፡ በታላቅ፡ ነገርና፡ በስድብ፡ የሚናገር። ሥልጣንም፡ ተሰጠው፡ ያደርግ፡ ዘንድ፡ †አርባ፡ ሁለት፡ወር። *ዳን፡ ፯፡ ፰፡ ፲፩፡፡ ፪፡ ተሰ፡ ፪፡ ፬፡፡
†ራእ፡ ፲፩፡ ፪፡፡

፮፡ አፉንም፡ከፈተ፡እግዚአብሔርን፡ ለመስደብ፡ ስሙንስ፡ይሰድባል፡ ማደርያውንም፡ በሰማይም፡ የሚኖሩትን።

፯፡ ከቅዱሳን፡ጋራም፡ ሰልፍ፡ያደርግ፡ ዘንድ፡ *ተሰጠው፡ያሸንፋቸውም፡ዘንድ፡ሥልጣንም፡ተሰጠው፡ በዘመድ፡ሁሉ፡በቋንቋም፡በወገንም። *ም፡ ፲፩፡ ፯፡፡
ዳን፡ ፯፡ ፳፩፡፡

፰፡ በምድር፡ *ላይም፡ ያሉ፡ ሁሉ፡ ይሰግዱለታል፡ ስማቸው፡ †ያልተጻፈ፡ ዓለም፡ **ሳይፈጠር፡ በታረደው፡ በበጉ፡ ሕይወት፡ መጽሐፍ። *ም፡ ፲፪፡ ፲፪፡፡
†ም፡ ፫፡ ፭፡፡ **ም፡ ፲፯፡ ፰፡፡

፱፡ ማንም፡ ጆሮ፡ ያለው፡ እንደሆን፡ ይስማ።

፲፡ ማንም፡ ወደ፡ አሥር፡ የሚያግዝ፡ ወደ፡ አሥር፡ ይገባል። *ማንም፡ በሰይፍ፡ ገድሉ፡ እንደሆን፡ ይገበዋል፡በሰይፍ፡ይሞት፡ ዘንድ። †ከዚህ፡ ነው፡ የቅዱሳን፡ትዕግሥት፡ሃይማኖታቸውም። *ዘፍ፡ ፱፡ ፮፡፡
ኢሳ፡ ፴፫፡ ፩፡፡ ማቴ፡ ፳፮፡ ፶፪፡፡ †ራእ፡ ፲፬፡ ፲፪፡፡

፲፩፡ ሌላም፡አርዌ፡ከምድር፡ ሲወጣ፡ አየሁ። ሁለት፡ ቀንዶችም፡ ነበሩት፡ እንደ፡ *በግ፡ ቀንዶች፡ እንደ፡ ዘንደውም፡ ይናገር፡ ነበር። *ም፡ ፲፮፡ ፲፫፡፡
ማቴ፡ ፯፡ ፲፭፡፡ ና፡ ፳፬፡ ፳፬፡፡

፲፪፤ የፊተኛውንም፡አርዌ፡ሥልጣን፡ሁሉ፡በፊቱ፡ ያደርጋል ። ምድርንም፡ በርስዋም፡ የሚኖሩን፡ ለፊተኛው፡ አርዌ፡ እንዲሰግዱ፡ ያደርጋል፡ የሞቱ፡ ቍስል፡ለተፈወሰችው። ቍ፡ ፪፤ ፬፤ ፭፤ ፯።

፲፫፤ ታላቅ፡ *ተአምራትም፡ ያደርጋል፡ ከሰማይ፡ በምድር፡ላይ፡እሳት፡ እስኪያወርድ፡ ድረስ፡ በሰው፡ ፊት። *ማቴ፡ ፳፬፤ ፳፬። ፪፤ ተሰ፡ ፪፤ ፱። ፩፤ ነገሥ፡ ፲፰፤ ፴፰።

፲፬፤ በምድር፡የሚኖሩትንም፡ ያታላል፡ በተሰጠችው፡*ተአምራት፡ በአርዌው፡ ፊት፡ ያደርጋት፡ ዘንድ። በምድር፡ ላይ፡ የሚኖሩትን፡ ሲል፡ የአርዌውን፡ መልክ፡ ያደርጉ፡ዘንድ፡ የሰይፍ፡ ቍስል፡ ያለበቱ፡ የዳነውም። *ዘዳግ፡ ፲፫፤ ፩።

፲፭፤ ለአርዌውም፡መልክ፡ ነፍስ፡ያገባለት፡ ዘንድ፡ ተሰጠው፡የአርዌው፡ መልክ፡ ደግሞ፡ እንዲናገር። ያደርግም፡ዘንድ፡ ለአርዌው፡ መልክ፡ የማይሰግድ፡ ሁሉ፡እንዲሞት።

፲፮፤ ሁሉንም፡አደረገ፡ ታላቁን፡ ታናሹንም፡ ባለጠጎችንም፡ድኆችንም፡ የሰው፡ ልጆችንም፡ ገሮችንም፡ *ምልክት፡ እስኪሰጣቸው፡ ድረስ፡ በቀኝ፡ እጃቸው፡ ወይም፡ በግምባራቸው። *ም፡ ፲፱፤ ፳።

፲፯፤ ማንም፡መግዛትና፡መሸጥ፡እስኪሳነው፡ ድረስ፡ምልክት፡ ከሌለበት፡ ወይም፡ የአርዌው፡ ስም፡ወይም፡የስሙ፡ቍጥር።

፲፰፤ ከዚህ፡*ጥበብ፡ናት። እውቀት፡ ያለው፡ የአርዌውን፡ †ቍጥር፡ ይቍጠር፡ የሰው፡ ቍጥር፡ ነውና። ቍጥሩም፡ ስድስት፡ መቶ፡ ስድሳ፡ ስድስት፡ ነው። *ም፡ ፲፯፤ ፱። †ም፡ ፲፭፤ ፪።

## ምዕራፍ፡ ፲፬፤

፩፤ አየሁም፡ እነሆም፡ በግ፡ በጽዮን፡ ተራራ፡ ላይ፡ *ቁሞ፡ከርሱም፡ጋራ፡ መቶ፡ አርባ፡ አራት፡ ሺህ፡ ያባቱም፡ †ስም፡ በግምባራቸው፡ ተጽፎዋል። *ም፡ ፯፤ ፬፤ ፱። †ም፡ ፫፤ ፲፪።

፪፤ ከሰማይም፡ድምጽን፡ ሰማሁ፡እንደ፡ብዙ፡ ውኆች፡ ድምጽ፡ እንደ፡ ታላቅ፡ ነጐድጓድም፡ ድምጽ። መሰንቆ፡የሚመቱትንም፡ድምጽ፡ ሰማሁ፡ በመሰንቋቸው፡ ሲደረድሩ። ም፡ ፩፤ ፲፭።

፫፤ እንደ፡ዲስ፡ምስጋናም፡ያለውን፡በዙፋኑ፡ፊት፡ ግራቱ፡ እንስሶችና፡ በቀሳውስቱም፡ ፊት፡ አዘመሩ። ማንም፡ያችን፡ዝማሬ፡ይማር፡ዘንድ፡አይቻለውም፡ ከምድር፡ዘንድ፡ከተዋጁ፡ከመቶ፡አርባ፡አራት፡ ሺህ፡ በቀር። ም፡ ፭፤ ፱።

፬፤ እሌህ፡ናቸው፡ ከሴቶች፡ ጋራ፡ ያልረከሱ፡ *ድንግሎች፡ናቸውና፡ በጉንም፡ ወደሚሔድበት፡ ሁሉ፡ የሚከተሉት፡ እሌህ፡ ናቸው። እሌህ፡ ከሰዎች፡ †ተዋጁ፡ ቀዳማያት፡ ሁነው፡ ለእግዚአብሔር፡ ለበጉም። *፪፤ ቆሮ፡ ፲፩፤ ፪። ኤፌ፡ ፭፤ ፳፯። †ም፡ ፭፤ ፱።

፭፤ ባፋቸውም፡አበት፡ አልተገኘም። በእግዚአብሔር፡ ዙፋን፡ፊት፡ያለ፡ ነውር፡ ናቸውና።

፮፤ ሌላም፡ *መልአክ፡ አየሁ፡ በሰማይ፡ መካከል፡ ሲበር፡ የዘላለሙንም፡ ወንጌል፡ ይዞዋል፡ በምድር፡ ለሚኖሩት፡ ይሰብክ፡ ዘንድ፡ ለሕዝብና፡ ለአሕዛብም፡ለቋንቋንም፡ ለወገንም፡ ሁሉ። *ም፡ ፰፤ ፲፫።

፯፤ በታላቅ፡ቃል፡እንዲህ፡ሲል። እግዚአብሔርን፡ ፍሩ፡*ምስጋናም፡ ስጡት፡የሚፈርድባት፡ ጊዜ፡ መጥታለችና። ሰማይንና፡ ምድሩንም፡ †ለፈጠረ፡ ስገዱ፡ ባሕሩንም፡ የውኃውንም፡ ምንጮች። *ዘዳግ፡ ፴፪፤ ፫። †የሐዋ፡ ፲፬፤ ፲፭።

፰፤ ሌላውም፡ መልአክ፡ ተከተለው፡ እንዲህ፡ ሲል።*ወደቀች፡ ወደቀች፡ታላቂቱ፡ አገር፡ባቢሎን። የዝሙትዋን፡ ቍጣ፡ ጸጅ፡ አሕዛብን፡ ሁሉ፡ አጠጥታለችና። *ም፡ ፲፰፤ ፪። ኢሳ፡ ፳፩፤ ፱። ኤር፡ ፶፩፤ ፰።

፱፤ ሦስተኛውም፡ መልአክ፡ ተከተላቸው፡ በታላቅ፡ቃል፡ እንዲህ፡ሲል። ማንም፡ ለአርዌው፡ ቢሰግድ፡ ለሥእሉም፡ ምልክቱንም፡ የሚወስድ፡ በግምባሩ፡ ወይም፡ *በጁ። ም፡ ፲፫፤ ፲፪፤—፲፯።

፲፤ ይህ፡ ከእግዚአብሔር፡ ቍጣ፡ ጸጅ፡ ይጠጣል፡ ሰይደበለቅ፡በቍጣው፡ጽዋ፡*የተቀዳውን። በሳትና፡ በዲንም፡በቅዱሳን፡መላእክት፡ፊት፡በበጉም፡ ፊት፡ †ይሣቀያል። *ም፡ ፲፮፤ ፲፱። ኤር፡ ፳፭፤ ፲፭። *ም፡ ፲፱፤ ፳።

፲፩፤ የሥቃያቸውም፡ ጢስ፡ ለዘላለምና፡ ዘላለምና፡ይወጣል።ዕረፍትም፡ የላቸውም፡ በቀንና፡ በሌት፡ ለአርዌው፡ለሚሰግዱ፡ለሥእሉም፡ ማንም፡ የስሙን፡ ምልክት፡ ቢወስድ። ም፡ ፲፱፤ ፫።

፲፪፤ ከዚህ፡ነው፡ የቅዱሳን፡*ትዕግሥት፡ የእግዚአብሔርን፡ ትእዛዝ፡ †የሚጠብቁ፡ የየሱስንም፡ ሃይማኖት። *ም፡ ፲፫፤ ፲። †ም፡ ፲፪፤ ፲፯።

፲፫፤ ከሰማይም፡ ቃልን፡ ሰማሁ፡ እንዲህ፡ የሚለኝን። ጻፍ። በጌታ፡ የሚሞቱ፡ ብፁዓን፡ ናቸው፡ ካሁን፡ ጀምረው። አዎን። መንፈስ፡ ይላል። ከድካማቸው፡ *ያርፉ፡ ዘንድ ፡ †ምግባራቸውም ፡ ትከተላቸዋለች። *ኢሳ፡ ፶፯፤ ፩፤ ፪። †ዕብ፡ ፬፤ ፲።

፲፬፤ አየሁም፡ እነሆም፡ *ነጭ፡ደመና፡ በደመናው፡ ላይም፡ ተቀምጦዋል፡ የሰው፡ ልጅ፡ የሚመስል። በራሱ፡ላይም፡ የወርቅ፡አክሊል፡ ነበረበት፡ በጁም፡ †የተሳለ፡ ማጭድ፡ ይዞ፡ ነበረ። *ዳን፡ ፯፤ ፲፫። †ማቴ፡ ፲፫፤ ፴፱፤ ፵፩።

፲፭፤ ሌላም፡ መልአክ፡ ከመቅደስ፡ ወጣ፡በታላቅ፡ ቃል፡ *ሲጮህ፡ በደመና፡ ላይ፡ ለተቀመጠው። ማጭድህን፡ ስደድና፡ እጭድ፡ የመከር፡ ጊዜ፡ ደርሳልሃለችና፡የምድሩ፡እህል፡ደርቋልና። *ኢዮ፡ ፫፤ ፲፰።

፲፮፤ በደመና፡ ላይ፡ የተቀመጠውም፡ ማጭዱን፡ በምድር፡ ላይ፡ አደረገ፡ ምድሪቱም፡ ታጨደች።

፲፯፤ ሌላውም፡ መልአክ፡ ከሰማይ፡ ካለው፡ መቅ

ደስ፡ ወጣ፡ ከርሱ፡ ጋራም፡ ደግሞ፡ የተሳለ፡ ማጭድ፡ አለ።

፲፰፡ ሌላውም፡ መልአክ፡ ከመሠውያው፡ ወጣ፡ እርሱም፡ በእሳት፡ ታዝዋል፡ በታላቅ፡ ጩኸትም፡ጩ ኸ፡የተሳለ፡ ማጭድ፡ ለያዘው፡ እንደዬህ፡ ሲል። የተሳ ለውን፡ማጭድህን፡ስደድ፡ የምድሩንም፡ ዘለላ፡ ቍ ረጥ፡ወይኑ፡ በሰልዋልና።

፲፱፡ መልአኩም፡ ማጭዲን፡ በምድር፡ አደረገ፡ የ ምድሩንም፡ወይን፡ ቈረጠ፡ በታላቁም፡ በእግዚአብ ሔር፡*ቍጣ፡መጥመቂያ፡ጣለው። *ም፡ ፲፱፡ ፲፭።

፳፡ *መጥመቂያውም ፡ ተረገጠ ፡ ካገር ፡ በሚ ከመጥመቂያውም፡ደም፡ ወጣ፡ወደ፡ፈረሱ፡ልጓም፡ እስኪደርስ፡ ወደ፡ ሺህ፡ ከስድስት፡ መቶ፡ ምዕራፍ። *ኢሳ፡ ፷፫፡ ፫።

## ምዕራፍ፡ ፲፭፡

፩፡ *ሌላ፡ምልክትም፡ በሰማይ፡አየሁ፡ የበለጠች፡ የተደነቀችም።ሰባት፡መላእክት፡ከርሳቸውም፡ጋራ፡ የኋለኞቹ፡ሰባት፡ መቅሠፍት። በለዚህ፡ የእግዚአ ብሔር፡ ቍጣ፡ ይፈጸማልና። *ም፡ ፲፪፡ ፩፡ ፫። *ም፡ ፲፩፡ ፲፰።

፪፡ *አየሁ፡ እንደ፡ብርጭቆ፡ ባሕርም፡ በእሳት፡ ተ ቀላቅሎ። አርዌውንም፡ ድል፡ †የነሡ፡ ምሳሌውን ም፡ መልኩንም፡ የስሙንም፡ ቍጥር፡ በብርጭቆ፡ ባ ሕር፡ ላይ፡ ቆመው። ከርሳቸውም፡ ጋራ፡ የእግዚአብ ሔር፡ **መሰንቆች፡ ነበሩ። *ም፡ ፬፡ ፮። †ም፡ ፲፫፡ ፲፭፡ ፲፯። **ም፡ ፭፡ ፰።

፫፡ የእግዚአብሔርንም፡ ባርያ፡ *የሙሴን፡ ምስጋ ና፡ያመሰግናሉ፡†የበጉንም፡ ምስጋና፡ እንደዬህ፡ ሲሉ። ሥራህ፡ታላቅ፡ናት፡ድንቅም፡ናት፡አምላክ፡ሆይ፡ጌታ፡ ሁሉን፡ የምቲዝ። መንገድህ፡ የቀናች፡ እውነተኛም፡ ናት፡ የቅዱሳን፡ ንጉሥ፡ ሆይ። *ዘፀአ፡ ፲፭፡ ፩፡ ፲፩። መዝ፡ ፻፵፭፡ ፲፯። †ም፡ ፭፡ ፱፡ ፲፪።

፬፡ ማነው፡ የማይፈራህ፡ አቤቱ፡ ስምህንስ፡ የማ ያመሰግን። አንተ፡ ብቻ፡ ቅዱስ፡ ነህና። *አሕዛብ፡ሁ ሉ፡መጥተው፡ በፊትህ፡ይሰግዳሉና፡ ፍርድህ፡ ስለ፡ ተ ገለጠ። *መዝ፡ ፹፮፡ ፱።

፭፡ ከዚህም፡ በኋላ፡ አየሁ፡ *እነሆም፡ የደብተራ፡ ስምዕ፡መቅደስ፡በሰማይ፡ተከፈተ። *ም፡ ፲፩፡ ፲፱።

፮፡ ሰባቱ፡መላእክትም፡ሰባት፡መቅሠፍት፡ የያዙ ት፡ ከመቅደስ፡ ወጡ፡ *ነጭ፡ የተልባግር፡ ለብሰው፡ የ ሚያበራ። በወርቅ፡ መታጠቂያም፡ በደረታቸው፡ ታ ጥቀው። ም፡ ፩፡ ፲፫።

፯፡ ካራቱ፡ እንስሶችም፡ *አንዱ፡ ለሰባቱ፡ መላእ ክት፡ ሰባት፡ የወርቅ፡ጽዋ፡ሰጠ፡ የዘላለሙን፡ ሕያው፡ የእግዚአብሔርን፡ †ቍጣ፡ የመላች። *ም፡ ፬፡ ፮፡—፰። †ም፡ ፲፬፡ ፲።

፰፡ በመቅደሱም፡ ጢስ፡መላበት፡ ከእግዚአብሔ ር፡ *ክብር፡ የተነሣ፡ ከችሎቱም። ማንም፡ወደ፡ መቅ ደስ፡ይገባ፡ ዘንድ፡ አልቻለም፡ የሰባቱ፡ መላእክት፡ ሰ ባቲቱ፡ መቅሠፍት፡ እስክትፈጸም፡ ድረስ። *ዘፀአ፡ ፵፡ ፴፬። ነገሥ፡ ፰፡ ፲። ኢሳ፡ ፮፡ ፬። ሕዝ፡ ፵፬፡ ፬።

## ምዕራፍ፡ ፲፮፡

፩፡ ታላቅ፡ድምጽም፡ከመቅደስ፡ ሰማሁ፡ ሰባቱን፡ መላእክት፡ እንደዬህ፡ ሲል። ሒዱና፡ የእግዚአብሔር ን፡የቍጣውን፡*ጽዋ፡ በምድር፡ ላይ፡ አፍሱ። *ም፡ ፲፭፡ ፯።

፪፡ የፊተኛውም፡ ሔደ፡ ጽዋውንም ፡ አፈሰሰ፡ በ ምድር፡ላይ።*ክፉም፡ቍስል፡ሆነ፡ርኩስም፡በሰዎች፡ ላይ፡ የአርዌው፡ ምልክት፡ ባለቸባቸው፡ ለምሳሌው ም፡ በሚሰግዱ። *ዘፀአ፡ ፱፡ ፲፡ ፲፩።

፫፡ ሁለተኛውም፡መልአክ፡ ጽዋውን፡አፈሰሰ፡ በባ ሕር፡ላይ፡ ደምም፡ ሆነ፡ እንደ፡ ሞተ፡ ደም፡ ሕይወት ም፡ያለው፡ነፍስ፡ሁሉ፡በባሕር፡ሞተ። ዘፀአ፡ ፯፡ ፲፯።

፬፡ ሦስተኛውም፡ መልአክ፡ ጽዋውን፡ አፈሰሰ፡ በ ፈሳሽ፡ ውኃ፡ በውኃውም፡ ምንጭ፡ ሁሉ፡ ላይ፡ *ደም ም፡ሆነ። *ዘፀአ፡ ፯፡ ፲፱፡—፳፬።

፭፡ የውኆችንም፡ መልአክ፡ ሲል፡ ሰማሁ። አንተ፡ ጻድቅ፡ነህ፡አቤቱ፡ የምትኖር፡ የነበርህም፡ የምትቀድ ስም፡ በዚህ፡ ፈርደሃልና።

፮፡ የቅዱሳንንና፡ የነቢያትን፡ ደም፡ አፍሰዋልና፡ ደምንም፡ ሰጠሃቸው፡ይጠጡ፡ ዘንድ፡ይገባቸዋልና።

፯፡ ሌላውንም፡*ከመሠዊያው፡ ሰማሁ፡እንደዬህ፡ ሲል። አዎን፡አቤቱ፡አምላክ፡ሆይ፡ሁሉን፡ የምቲዝ። ፍርድህ፡ †እውነትና፡ ቅን፡ ናት። *ም፡ ፱፡ ፲፫። †ም፡ ፲፱፡ ፪።

፰፡ አራተኛውም፡ መልአክ፡ ጽዋውን፡ አፈሰሰ፡ በ ጸሓይ፡ ላይ። ሰውንም፡ በሳት፡ ታቃጥል፡ ዘንድ፡ ተሰ ጣት።

፱፡ ሰዎችም፡ ታላቅ፡ መቃጠል፡ ተቃጠሉ፡ በዚህ፡ መቅሠፍትም፡ ሥልጣን፡ ያለውን፡ የእግዚአብሔር ን፡ስም፡*ሰደቡ፡ ንስሐም፡ †አልገቡም፡ ምስጋና፡ ለር ሱ፡ይሰጡ፡ዘንድ። *ቍ፡ ፺፩። †ም፡ ፱፡ ፳፡ ፳፩።

፲፡ አምስተኛውም፡ መልአክ፡ ጽዋውን፡ አፈሰሰ፡ በአርዌው፡ ዙፋን፡ ላይ ፡ መንግሥቱም፡ *ጨለመች፡ መላሳቸውንም ፡ ቀረጠሙ፡ ከማመሙ ፡ የተነሣ። *ዘፀአ፡ ፲፡ ፳፩። ኢሳ፡ ፰፡ ፳፩፡ ፳፪።

፲፩፡ የሰማይንም፡ አምላክ፡ ሰደቡ፡ ከመታመማ ቸው፡ የተነሣ፡ከቍስላቸውም፡ከስራቸውም፡ *አል ተመለሱም። *ም፡ ፱፡ ፳።

፲፪፡ ስድስተኛውም፡መልአክ፡ ጽዋውን፡ አፈሰሰ፡ በታላቁ፡በኤፍራጥስ፡ ወንዝ፡ ላይ፡ *ውኃውም፡ ደረ ቀ፡ መንገድ፡ ይጸረግላቸው፡ ዘንድ፡ ከጸሓይ፡ መው ጫ፡ ላሉት፡ ነገሥታት። *ኢሳ፡ ፲፩፡ ፲፭፡ ፲፮።

፲፫፡ *ከዘንዶውም፡ አፍ፡ †ከአርዌውም፡ አፍ፡ **ካሰተኛውም፡ ነቢይ፡ አፍ፡ ሦስት፡ **ርኩሳን፡ መ

ናፍስት፡ ሲወጡ፡ አየሁ፡ እንቊራሪትር፡ የሚመስሉ።
*ምዕ፡ ፲፱፡ ፲፡፡ †ምዕ፡ ፲፫፡ ፩፡፡ **ምዕ፡ ፲፫፡ ፲፩፡፡
††ዘፀአ፡ ፳፡ ፯፡ ና፡ ፩፡ ነገሥ፡ ፳፪፡ ፳፩፡፡

፲፬፡ የሰይጣናት፡ መናፍስት፡ ናቸውና፡ *ተአምራ ት፡ የሚያደርጉ፡ በምድር፡ ነገሥታት፡ ያልፋ፡ ዘንድ፡ በዓለምም፡ ሁሉ፡ይሰበስቡብዋቸው፡ዘንድ፡ ወደዚያ፡ ወደ፡ ታላቁ፡ ቀን፡ ሰልፍ፡ ሁሉን፡ የሚይዝ፡ †የእግዚ አብሔር፡ ቀን።
*ምዕ፡ ፲፫፡ ፲፫፡፡ †ምዕ፡ ፲፬፡ ፲፬፡፡

፲፭፡ እነሆ፡ እኔ፡ እንደ፡ሌባ፡ *እመጣለሁ። የሚተ ጋ፡ ብፁዕ፡ ነው፡ ልብሱንም፡ የሚጠብቅ፡ †ራቁቱን፡ እንደይሔድ፡ ኃፍረቱንም፡ እንደያዩ።
*፩፡ ተሰ፡ ፭፡ ፪፡፡ †ምዕ፡ ፫፡ ፲፰፡፡

፲፮፡ በዕብራይስጥ፡ ቋንቋ፡ *አርማጌዶን፡ ወደሚ ባል፡ ስፍራም፡ ሰበሰባቸው።
*መሳ፡ ፭፡ ፲፱፡ ፳፩፡፡
፪፡ ነገሥ፡ ፱፡ ፳፯፡፡ ና፡ ፳፫፡ ፳፱፡፡ ዘካ፡ ፲፪፡ ፲፩፡፡

፲፯፡ ሰባተኛውም፡ መልአክ፡ጽዋውን፡ አፈሰሰ፡ በ አየር፡ ላይ፡ ታላቅ፡ ድምጽም፡ ከሰማይ፡ መቅደስ፡ ወጣ፡ ከዙፋኑ፡ እንዲህ፡ ሲል። ፈጽሞ፡ ሆነ።

፲፰፡ ድምጽም፡ ነጐድጓድም፡ መብረቅም፡ ሆነ፡ ታላቅ፡ መናወጥም፡ ነበረ። ሰውም፡ በምድር፡ ላይ፡ ከተፈጠረ፡ጀምሮ፡ መናወጥ፡ አልሆነም፡ እንዲህ፡ ታ ላቅ፡ እንደርሱ።
ምዕ፡ ፱፡ ፭፡፡ ና፡ ፳፡ ፭፡ ፲፩፡ ፲፱፡፡

፲፱፡ ታላቂቱም፡ *አገር፡ ለሦስት፡ክፍል፡ ሆነች፡ የአ ሕዛብም፡ ከተሞች፡ ወደቁ፡ ታላቂቱም፡ ባቢሎን፡ በ እግዚአብሔር፡ ፊት፡ ታሰበች፡ የመቅሠፍቱን፡ ቍ ጣ፡ ወይን፡ †ጽዋ፡ ይሰጣት፡ ዘንድ።
*ምዕ፡ ፲፩፡ ፳፡፡
†ምዕ፡ ፲፬፡ ፲፡፡

፳፡ ደሴትም፡ ሁሉ፡ ሸሸች፡ ተራሮችም፡ አልተገኙ ም።
ምዕ፡ ፮፡ ፲፬፡፡ ና፡ ፳፡ ፲፩፡፡

፳፩፡ ታላቅ፡ *በረዶም፡ እንደ፡ ሚዛን፡ አዋቂ፡ ያለ፡ ከሰማይ፡ ወረደ፡ በሰዎች፡ ላይ። ሰውም፡ እግዚአብ ሔርን፡ †ሰደበ፡ ከበረዶው፡ መቅሠፍት፡ የተነሣ፡ መ ቅሠፍቱ፡ እጅግ፡ ታላቅ፡ ነበረና።
*ዘፀአ፡ ፱፡ ፳፫፡፡
†ቍ፡ ፱፡፡

## ምዕራፍ፡ ፲፯፡

፩፡ ከሰባቱም፡ መላእክት፡ ሰባት፡ ጽና፡ ይዘው፡ ከ ነበሩት፡ አንዱ፡ መጣ፡ ከኔ፡ ጋራም፡ ተናገረ፡ እንዲህ፡ ሲለኝ። ና፡ የታላቂቱን፡ ጋለሞታ፡ ኩነኔ፡ አሳይህ፡ በብ ዙ፡ ወኖች፡ ላይ፡ የተቀመጠችውን።
ምዕ፡ ፲፭፡ ፩፡፡

፪፡ ከርሰዋ፡ ጋራ፡ ያመነዘሩ፡ የምድር፡ ነገሥታት፡ በ ምድርም፡ የሚኖሩ፡ ከምንዝርዋ፡ ወይን፡ *የሰከሩ።
*ምዕ፡ ፲፬፡ ፰፡፡ ኤር፡ ፶፩፡ ፯፡፡

፫፡ በመንፈስም፡ ወደ፡ ምድረ፡ በዳ፡ ይዞኝ፡ ሔደ፡ ሴትም፡ አየሁ፡ በቀይ፡አርዌ፡ ተቀምጣ፡ የስድብ፡ ስ ም፡ በመላበት። ለርሱም፡ *ሰባት፡ ራስ፡አሥር፡ቀንደ ችም፡ አሉት።
*ምዕ፡ ፲፫፡ ፩፡፡

፬፡ *ሴቲቱም፡ በቀይ፡ ሐርና፡ በነጭ፡ ሐር፡ ተጐናጽ ፋ፡ ነበረች፡ በወርቅና፡ በዕንቍ፡ በከበረም፡ ደንጊያ፡ በተሰራ። በጅዋም፡ የወርቅ፡ *ጽዋ፡ ይዞ፡ ነበረች፡ እ ድፍ፡ የምንዝርዋም፡ ርኵሰት፡ የመላበት።
*ሕዝ፡ ፳፰፡ ፲፫፡ ፲፮፡፡ †ኤር፡ ፶፩፡ ፯፡፡

፭፡ በግምባርዋም፡ ስም፡ ተጽፎዋል። *ምሥጢ ር። †ታላቂቱ፡ ባቢሎን። የጋለሞቶች፡ እናት፡ የምድ ርም፡ርኵሰት፡ሁሉ።
*፪፡ ተሰ፡ ፪፡ ፯፡፡ †ራእ፡ ፲፬፡ ፰፡፡
ና፡ ፲፰፡ ፲፱፡፡ ዳን፡ ፬፡ ፳፯፡፡

፮፡ ሴቲቱንም፡ ሰክራ፡ አየሁ፡ ከቅዱሳን፡ደም፡ ከ የሱስም፡ ሰማዕታት፡ደም። ባየኋትም፡ ጊዜ፡ ታላቅ፡ ድንቅ፡ ተደነቅሁ።
ምዕ፡ ፲፰፡ ፳፬፡፡

፯፡ መልአኩም፡አለኝ። ለመን፡ ትደነቃለህ። እኔ፡ የሴቲቱን፡ ምሥጢር፡ እነግርሃለሁ፡ የተሸከማትን ም፡ አርዌ፡ ሰባት፡ ራስ፡ አሥር፡ቀንዶችም፡ ያሉትን።

፰፡ ያየኸው፡ አርዌ፡ እርሱ፡ *ነበረ፡ እርሱም፡ †አ ይደለም፡ ከቀላይም፡ ይወጣ፡ ዘንድ፡ ጊዜ፡ አለው፡ ወደ፡ ጥፋትም፡ ይሔድ፡ ዘንድ። በምድር፡ የሚኖሩ ም፡ ይደነቃሉ፡ ስማቸው፡ †በሕይወት፡ መጽሐፍ፡ ያ ልተጻፈ፡ ዓለም፡ ሳይፈጠር። አርዌውን፡ አይተው፡ የነበረውን፡ ያይደለውንም፡ ምንስ፡ እርሱ፡ ቢሆን።
*ምዕ፡ ፲፫፡ ፩፡ ፪፡፡ †ምዕ፡ ፲፫፡ ፫፡፡ **ምዕ፡ ፫፡ ፭፡፡

፱፡ ከዚህ፡ *ጥበብ፡ ያለው፡ አእምሮ፡ አለ። †ሰባ ቱ፡ ራሶች፡ ሰባት፡ ተራሮች፡ ናቸው፡ ሴቲቱ፡ ተቀምጣ ባቸው፡ ያለች።
*ምዕ፡ ፲፫፡ ፲፰፡፡ †ምዕ፡ ፲፫፡ ፩፡፡

፲፡ እርሳቸውም፡ ሰባት፡ ነገሥታት፡ ናቸው። አም ስቱ፡ወደቁ፡አንዱም፡አለ። ሌላውም፡ገና፡አልመጣ ም። ቢመጣም፡ ጥቂት፡ ይቀመጥ፡ ዘንድ፡ይገባዋል።

፲፩፡ የነበረውም፡ አርዌ፡ እርሱም፡ያይደለውም። እርሱ፡ ስምንተኛ፡ ነው፡ ከሰባቱም፡ ነው፡ ወደ፡ *ጥፋ ትም፡ ይሔዳል።
*ቍ፡ ፰፡፡ ምዕ፡ ፲፱፡ ፳፡፡

፲፪፡ *አሥሩም፡ ቀንዶች፡ ያየሃቸው፡ እርሳቸው፡ አሥር፡ ነገሥታት፡ ናቸው፡ ገና፡ መንግሥት፡ ያልወሰ ዱ። ነገር፡ግን፡ሥልጣን፡ ይወስዳሉ፡እንደ፡ ነገሥታት፡ አንዲት፡ ሰዓት፡ ከአርዌው፡ ጋራ።
*ምዕ፡ ፲፫፡ ፩፡፡
ዳን፡ ፯፡ ፳፡ ፳፬፡፡

፲፫፡ ለለዚህ፡ አንድ፡ ምክር፡ አላቸው፡ ኃይላቸው ንም፡ ሥልጣናቸውንም፡ የአርዌው፡ ይሰጣሉ።

፲፬፡ እሌህ፡ ከበጉ፡ ጋራ፡ ይዋጋሉ፡ በጉም፡ ያሸንፋ ቸዋል፡ *የጌቶች፡ ጌታ፡ ነውና፡ የነግሥታትም፡ ንጉሥ፡ ከርሱም፡ ጋራ፡ ያሉት፡ †የተጸሩ፡ ናቸው፡ የተመረጹ ም፡ ያመኑም።
*ምዕ፡ ፲፱፡ ፲፮፡፡ †ምዕ፡ ፲፱፡ ፲፬፡፡

፲፭፡ አለኝም። ገለሞቱ፡ተቀምጣባቸው፡ ያየሃቸ ው፡ *ውኆች፡ †ሕዝብና፡ አሕዛብ፡ ናቸው፡ ወገኖች ም፡ ቋንቋችም።
*ቍ፡ ፩፡፡ †ኢሳ፡ ፰፡ ፯፡፡
ኤር፡ ፵፯፡ ፪፡፡

፲፮፡ አሥሩም፡ ቀንዶች፡ በአርዌው፡ ላይ፡ ያየሃቸ ው፡ እርሳቸው፡ ጋለሞቱን፡ *ይጸላሉ፡ ፍቹም፡ራቁት ዋንም፡ የሚያደርጓት፡ ጊዜ፡ አላቸው፡ ሥጋዋንም፡ ይበልዋታል፡ †በእሳትም፡ ያቃጥልዋታል።
*ቍ፡ ፲፪፡ ፲፫፡፡ †ምዕ፡ ፲፰፡ ፰፡፡

፲፯፤ እግዚአብሔር፡ በልባቸው፡ አድርጓልና፡ ምክሩን፡ ያደርጉ፡ ዘንድ፡ አንድ፡ ምክርም፡ ያደርጋሉ፡ መንግሥታቸውንም፡ለአርዌው፡ ይሰጣሉ፡የእግዚአብሔር፡ ቃል፡ እስኪፈጸም፡ ድረስ። ም፡ ፲፡ ፯።

፲፰፤ ያየሃትም፡ ሴት፡ እርሷ፡*ታላቂቱ፡ አገር፡ ናት፡ መንግሥት፡ ያላት፡ በምድር፡ ነገሥታት፡ ላይ። *ም፡ ፲፯፡ ፲።

## ምዕራፍ፡ ፲፰፤

፩፤ ከዚህም፡ በኋላ፡ ሌላ፡ መልአክ፡ አየሁ፡ ከሰማይ፡ *ሲወርድ፡ ለርሱም፡ ታላቅ፡ ሥልጣን፡ አለው፡ †ምድርም፡ አበራች፡ ከብርሃኑ፡ የተነሣ። *ም፡ ፲፡ ፩። †ሕዝ፡ ፵፫።

፪፤አበርትተም፡ጮኸ፡በታላቅ፡ቃል፡እንዲህ፡ሲል። *ወደቀች፡ ወደቀች፡ ታላቂቱ፡ ባቢሎን፡ ለሰይጣናትም፡ ተማደርያ፡ ሆነች። ለርኩስ፡ መንፈስ፡ ሁሉም፡ መጠበቂያ፡ ሆነች፡ ርኩስ፡ ወፍም፡ ሁሉ፡ የተጸላም፡ የሚያድርባት፡ ሆነች። *ም፡ ፲፬፡ ፰። ኢሳ፡ ፳፩፡ ፱። ኤር፡ ፶፩፡ ፰። †ኢሳ፡ ፲፫፡ ፳፩። ና፡ ፴፬፡ ፲፩፡ ፲፫። ኤር፡ ፶፡ ፫፡ ፴፱፡ ፵።

፫፤ አሕዛብ፡ ሁሉ፡ ከምንዝርዋ፡ ቍጣ፡ *ወይን፡ ጠጥተዋልና፡ የምድርም፡ ነገሥታት፡ ከርስዋ፡ ጋራ፡ አመነዘሩ፡ የምድርም፡ ነጋዴች፡ ከተድላዋ፡ ብዛት፡ ባለጠጎች፡ ሆኑ። *ኤር፡ ፶፩፡ ፯። ናሆ፡ ፫፡ ፬።

፬፤ ሌላ፡ ቃልም፡ ሰማሁ፡ ከሰማይ፡እንዲህ፡ሲል። ከርሰዋ፡ *ውጡ፡ ወገኖቼ፡ ሆይ፡ በኃጢአትዋ፡ እንዳትገኙ፡ ከመቅሠፍትዋም፡ እንዳትወሰዱ። *ኢሳ፡ ፵፰፡ ፳። ና፡ ፶፪፡ ፲፩። ኤር፡ ፶፡ ፰። ና፡ ፶፩፡ ፮፡ ፵፭።

፭፤ ኃጢአትዋ፡ እስከ፡ *ሰማይ፡ ተከትለዋታልና፡ እግዚአብሔርም፡ ግፍዋን፡ አሰበው። *ዘፍ፡ ፲፰፡ ፳። ኤር፡ ፶፩፡ ፱።

፮፤ *ተበቀልዋት፡ እርስዋ፡ ደግሞ፡ እንደ፡ ተበቀለቻችሁ፡ ደግማችሁም፡ ዉምሩላት፡ እንደ፡ስራዋ። በመላችው፡ጽዋ፡ እላንትም፡ አብልጣችሁ፡ምሉላት። *መዝ፡ ፻፴፯፡ ፰። ኤር፡ ፶፡ ፲፭፡ ፳፱።

፯፤ ራስዋን፡ *እንዳከበረች፡ ደስም፡ እንዳላት፡ በዚያ፡ልክ፡ሥቃይ፡ ልቅሶም፡ ስጥዋት። በልብዋ፡ ትላለችና። †ንግሥት፡ ሁኜ፡ እቀመጣለሁ፡ ድኃም፡ አልሆንም፡ ልቅሶም፡ አላይም። *ኤር፡ ፶፡ ፳፱። †ኢሳ፡ ፵፯፡ ፯፡ ፰።

፰፤ ስለዚህም፡ *ባንድ፡ ቀን፡ መቅሠፍትዋ፡ ይመጣል፡ ሞት፡ ልቅሶም፡ ራብም፡ †በእሳትም፡ ትቃጠላለች። እግዚአብሔር፡ አምላክ፡ የሚፈርድባት፡ ብርቱ፡ ነውና። *ኢሳ፡ ፵፯፡ ፱። ኤር፡ ፶፡ ፴፩። †ራእ፡ ፲፯፡ ፲፮።

፱፤ የምድርም፡ ነገሥታት፡ ያለቅሱላታልና፡ ወይ፡ ይሉላታል፡ ከርስዋ፡ ጋራ፡ *ያመነዘሩ፡ ደስታም፡ ያደረጉ፡ የመቃጠልዋን፡ ጢስ፡ ባዩ፡ ጊዜ። *ም፡ ፲፯፡ ፪።

፲፤ ከሥቃይዋ፡ ፍርሃት፡ የተነሣ፡ በሩቅ፡ ቁመው፡ እንዲህ፡ ሲሉ። *ወዮላት፡ ወዮላት፡ ለታላቂቱ፡ አገር፡ ለባቢሎን፡ ለብርቱዪቱ፡ አገር፡ ባንዲት፡ሰዓት፡ ኩነኔ፡ መጥትዋልና። *ም፡ ፲፬፡ ፰። ኢሳ፡ ፳፩፡ ፱። ኤር፡ ፶፩፡ ፰።

፲፩፤ የምድርም፡ ነጋዴች፡ ስለርስዋ፡ ያለቅሳሉና፡ ወይ፡ ይላሉ፡ሸያጫቸውን፡ ከዚያ፡ ወዲያ፡ የሚገዛት፡ የለምና። ቍ፡ ፲፰። ሕዝ፡ ፳፯፡ ፴፮።

፲፪፤ የወርቅ፡ እቃ፡ የብርም፡ የዕንቍም፡የሉልም፡ የቢሰም፡ ቀይ፡ ሐርም፡ ነጭ፡ ሐርም፡ ብጫ፡ ሐርም፡ የሽቱ፡ እንጨትም፡ ሁሉ፡ የዝሆን፡ ጥርስም፡ እቃ፡ ሁሉ፡ የከበረም፡ እንጨት፡ሁሉ፡ ናስም፡ ብረትም፡እብነ፡ በረድም። ሕዝ፡ ፳፯፡ ፲፪፡ ፲፫፡ ፳፪።

፲፫፤ቀረፋም፡ዕጣንም፡ቅቤንም፡ምስክም፡የወይን፡ ጸጅም፡ ዘይትም። የከበረም፡ ዱቄት፡ ስንዴም፡ ላምም፡ በግም፡ ፈረስም፡ መንኰራኩርም፡ ባሮችም፡ የሰው፡ ነፍሳትም።

፲፬፤ የነፍስሽም፡ ፈቃድ፡ ፍሬ፡ ካንቺ፡ ተቈረጠ። ያመረም፡ የተወደደም፡ ሁሉ፡ካንቺ፡ ጠፋ። እንግዲህም፡ አታገኚውም።

፲፭፤ የዚህ፡ ሁሉ፡ ነጋዴች፡ከርስዋ፡ የከበሩ፡ርቀው፡ ይቆማሉ፡ ስለ፡ ሥቃይዋ፡ ፍርሃት፡ ኢያለቀሱና፡ ወይ፡ ኢያሉ፡ እንዲህም፡ ኢያሉ። ሕዝ፡ ፳፯፡ ፳፯፡ ፴፡ ፴፮።

፲፮፤ ወዮ፡ ወዮ፡ ለታላቂቱ፡ አገር፡ በብጫ፡ሐር፡ የምትጐናጸፍ፡ በቀይ፡ ሐርም፡ በነጭ፡ ሐርም። በወርቅም፡የተለቀለቀች፡*በዕንቍም፡በሉልም። †ባንዲት፡ ሰዓት፡ ይህ፡ ታላቅ፡ ባለጠግነት፡ ጠፍትዋልና። *ም፡ ፲፯፡ ፬። †ኢሳ፡ ፳፫፡ ፲፬።

፲፯፤ የመርከቡ፡*መሪም፡ ሁሉ፡*በመርከብም፡ የሚሔድ፡ ሰዎች፡ ሁሉ፡ መርከበኞችም፡ በባሕርም፡ የሚዞሩ፡ ሁሉ፡ በሩቅ፡ ቆሙ። *ሕዝ፡ ፳፯ ፳፯፡—፴፮።

፲፰፤ የመቃጠልዋንም፡ ጢስ፡ ባዩ፡ ጊዜ፡ ጮሁ፡ እንዲህ፡ ሲሉ። ምን፡ አገር፡ ይህቺን፡ ታላቅ፡ አገር፡ ይመስላታል። ኢሳ፡ ፴፬፡ ፲።

፲፱፤ በራሳቸውም፡ላይ፡ *አፈር፡ነሰነሱ፡ ኢያዘኑና፡ ኢያለቀሱ፡ ጮሁ፡ እንዲህ፡ ሲሉ። ወዮ፡ ወዮ፡ ለታላቂቱ፡ አገር፡ መርከብ፡ በባሕር፡ ያላቸው፡ ሁሉ፡ከክብርዋ፡ የከበሩባት። ባንዲት፡ሰዓት፡ ተፈትታለችና። *ሕዝ፡ ፳፯፡ ፳፬፡ ፴።

፳፤ ሰማይ፡ ሆይ፡ *ደስ፡ ይበልሽ፡ እላንትም፡ ቅዱሳን፡ ሆይ፡ ሐዋርያት፡ነቢያትም፡ እግዚአብሔር፡ፍርዳችሁን፡ በርስዋ፡ ላይ፡ ፈርደላችኋልና። *ኢሳ፡ ፵፬፡ ፳፫። ኤር፡ ፶፩፡ ፵፰።

፳፩፤ ብርቱ፡ መልአክም፡ *ደንጊያ፡ አነሣ፡ እንደ፡ ታላቅ፡ወፍጮ፡ያለ፡ በባሕርም፡ ጣለው፡ እንዲህ፡ ሲል። እንዲህ፡ ተገፍታ፡ ትወድቃለች፡ ታላቂቱ፡ አገር፡ ባቢሎን፡ደግሞም፡አትገኝም። *ኤር፡ ፶፩፡ ፷፫፡ ፷፬።

፳፪፡ *መሰንቆ፡የሚመቱም፡ድምጽ፡ ያዝማሮችም፡ መለከትም፡ የሚነፉ፡ ዝማሬም፡ የሚዘምሩ፡ እንግዲህ፡ አይሰማብሽም። ስራን፡ ሁሉ፡ የሚሰራም፡እንግዲህ፡ አይገኝብሽም። የወፍጮም፡ድምጽ፡ እንግዲህ፡አይሰማብሽም።

*ኢሳ፡ ፳፬፡ ፰። ሕዝ፡ ፳፮፡ ፲፫።

፳፫፡ የመብራትም፡ ብርሃን፡ እንግዲህ፡አይበራብሽም። የሙሽራና፡ *የሙሽራዪቱም፡ ድምጽ፡ እንግዲህ፡አይሰማብሽም። †ነጋዴችሽ፡የምድር፡ታላቆች፡ ነበሩና። ባስማትሽ፡ አሕዛብ፡ ሁሉ፡ ስተዋልና።

*ኤር፡ ፯፡ ፴፬። ና፡ ፲፮፡ ፱። ና፡ ፳፭፡ ፲። †ኢሳ፡ ፳፫፡ ፰።

፳፬፡ እርስዋም፡ ተገኘ፡ የነቢያትና፡የቅዱሳን፡*ደም፡ በምድር፡ ላይም፡ ተዋግተው፡ የሞቱ፡ ሁሉ።

*ም፡ ፮፡ ፲። ም፡ ፲፯፡ ፮። ና፡ ፲፱፡ ፪። ማቴ፡ ፳፫፡ ፴፭፡ ፴፮።

## ምዕራፍ፡ ፲፱፡

፩፡ ከዚህም፡ በኋላ፡ ታላቅ፡ *ድምጽ፡ ሰማሁ፡የብዙ፡ ጉባዔ፡ በሰማይ፡ የሚል። ሃሌሉያ። መድኃኒት፡ ምስጋናም፡ ክብርም፡ ኃይልም፡ ለእግዚአብሔር፡ ለምላካችን።

*ም፡ ፲፩፡ ፲፭።

፪፡ ፍርዱ፡ *እውነት፡ ቅንም፡ ነውና። ምድርን፡ በምንዝርዋ፡ ባጠፋች፡ በታላቂቱ፡ ጋለሞታ፡ ላይ፡ ፈርድዋልና። ለባሮቹም፡ †ደም፡ ከጅዋ፡ ተበቀለ።

*ም፡ ፲፮፡ ፯። †ም፡ ፮፡ ፲። ዘዳግ፡ ፴፪፡ ፵፫።

፫፡ ሁለተኛም፡ አሉ። ሃሌሉያ። *ጢስዋም፡ ለዘላለም፡ ይወጣል።

*ኢሳ፡ ፴፬፡ ፲።

፬፡ ሀያ፡ አራቱም፡ ሽማግሎች፡ አራቱም፡ እንስሶች፡ ወደቁ፡በዙፋኑ፡ላይም፡ለተቀመጠው፡ለእግዚአብሔር፡ሰገዱ፡ እንደህ፡ሲሉ። *አሜን። ሃሌሉያ።

*ም፡ ፭፡ ፲፬። መዝ፡ ፻፮፡ ፵፰።

፭፡ ከዙፋኑም፡ ድምጽ፡ ወጣ፡ እንደህ፡ ሲል። አምላካችንን፡ አመስግኑ፡ እላንተ፡ባሮቹ፡ ሁላችሁ። እርሱንም፡ የምትፈሩ፡ ታናናሾችም፡ ታላላቆችም።

፮፡ እንደ፡ ብዙ፡ ጉባዔም፡ ድምጽ፡ሰማሁ፡ እንደ፡ ብዙም፡ ውኆች፡ እንደ፡ ብርቱም፡ ነጐድጓድ፡ ድምጽ፡ ሲሉ። ሃሌሉያ። ሁሉን፡ የሚይዝ፡ እግዚአብሔር፡ አምላካችን፡ ነግሥዋልና።

ም፡ ፲፩፡ ፲፭፡ ፲፯።

፯፡ *ደስ፡ ይበለን፡ በብዙ፡ ደስታ፡ ምስጋናም፡እንስጠው። የበጉ፡ †ሰርግ፡ ደርሰዋልና፡ ምሽቱም፡ ራስዋን፡ አዘጋጅታለች። *መዝ፡ ፻፲፰፡ ፳፬። †ም፡ ፳፩፡ ፱።

፰፡ ቢስም፡ *ትለብስ፡ ዘንድ፡ተሰጣት፡የጸራ፡የሚያበራም። ይህም፡ ቢስ፡ የቅዱሳን፡ ንጽሕና፡ ነው።

*መዝ፡ ፵፭፡ ፲፬፡ ፲፭። ኢሳ፡ ፷፩፡ ፲።

፱፡ አለኝም። ጻፍ። *ብፁአን፡ ናቸው፡ ወደ፡ በጉ፡ ሰርግ፡ ምሳ፡ የተጸሩ። አለኝም፡ ይህ፡ የእግዚአብሔር፡የእውነት፡ ነገር፡ ነው።

*ሉቃ፡ ፲፬፡ ፲፭።

፲፡ በግሩ፡ ፊትም፡ *ወደቅሁ፡ እሰግድለት፡ ዘንድ። አለኝም። እይ፡ አታድርገው። እኔ፡ እንደንተ፡ አገልጋይ፡ ነኝ፡ የየሱስንም፡ †ምስክር፡ እንደ፡ ያዙ፡ እንደ፡ ወንድሞችህ፡ ነኝ። ለእግዚአብሔር፡ ስገድ። የየሱስ፡ ምስክር፡ የትንቢት፡ መንፈስ፡ ናትና።

*ም፡ ፳፪፡ ፰። የሐዋ፡ ፲፡ ፳፭፡ ፳፮። †ም፡ ፲፪፡ ፲፯።

፲፩፡ ሰማይንም፡ተከፍታ፡አየሁ። እነሆም፡ *አምበላይ፡ ፈረስ። በርሱም፡ የተቀመጠ፡ †የታመነ፡እውነተኛም፡ ይባላል። በጽድቅም፡ **ይፈርዳል፡ ይጸላማል።

*ም፡ ፮፡ ፪። †ም፡ ፩፡ ፭። ና፡ ፫፡ ፲፬። **ኢሳ፡ ፲፩፡ ፬፡ ፭።

፲፪፡ *ዓይኖቹም፡ እንደ፡ እሳት፡ ነበልባል፡ ናቸው፡ በራሱ፡ ላይም፡ ብዙ፡ አክሊሎች፡ ነበሩ። የተጻፈም፡ †ስም፡ ነበረው፡ ማንም፡ የማያውቀው፡ ከርሱ፡ በቀር።

*ም፡ ፩፡ ፲፬። ና፡ ፪፡ ፲፯። †ም፡ ፫፡ ፲፪።

፲፫፡ በደም፡ የታለለም፡ *ልብስ፡ ተጐናጽፎ፡ ነበር። †ስሙም፡ የእግዚአብሔር፡ ቃል፡ ይባላል።

*ኢሳ፡ ፷፫፡ ፩። †ዮሐ፡ ፩፡ ፩።

፲፬፡ በሰማይም፡ያሉ፡*ጭፍሮች፡ይከተሉት፡ነበሩ፡ ባምበላይ፡ ፈረስ፡ ተቀምጠው፡ የነጻ፡ የጸራም፡ ልብስ፡ ለብሰው።

*ም፡ ፲፯፡ ፲፬።

፲፭፡ ካፉም፡ የተሳለ፡ ሰይፍ፡ይወጣል፡ አሕዛብን፡ ይመታበት፡ ዘንድ። እርሱም፡ ያሰማራቸዋል፡ *በብረት፡ በትር። እርሱም፡ ሁሉን፡ የሚይዝ፡የእግዚአብሔርን፡ የመቅሠፍቱን፡ የቍጣውንም፡ ወይን፡ መጥመቂያ፡ †ይረግጣል። *ም፡ ፲፪፡ ፭። መዝ፡ ፪፡ ፱፡—፲፪። †ም፡ ፲፬፡ ፲፱፡ ፳። ኢሳ፡ ፷፫፡ ፫።

፲፮፡ በልብሱም፡ በጭኑም፡ የተጻፈ፡ ስም፡ ነበረበት። †የነገሥታት፡ ንጉሥ፡ የጌቶችም፡ ጌታ።

*ም፡ ፲፯፡ ፲፬። ፩፡ ጢሞ፡ ፮፡ ፲፭።

፲፯፡ አንድ፡ መልአክም፡ በጸሐይ፡ ቁሞ፡ አየሁ፡ በታላቅ፡ ቃልም፡ ጮኸ፡ እንደህ፡ ሲል፡ በሰማይ፡ መካከል፡ ለሚበሩ፡ ወፎች፡ *ኑ፡ ወደ፡ ታላቁ፡ ወደ፡ እግዚአብሔር፡ ምሳ፡ ተከማቹ። *ሕዝ፡ ፴፱፡ ፬፡ ፲፯።

፲፰፡ የነገሥታትን፡ሥጋ፡ ትበሉ፡ዘንድ። የአምበሎችንም፡ ሥጋ። የኃያላኑንም፡ ሥጋ። የፈረሶችንም፡ ሥጋ፡ በላያቸውም፡ የተቀመጡባቸውን። የሰው፡ ልጆችንም፡ ሁሉ፡ ሥጋ፡ የባሮችንም፡የታናሾችንም፡የታላቆችንም።

፲፱፡ አርዌውንም፡*የምድርንም፡ ነገሥታት፡ ጭፍሮቻቸውንም፡ተከማችተው፡አየሁ፡†ሰልፍ፡ያደርጉ፡ ዘንድ፡ በፈረስ፡ ከተቀመጠው፡ ጋራ፡ ከጭፍሮቹም፡ ጋራ። *ም፡ ፲፯፡ ፲፪፡—፲፬። †ም፡ ፲፮፡ ፲፬፡ ፲፮።

፳፡ *አርዌውም፡ ተያዘ፡ ከርሱም፡ ጋራ፡ አሰተኛው፡ ነቢይ፡ በፊቱ፡ †ተአምራት፡ ያደረገው። የአርዌውን፡ምሳሌ፡ የወሰዱን፡ያሳተባት፡ለመልኩም፡ የሰገዱን። እሌህ፡ ሁለቱ፡ በሕይወታቸው፡ በዲን፡ በምትቃጠል፡ **በእሳት፡ ፈሳሽ፡ ወንዝ፡ ተጣሉ።

*ም፡ ፲፫፡ ፩፡ ፲፭። †ም፡ ፲፫፡ ፲፩፡—፲፬። **ም፡ ፳፡ ፲። ዳን፡ ፯፡ ፲፩፡ ፳፯።

፳፩፤ የቀሩትም፡ ተገደሉ፡ በፈረስ፡ ላይ፡ በተቀመጠው፡ ሰይፍ፡ ካፉ፡ በሚወጣው፡ ወፎም፡ ሁሉ፡ ሥጋቸውን፡ ጸገቡ።

ምዕራፍ፡ ፳፤

፩፤ መልአክም፡ ከሰማይ፡ ሲወርድ፡ አየሁ፡ ከርሱም፡ ጋራ፡ የቀላይ፡ *መክፈቻ፡ ነበር፡ ታላቅም፡ ሰንሰለት፡ተበጂ፡ነበር። *ም፡ ፱፡ ፩። †፪፡ ጴጥ፡ ፪፡ ፬። ይሁዳ፡ ቍ፡ ፮።

፪፤ ዘንደውንም፡*ያዘው፡ ያን፡ የቀደመውን፡ እባብ። እርሱም፡ ዲያብሎስ፡ ሰይጣንም፡ ሺህ፡ አመትም፡ አሠረው። *ም፡ ፲፪፡ ፱።

፫፤ በጠለቀም፡ ጕድጓድ፡ አኖረው፡ ቈለፈውም፡ አተመበትም፡ ደግሞ፡ አሕዛብን፡ *እንዳያስት፡ ሺዩው፡አመት፡እስኪፈጸም፡ ድረስ፡ከዚያ፡ በኋላም፡ ጥቂት፡ወራት፡ይፈታ፡ዘንድ፡ይገባል። *፪፡ ተሰ፡ ፪፡ ፱፡ ፲።

፬፤ *ዙፋኖችም፡ አየሁ። በርሳቸውም፡ ተቀመጡባቸው፡ ፍርድም፡ ተሰጣቸው። ስለ፡ የሱስ፡ ምስክርም፡ የሞቱትን፡ ነፍሳት፡ አየሁ፡ ስለ፡ እግዚአብሔርም፡ ቃል፡ ለአርዌውም፡ ያልሰገዱ፡ ለመልኩም፡ ጽፈቱንም፡ ያልወሰዱ፡ በግምባራቸው፡ በጃቸውም። በሕይወትም፡ ተቀመጡ፡ ከክርስተስ፡ ጋራም፡ ነገሡ፡ ሺህ፡አመት። *ዳን፡ ፯፡ ፱፡ ፳፪፡ ፳፯። ሉቃ፡ ፳፪፡ ፴። ፩፡ ቆሮ፡ ፮፡ ፪።

፭፤ የቀሩት፡ ሙታን፡ ግን፡አልደኑም፡ ሺዩው፡አመት፡እስኪፈጸም፡ድረስ። ይህች፡ናት፡ መጀመርያይቱ፡ ትንሣኤ። ፩፡ ቆሮ፡ ፲፭፡ ፳፫። ፩፡ ተሰ፡ ፬፡ ፲፮።

፮፤ ከመጀመርያይቱ፡ ትንሣኤ፡እድል፡ ያለው፡ ብፁዕ፡ቅዱስም፡ ነው። በእሌህ፡ ላይ፡ ሁለተኛይቱ፡ ሞት፡ ሥልጣን፡ የላትም፡ የእግዚአብሔርና፡ የክርስቶስ፡*ካህናት፡ይሆናሉ፡እንጂ፡ከርሱም፡ጋራ፡ሺህ፡ አመት፡ ይነግሣሉ። *ም፡ ፭፡ ፲።

፯፤ ሺህ፡አመትም፡በተፈጸመ፡ጊዜ፡ሰይጣኑ፡ ከሥራቱ፡ ይፈታል።

፰፤ ባራቱ፡ ምድር፡ ማዝንም፡ ያሉትን፡ አሕዛብ፡ ለማሳት፡ይወጣል፡*ጎግንና፡ማጎግን፡ለሰልፍ፡ ይሰበስባቸው፡ ዘንድ፡ቍጥራቸው፡ እንደ፡ †ባሕር፡ አሸዋ፡የሚሆን። *ሕዝ፡ ፴፰፡ ፪። †ሕዝ፡ ፴፰፡ ፱፡ ፲፭።

፱፤ በሰፊ፡ ምድር፡ ላይም፡ ወጡ፡ የቅዱሳንንም፡ ጭፍሮች፡ ከበቡ፡ የተወደደችውንም፡ አገር፡ *እሳትም፡ ከእግዚአብሔር፡ ዘንድ፡ ከሰማይ፡ወርዶ፡ በላቻቸው። *ሕዝ፡ ፴፰፡ ፳፪። ና፡ ፴፱፡ ፮። ዘካ፡ ፲፪፡ ፱።

፲፤ ዲያብሎስም፡ ያሳታቸው፡ በዲኙና፡ በእሳት፡ፈሳሽ፡ወንዝ፡ተጣለ።*አርዌውና፡ አሰተኛው፡ነቢይ፡ወደሉበት። ቀንና፡ ሌትም፡ †ይሣቀያሉ፡ ለዘላለም። *ም፡ ፲፱፡ ፳። †ም፡ ፲፬፡ ፲፡ ፲፩።

፲፩፤ ታላቅ፡ነጭ፡ ዙፋንም፡ አየሁ። የተቀመጠበቱንም፡ከፊቱ፡*ምድር፡የሸሸች፡ሰማይም፡ ቦታም፡አልተገኘላቸውም። *ማቴ፡ ፳፭፡ ፴፩፡—፵። ፪፡ ጴጥ፡ ፫፡ ፯፡—፲፪።

፲፪፤ ሙታንንም፡ አየሁ፡ ታናሾችን፡ ታላቆችንም፡ *በእግዚአብሔር፡ ፊት፡ ቁመው፡ መጻሕፍትም፡ ተከፈቱ። ሌላውም፡ †መጽሐፍ፡ ተከፈተ፡ እርሱም፡ የሕይወት፡ መጽሐፍ። ሙታንም፡ ተፈረዱ፡ በመጻሕፍት፡ተጽፎ፡እንደ፡ ነበረ፡ እንደ፡**ሰሩት፡ መጠን። *ዳን፡ ፯፡ ፲፡ ፳፪። †ም፡ ፫፡ ፭። ፊል፡ ፬፡ ፫። **ሮሜ፡ ፪፡ ፮።

፲፫፤ ባሕርም፡ በርሱ፡ያሉትን፡ሙታን፡ሰጠ። ሞትና፡ሲኦልም፡ በርሳቸው፡ ያሉትን፡ ሙታን፡ ሰጡ። ከርሳቸውም፡ሁሉ፡ኢያንዳንዱ፡እንደ፡ ስራው፡ መጠን፡ ተፈረደበት።

፲፬፤ *ሞትና፡ ሲኦልም፡ በእሳት፡ ባሕር፡ ተጣሉ። ይህች፡ ናት፡ ሁለተኛይቱ፡ ሞት። *፩፡ ቆሮ፡ ፲፭፡ ፳፮፡ ፶፬፡ ፶፭።

፲፭፤ ማንም፡ በሕይወት፡ መጽሐፍ፡ ተጽፎ፡ ባይገኝ፡ በእሳት፡ ባሕር፡ ተጣለ። *ም፡ ፲፱፡ ፳። ማቴ፡ ፳፭፡ ፵፩።

ምዕራፍ፡ ፳፩፤

፩፤ *አዲስ፡ ሰማይም፡ አዲስ፡ ምድርም፡ አየሁ። የፊተኛይቱ፡ ሰማይ፡†የፊተኛይቱም፡ ምድር፡አልፋለችና። ባሕርም፡ እንግዴህ፡ አይገኝም። *ኢሳ፡ ፷፭፡ ፲፯። ፪፡ ጴጥ፡ ፫፡ ፲፫። †ም፡ ፳፡ ፲፩።

፪፤ እኔም፡ዮሐንስ፡ የተቀደሰችውን፡አገር፡ አየሁ፡ አዲሲቱን፡*የሩሳሌምን፡ከሰማይ፡ስትወርድ፡†ከእግዚአብሔር፡ዘንድ፡ተዘጋጅታ፡ለባልዋ፡ እንደጌጸች፡ **ሙሽራ። *ዕብ፡ ፲፩፡ ፲፡ ፲፮። †ዕብ፡ ፲፪፡ ፳፪። ገላት፡ ፬፡ ፳፮። **ም፡ ፲፱፡ ፯፡ ፰።

፫፤ ከሰማይም፡ ታላቅ፡ ድምጽ፡ ሰማሁ፡ እንዲህ፡ ሲል። እነኋት፡ የእግዚአብሔር፡ ድንኳን፡ ከሰዎች፡ ጋራ። ከርሳቸውም፡ ጋራ፡ *ያድራል። እርሳቸውም፡ ወገኖቹ፡ይሆናሉ። †እግዚአብሔርም፡ እርሱ፡ አምላካቸው፡ከርሳቸው፡ጋራ፡ ይሆናል። *ሕዝ፡ ፴፯፡ ፳፯። †ም፡ ፯፡ ፲፯። ኢሳ፡ ፳፭፡ ፰።

፬፤ *እግዚአብሔርም፡ እንብን፡ ሁሉ፡ ካይናቸው፡ ያብሳል። ሞትም፡ እንግዴህ፡ አይሆንም፡ ልቅሶም፡ ጩኸትም፡መጣጣርም፡ እንግዴህ፡ አይሆንም። የቀደመው፡ ሐዲዋልና። ኢሳ፡ ፴፭፡ ፲።

፭፤ *በዙፋን፡ ላይ፡ የተቀመጠውም፡ አለ። እነሆ፡ ሁሉን፡†አዲስ፡አደርጋለሁ። አለኝም። ጻፍ። ይህ፡ነገር፡ እውነት፡ የታመነም፡ ሁንዋልና። *ም፡ ፬፡ ፪፡ ፱። ና፡ ፳፡ ፩። †፪፡ ቆሮ፡ ፭፡ ፲፯፡—፳፩።

፮፤ አለኝም። ፈጽሞ፡ሆነ። *እኔ፡ነኝ፡አልፋ፡ ወሜጋም። መጀመርያ፡ መጨረሻም። እኔ፡ ለተጸማ፡ ከሕይወት፡ ውኃ፡ ምንጭ፡ በከንቱ፡ እሰጣለሁ። *ም፡ ፩፡ ፰።

፯፤ *ድል፡ የነሣ፡ ሁሉን፡ ይወርሳል። †እኔም፡ አምላክ፡ እሆነዋለሁ፡ እርሱም፡ ልጂ፡ ይሆናል። *ም፡ ፪፡ ፯። †ዘካ፡ ፰፡ ፰።

፰፡ *የሚፈሩ፡ግን፡የማያምኑም፡ የተጸሉም። †የሚገድሉም። አመንዝሮችም። አስማተኞችም። ጣዖት፡ የሚያመልኩም። አሰተኞችም፡ ሁሉ። እድላቸው፡ በዲኝ፡ **በእሳት፡ ወደምትቃጠል፡ ባሕር፡ ነው።እርስዋ፡ ሁለተኛ፡ሞት፡ የምትሆን።
*ዕብ፡ ፲፡ ፴፰፡ ፴፱። †ም፡ ፳፪፡ ፲፭። **ም፡ ፳፡ ፲፬።

፱፡ እንዲም፡ ከሰባቱ፡ *መላእክት፡ ወደኔ፡ መጣ፡ የኋለኞቹ፡ቱን፡ ሰባት፡ መቅሠፍት፡ የመላቸ፡ ሰባት፡ ጽዋ፡ ከያዙት፡ ከኔም፡ ጋራ፡ተናገረ፡ እንደህ፡ሲል። ና፡ ተሙሽራዪቱን፡ አሳይሀ፡ የበጉን፡ ምሽት።
*ም፡ ፲፭፡ ፩፡ ፯፡ ፰። †ም፡ ፲፱፡ ፯።

፲፡ በመንፈስም፡ ወደ፡ *ታላቅ፡ ወደ፡ ረጅም፡ ተራራ፡ወሰደኝ፡ ታላቂቱንም፡ አገር፡ አሳየኝ፡ የተቀደሰችውን፡የሩሳሌምን፡ከሰማይ፡ ስትወርድ፡ ከእግዚአብሔር፡ ዘንድ፡ የእግዚአብሔርም፡ ክብር፡ አለባት።
*ሕዝ፡ ፵፡ ፪።

፲፩፡ *ብርሃንዋም፡ እጅግ፡ እንደ፡ ከበረ፡ ደንጊያ፡ ነው። እንደ፡ጸራ፡እንደ፡ ኢያስጲስ፡ደንጊያ።
*ቍ፡ ፳፫። ሕዝ፡ ፵፰፡ ፴፩።

፲፪፡ ለርስዋም፡ ታላቅ፡ ረጅም፡ ቅጥር፡ አለባት። *አሥራ፡ ሁለትም፡ ደጆች፡ አልዋት። በደጆችዋም፡ ላይ፡አሥራ፡ሁለት፡መላእክት፡አሉ፡ ስሞችም፡ ተጽፈውባቸዋል። ያሥራ፡ ሁለቱ፡ የእሥራኤል፡ ልጆች፡ ወገን፡ ስሞች።
*ሕዝ፡ ፵፰፡ ፴፩።

፲፫፡ በምሥራቅ፡ ሶስት፡ ደጆች። በሰሜን፡ ሶስት፡ ደጆች። በደቡብ፡ ሳስት፡ ደጆች። በምዕራብ። ሶስት፡ ደጆች።

፲፬፡ ያገሪቱም፡ቅጽር፡ አሥራ፡ሁለት፡ መሠረቶች፡ አልዋቸው። በርሳቸውም፡ ላይ፡ ያሥራ፡ ሁለቱ፡ የበጉ፡ ሐዋርያት፡ ስሞች፡ አሉባቸው።

፲፭፡ ከኔም፡ጋራ፡ይናገር፡*የነበረው፡የወርቅ፡ ዘንግ፡ ይዞ፡ ነበረ፡ አገሪቱን፡ ይለካ፡ ዘንድ፡ ደጆችዋንም፡ ቅጽርዋንም።
*ሕዝ፡ ፵፡ ፫።

፲፮፡ አገሪቱም፡ *አራት፡ማዝን፡ ነበረች። ርዝመትዋም፡በወርድዋ፡ እኩል፡ ነው። አገሪቱንም፡ በዘንግ፡ ለካት፡ አሥራ፡ ሁለት፡ ሺህ፡ ምዕራፍ፡ የሚሆን፡ ርዝመትዋ፡ ወርድዋም፡ ከፍታዋም፡ የተካከለ፡ ነው።
*ሕዝ፡ ፵፰፡ ፲፮፡ ፲፯።

፲፯፡ ቅጽርዋንም፡ለካ፡መቶ፡ አርባ፡አራት፡ ክንድ፡ በሰው፡ ልክ፡ እርሱም፡ በመልአክ፡ ልክ።

፲፰፡ የቅጽርዋም፡ ስራ፡ በኢያስጲስ፡ ደንጊያ፡ ነበረ። አገሪቱም፡ ከጽሩ፡ ወርቅ፡ ናት፡ ጽሩ፡ ብርጭቆ፡ የሚመስል።

፲፱፡ ያገሪቱም፡ ቅጽር፡ መሠረቶች፡ በከበረ፡ ደንጊያ፡ሁሉ፡ *ተጌጽዋል። መጀመርያው፡ መሠረት፡ ኢያስጲስ፡ ነው። ሁለተኛው፡ ሰፊርስ። ሶስተኛው፡ ከልቄዶን።አራተኛው፡መረግድ።
ኢሳ፡ ፶፬፡ ፲፩፡ ፲፪።

፳፡ አምስተኛው፡ ሰርዶንክዮስ። ስድስተኛው፡ ሰርድዮን።ሰባተኛው፡ክሪሶሊት።ስምንተኛው፡ በሪሌ። ዘጠነኛው፡ ተጳዚዮን። አሥረኛው፡ክሪሶጵራስ። አሥራ፡ አንደኛው፡ ሀያክንቶስ። አሥራ፡ ሁለተኛው፡ አሜቴስጦስ።

፳፩፡ አሥራ፡ሁለቱም፡ ደጆች፡ አሥራ፡ ሁለት፡ ሉሎች፡ናቸው። ደጆቹ፡ኢያንዳንዱ፡ አንድ፡አንድ፡ ሉል፡ ነበረ።*ያገሪቱም፡አደባባይ፡ በጽሩ፡ ወርቅ፡ ነበረ፡እንደ፡ ጽሩ፡ ብርጭቆ።
ም፡ ፳፪፡ ፪።

፳፪፡ መቅደስም፡አላየሁባትም።እግዚአብሔር፡ኹሉን፡ የሚይዝ፡መቅደስዋ፡ ነውና፡ በጉም።

፳፫፡ አገሪቱም፡ ጸሓይ፡ ጨረቃም፡ያበሩላት፡ ዘንድ፡አትሻም። የእግዚአብሔር፡ ክብር፡ አብርቶላታልና፡ መብራትዋም፡ በጉ፡ ነውና።
ም፡ ፳፪፡ ፭።
ኢሳ፡ ፳፬፡ ፳፫። ና፡ ፷፡ ፲፱፡ ፳።

፳፬፡ የዳኑም፡ አሕዛብ፡ በብርሃንዋ፡ ይሔዳሉ። የምድርም፡ነገሥታት፡ክብራቸውን፡ ባለጠግነታቸውንም፡ ወደርስዋ፡ ያመጣሉ።
ኢሳ፡ ፷፡ ፫፡ ፭።

፳፭፡ ደጆችዋም፡በቀን፡አይዘጉም። ሌት፡ ከዚያ፡ የለምና። ኢሳ፡ ፷፡ ፲፩። ዘካ፡ ፲፬፡ ፯። ራእ፡ ፳፪፡ ፭።

፳፮፡ የአሕዛብንም፡ ክብር፡ ምስጋናቸውንም፡ ወደርስዋ፡ ያመጣሉ።

፳፯፡ ርኩሰም፡ሁሉ፡ አይገባባትም፡ ጽያፍና፡ ሐሰት፡ የሚያደርግም፡ በበጉ፡ ሕይወት፡ መጽሐፍ፡ ከተጻፈት፡በቀር።
ም፡ ፳፡ ፲፭። ፊል፡ ፬፡ ፫—፱።

ምዕራፍ፡ ፳፪፡

፩፡ *ጽሩ፡ ፈሳሽም፡ አሳየኝ፡ከሕይወት፡ ውኃ፡እንደ፡ ባሉር፡ የሚያበራ፡ ከእግዚአብሔር፡ ዙፋን፡ ከበጉም፡ ሲወጣ።
*ሕዝ፡ ፵፯፡ ፲፪። ዘካ፡ ፲፬፡ ፰።

፪፡ *ባደባባዩዋም፡ መካከል፡ በፈሳሹ፡ ወንዝም፡ ዳር፡ ወዲህና፡ወዲያ፡ የሕይወት፡ ዛፍ፡ አለች። አሥራ፡ ሁለት፡ ፍሬም፡ ትሰጣለች፡ በወር፡ በወርም፡ ታፈራለች።የዛፊቱም፡†ቅጠል፡የአሕዛብ፡ፈውስ፡ነው።
*ም፡ ፳፩፡ ፳፩። †ሕዝ፡ ፵፯፡ ፲፪።

፫፡ *መርገምም፡ ሁሉ፡ ከዚያ፡በኋላ፡ አይሆንም። የእግዚአብሔርና፡ የበጉም፡ ዙፋን፡ በርስዋ፡ ይኖራል፡ ባሮቹም፡ያመልኩታል።
*ዘካ፡ ፲፬፡ ፲፩።

፬፡ ፊቱንም፡*ያዩታል፡ †ስሙም፡በግምባራቸው፡ ተጽፎዋል።
*ም፡ ፳፩፡ ፫። †ም፡ ፫፡ ፲፪።

፭፡ *ሌትም፡ ከዚያ፡አይሆንም። መብራትም፡ አይሹም፡ የጸሓይንም፡ ብርሃን። እግዚአብሔር፡አምላክ፡ ያበራላቸዋልና። ለዘላለሙም፡ †ይነግሣሉ።
*ም፡ ፳፩፡ ፳፫። †ም፡ ፫፡ ፲። ዳን፡ ፯፡ ፲፰፡ ፳፯።

፮፡ አለኝም። ይህ፡ ነገር፡ እውነተኛ፡ የታመነም፡ ነው፡ እግዚአብሔርም፡የቅዱሳን፡ነቢያት፡ አምላክ፡ *መልአኩን፡ ሰደደ፡ ፈጥና፡ ይሆን፡ ዘንድ፡የሚገባውን፡ ለባሮቹ፡ ይገልጥ፡ ዘንድ።
*ም፡ ፩፡ ፩።

፯፡ እነሆኝ፡እኔ፡ ፈጥኜ፡እመጣለሁ። የዚህን፡ መጽሐፍ፡ ትንቢት፡ ነገር፡ የሚጠብቅ፡ ብፁዕ፡ ነው።
ቍ፡ ፲፪፡ ፳። ም፡ ፫፡ ፲፩። ና፡ ፩፡ ፫።

፰፡ እኔ፡ ዮሐንስ፡ ነኝ፡ የህቸን፡ ያየሁ፡ የሰማኋት ም። ባየሁም፡ በሰማሁም፡ ጊዜ፡ ይህቸን፡ ይገልጥል ኝ፡ በነበረው፡በመልአኩ፡ *እግር፡ ፊት፡ እሰግድ፡ዘን ድ፡ ወደቅሁ። *ምዕ፡ ፲፱፡ ፲፡፡

፱፡ አለኝም። ተመልከት፡ አታድርገው። እኔ፡ አን ደንተ፡ ባርያ፡ ነኝና፡ እንደ፡ ወንድሞችህም፡ እንደ፡ ነቢያት። የዚህንም፡ መጽሐፍ፡ ነገር፡ እንደሚጠብ ቁ። ለእግዚአብሔር፡ ስገድ።

፲፡ አለኝም። የዚህን፡ መጽሐፍ፡ ትንቢት፡ ነገር፡ አትቍልፍ። ዘመኑ፡ ቀርብዋልና።

፲፩፡ ግፍ፡ የሚሰራ፡ግፍ፡ይስራ፡ደግሞ። ርኩስም፡ የሚሆን፡ርኩስ፡ይሁን፡ደግሞ። ጻድቁም፡ይጸድቅ፡ ደግሞ። ቅዱሱም፡ ይቀደስ፡ ደግሞ።

፲፪፡ *እነሆኝም፡ ፈጥኜ፡እመጣለሁ፡ ዋጋዬም፡ ከ ኔ፡ጋራ፡ ነው፡ ለሁሉ፡ ኢያንዳንዱ፡ እንደ፡ስራው፡ †እ ሰጠው፡ ዘንድ። *ቈላ ፫፡፡ ምዕ፡ ፫፡ ፲፩፡፡ †ሮሜ፡ ፪፡ ፯፡—፲፩፡፡

፲፫፡ እኔ፡ ነኝ፡ አልፋ፡ ዖሜጋም፡ መጀመርያ፡ መጨ ረሻም። የፊተኛው፡ የኋለኛውም። ምዕ፡ ፩፡ ፰፡ ፲፯፡፡

፲፬፡ ትእዛዙን፡የሚያደርጉ፡ብፁዓን፡ናቸው። ሥ ልጣናቸው፡ በሕይወት፡ ዛፍ፡ ላይ፡ ይሆን፡ ዘንድ። በ ደጆም፡ ወደ፡ ከተማ፡ ይገባሉ። ምዕ፡ ፲፫፡ ፯፡፡

፲፭፡ በሚደዋ፡ ግን፡ ናቸው፡ ውሾች፡ አስማተኞች ም፡ አመንዝሮችም፡ ነፍሰ፡ ገዳዮችም፡ ጣዖት፡ የሚ ያመልኩም፡ አሰትም፡ የሚወድ፡ ሁሉ፡ የሚያደርገ ውም። ምዕ፡ ፳፩፡ ፳፯፡፡ ፩፡ ቆሮ፡ ፮፡ ፱፡ ፲፡፡

፲፮፡ እኔ፡ የሱስ፡ *መልአኬን፡ ላክሁ፡ ይህቸን፡ ተደ መሰክርላችሁ፡ ዘንድ፡በአብያተ፡ክርስቲያናት። እኔ፡ የደዊት፡ **ሥር፡ ዘሩም፡ ነኝ፡ የሚያበራ፡ የንጋት፡ ††ኮከብ። *ምዕ፡ ፩፡ ፩፡፡ †ምዕ፡ ፩፡ ፪፡፡ **ኢሳ፡ ፲፩፡ ፲፡፡ ራእ፡ ፭፡ ፭፡፡ ††ሉቃ፡ ፩፡ ፸፰፡፡

፲፯፡ *መንፈስም፡ ሙሽራይቱም፡ ይላሉ። ና። የ ሚሰማም፡ ይበል። ና። †የተጸማም፡ ይምጣ። የወ ደደም፡ የሕይወት፡ ውኃ፡ በከንቱ፡ ይውሰድ። *ሮሜ፡ ፰፡ ፳፫፡፡ †ምዕ፡ ፳፩፡ ፮፡፡ ኢሳ፡ ፶፭፡ ፩፡፡ ዮሐ፡ ፯፡ ፴፯፡፡

፲፰፡ የዚህን፡ መጽሐፍ፡ ትንቢት፡ነገር፡ ለሚሰማ፡ ሁሉ፡እመሰክራለሁና። ማንም፡ በዚህ፡ ላይ፡ አንዳ ች፡ ቢጨምር፡እግዚአብሔር፡*በዚህ፡ መጽሐፍ፡የተ ጻፈውን፡ መቅሠፍት፡ ይጨምርበታል። *ምዕ፡ ፲፭፡ ፩፡ ፮፡—፰፡፡

፲፱፡ ደግም፡*ማንም፡አንዳች፡ከዚህ፡ትንቢት፡መ ጽሐፍ፡ነገር፡ቢያጉድል፡እግዚአብሔር፡ ከሕይወት፡ መጽሐፍ፡ ከተቀደሰችውም፡ አገር፡ †መክፈሉን፡ ያጐድልበታል፡ በዚህ፡ መጽሐፍም፡ ከተጻፈው። *ዘዳግ፡ ፬፡ ፪፡፡ ፭፡ ፲፪፡ ፴፪፡፡ †ፊል፡ ፬፡ ፫፡፡

፳፡ በዚህ፡ የሚመሰክረው፡ ይላል። አዎን፡ ፈጥ ኜ፡እመጣለሁ።አሜን። አዎን፡ጌታ፡ሆይ፡ የሱስ፡ ና።

፳፩፡ የጌታ፡ የየሱስ፡ ክርስቶስ፡ ጸጋ፡ ከሁላችሁ፡ ጋ ራ፡ትሁን።አሜን።

ተፈጸመች ፡ የዮሐንስ ፡ ራእይ ፡ አጶቃሊጵሲስ።

